# ኖኅተ ጥበብ
# ዘሥነ ጽሑፍ



# ጥንተ ጥበብ ዘሥነ ጽሑፍ

ይህን PDF ያዘጋጀነው

www.binyamhk.wordpress.com

አቀረብነልዎት ።

አዲስ አበባ፣ 2015 ዓ.ም ።

# ኖኅተ ጥበብ ዘሥነ ጽሑፍ

ከተክለ ማርያም ፋንታዬ

ቴባ

አዲስ አበባ ፲፱፻፺፭ ዓ.ም. ፫ኛ ጊዜ ታተመ ።

መልሶ ማሳተም መብቱ የደራሲው ነው ።

በግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ንጉሠ ነገሥት ዘኢትዮጵያ
በ፵፭ኛው ዘመነ መንግሥት
፲፱፻፷፬ ዓመተ ምሕረት ይህ መጽሐፍ ታተመ ።
እንደገና በ፲፱፻፷፰ ዓ. ም. ታተመ ።

በብርሃንና ሰላም ቀ.ኃ.ሥ. ማተሚያ ቤት ታተመ ።



ግርማዊ ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡
ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ዘኢትዮጵያ ፡

ክቡር ፡ የትምህርትና ፡ የሥነ ፡ ጥበብ ፡ ሚኒስቴር ፡ መልካም፡ ፈቃዱ ፡ ሆኖ ፡ መጽሐፉን ፡ በበጎ ፡ አስተያየት ፡ በመቀበል ፡ ሁኔታውን፡ አስመርምሮ ፡ እንዲታተም ፡ ስለ ፡ ፈቀደና ፡ አስፈላጊውን ፡ ርዳታ ፡ ስላደረገ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ምስጋናዬን ፡ በትሕትና ፡ አቀርባለሁ ።

አቶ ፡ መኰሪያ ፡ ወርቁ ፡ ይህን ፡ መጽሐፍ ፡ ከማዘጋጀቴ ፡ በፊትና ፡ ካዘጋጀሁም ፡ በኋላ ፡ በሐሳብ ፡ ከመርዳታቸው ፡ በላይ ፡ እንዲታተም ፡ በብዙ ፡ ስለ ፡ ጣሩበት ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ ምስጋናዬን ፡ አበረክታለሁ ።

ይህ ፡ መጽሐፍ ፡ ከተዘጋጀ ፡ በኋላ ፡ አሳቡን ፡ በማቃናት ፡ ለደከሙልኝ ፡

ለመምህር ፡ መዝገበ ፡ ሥላሴ ፡

ለአባ ፡ ዐሥራት ፡ ዘገየ ፡

ለአባ ፡ ፍሥሓ ፡

ላለቃ ፡ ኃይለ ፡ ጊዮርጊስና ፡ ተረትና ፡ ምሳሌ ፡ በመሰብሰብ ፡ ለረዱኝ ።

ላቶ ፡ ዓለሙ ፡ ፈቃጁ ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ ምስጋናዬን ፡ አቀርባለሁ ።



ተክለ ፡ ማርያም ፡ ፋንታዬ ፡

# ማውጫ

መጻሕፍት ፡ የተፈጥሮ ፡ ዕውቀታችንን ፡ በመልካም ፡ አኳኋን ፡ እየመራን ፡ የኑ፡ ሯችንን ፡ ዘዴ ፡ የምናሻሽልበትን ፡ ያስተምሩናል ፡ እንጂ፡ አዲስ ፡ የተፈጥሮ ፡ ዕውቀትን አይሰጡንም ። እንደዚሁም ፡ የጥንተ ፡ ጥበብ ፡ ዘሥነ ፡ ጽሑፍ ፡ ዐላማው ፡ ወጣቶችን ፡ ወደ ፡ ትክክለኛው ፡ የሥነ ፡ ጽሑፍ ፡ አገባብና ፡ ወደ ፡ መልካሙ ፡ የንግግር ፡ አሰጣጥ ፡ መምራት ፡ ነው ። ትርጓሜውም ፡ የአጻጻፍ ፡ ሥነ ፡ ሥርዐት ፡ በር ፡ ማለት ፡ ነው ። በውስጡም ፡ የሚገኙት ፡ የትምህርት ፡ ዐይነቶች ፡ የሚከተሉት ፡ ናቸው ።

፩ ፡ ሰዋስው ፡

ሰዋስው ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ በሌላ ፡ በኩል ፡ ትርጕሙ ፡ መሰላል ፡ ማለት ፡ ቢሆን ፡ በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ የቃላትን ፡ ንብረትና ፡ አገባብ ፡ የሚያስተምር ፡ ክፍል ፡ ነው። የንግግር ፡ ክፍሎች ፡ አንድ ፡ ቤት ፡ ለመሥራት ፡ በሚሰበሰቡ ፡ ነገሮች ፡ ይመሰላሉ ።

አንድ ፡ ቤተ ፡ ሠሪ ፡ አስቀድሞ ፡ ቤቱን ፡ ከመሥራቱ ፡ በፊት፡ ዕንጨት ፡ ድንጋይ፡ ሲሚንቶ ፡ አሸዋ ፡ ወይም ፡ ጭቃ ፡ ቆርቆሮ ፡ ወይም ፡ ሣር ፡ ገመድ ፡ ወይም ፡ ምስማር ፡ ማንቃ ፡ ጉበን ፡ መቃንና ፡ ደፍ ፡ ያዘጋጅና ፡ ከቤቱ ፡ መሠረት ፡ አንሥቶ ፡ በየደረጃው ፡ ይሠራባቸዋል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ቤቱ ፡ አምሮ ፡ ተለስኖ ፡ ወለሉ ፡ ተነጥፎ ፡ መስኮቶቹና ፡ መዝጊያዎቹ ፡ ተገጣጥመው ፡ ያማረና ፡ የተዋበ ፡ ሆኖ ፡ ለሰውዬው ፡ መኖሪያ ፡ ይሆናል።

እንደዚሁም ፡ የንግግር ፡ ክፍሎችን ፡ በያይነታቸውና ፡ በየወገናቸው ፡ ሰብስቤ ፡ ተጠንተው ፡ አንድ ፡ ጽሑፍን ፡ ማዘጋጃ ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ በማለት ፡ ማስረጃ ፡ እየሰጠሁ ፡ አሰናድቻቸዋለሁ ።

፪ ፡ አገባብ ፤

የቃላትን ፡ ንብረትና ፡ አገባብ ፡ ማወቅ ፡ በቂ፡ አለመሆኑን ፡ በመረዳትና፡ ዋናው፡ ነገር ፡ አሳብን ፡ በቅደም ፡ ተከተልነት ፡ ማስገባት፡ መሆኑን ፡ በመገንዘብ ፡ ያንድ፡ ጽሑፍ፡ ፍሬ ፡ ነገር ፡ ጕልቶ፡ የሚሰጥበትን፡ ዘዴ፡ ጽፌያለሁ። ስለዚህ፡ የቃላትን ፡ አቀነባበር፡ ማጥናት ፡ እንደሚገባ ፡ ሁሉ ፡ ሐረጎችንና ፡ ዐረፍተ ፡ ነገሮችንም ፡ በየስልታቸው ፡ መማር ፡ ይገባል ።

ይህ ፡ ክፍል ፡ ከዚህ ፡ በቀር ፡ የቃላትን ፡ ጥቅም ፡ እያስፋፋ ፡ ከማስረዳቱ ፡ በላይ ፡ የሚጠኑበትንም ፡ ዘዴ ፡ ከነማስረጃው ፡ በመጠኑ ፡ አጠናቆ ፡ ያሳያል ።

፫ ፡ ምሥጢርን ፡ የሚያጐሉ ፡ ንግግሮች ፡

ምሥጢርን ፡ የሚያጐሉ ፡ ንግግሮች፡ ስሜታቸውን ፡ እንደ ፡ ባሕር፡ ማሽላ ፡ በኀይለ ፡ ቃላቸው ፡ ሰውረው ፡ የሚያጐርሱ ፡ ናቸው ። ተረትና ፡ ምሳሌ ፡ ምጸትና ፡ ምሳሌያውያን ፡ ንግግሮች ፡ (የሠምና ፡ የወርቅ ፡ መንገድ ፡ ንግግሮች፡) የተሰወሩ ፡ አሳቦች፡ ስለሚገለጹባቸው ፡ ባንድነት ፡ ምሥጢርን፡ የሚያጐሉ ፡ ንግግሮች፡ ተብለው፡ ተጠቅለዋል። እነዚህም ፡ እንደ ፡ ሌሎቹ ፡ በየስልታቸው ፡ ቢጠኑ ፡ የተመራማሪነትንና ፡ የተራቃቂነትን ፡ መንፈስ ፡ እንደሚቀሰቅሱ ፡ በማረጋገጥ ፡ በያገባባቸው ፡ ተጽፈዋል ።

፩ ፤ ያሳብ ፡ መግለጫዎች ፤

ያሳብ ፡ መግለጫዎች ፡ ሰው ፡ አሳቡን ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ አካሄድ ፡ እያደረገ ፡ የሚስጥባቸው ፡ ድርሰቶች ፡ ናቸው ። ባሳብ ፡ መግለጫዎች ፡ ውስጥ ፡ የሚጠቀለሉት ፡ ንግግር፡ አስተዋፅኦ ፡ አጎጽሮተ ፡ ጽሑፍ ፡ አንቀጽና ፡ ነጥቦች ፡ ናቸው ። እነዚህ ፡ አርእስት ፡ ለሁለተኛ ፡ ደረጃ ፡ ትምህርት ፡ ቤቶች ፡ የጽሑፍ ፡ ማስፋፊያ ፡ መምሪያዎች ፡ እንዲሆኑ ፡ ተዘጋጅተዋል ።

ስለዚህ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ የድርሰት ፡ ዐይነቶች ፡ በሙሉ ፡ ባይዘረዘሩ ፡ ዋና፤ ዋናዎቹ፡ ስለ ፡ ተጻፉ ፡ በጥንቃቄ ፡ እያስተዋሉ ፡ ቢያጠኗቸው ፡ አሳብን ፡ በጽሑፍም ፡ ሆነ ፡ በንግግር ፡ ለመግለጽ ፡ እንደሚያስችሉ ፡ የተረጋገጠ ፡ ነው ።

መጽሐፉ ፡ የሚጠናበት ፡ ዘዴ ፤

ይህ ፡ መጽሐፍ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተደጋጋፊ ፡ የሆኑትን ፡ ክፍሎች ፡ የያዘ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፤ የመዠመሪያውን ፡ ክፍል ፡ ወደ ፡ ሁለተኛው ፡ ሳያልፉ ፡ ድቅቅ ፡ እያደረጉ፤ ያጠኑት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፤ የሚቀጥለው ፡ አይከብድም ። ለምሳሌ ፡ አንድ ፡ ገበሬ ፡ ጫካውን፡ መንጥሮ ፡ አቃጥሎ ፡ ገምሶ ፡ አለስልሶ ፡ ዘርቶ ፡ አርሞ ፡ ዐጭዶ ፡ ወይም ፡ ቈርጦ ፡ ከምሮና ፡ ወቅቶ ፡ ምርቱን ፡ ከገለባው ፡ እንደሚለየው ፡ ሁሉ ፤ የመጽሐፉንም ፡ ፍሬ ፡ ነገር ፡ በዚሁ ፡ ዐቅድ ፡ ቢከታተሉት ፡ አሳቡን ፡ ለማግኘት ፡ ይቻላል ። ነገር ፡ ግን ፡ ያለድካም ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ አንብበን ፡ እናገኘዋለን ፡ ብሎ ፡ ማሰብ ፡ የሚከናወን ፡ ነገር ፡ አይደለም ። እንግዴህ ፡ ይህን ፡ መጽሐፍ ፡ ለማጥናት ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ አስተዋይ ፡ ትዕግሥተኛና ፡ ቈራጥ፡ ገበሬ ፡ ሆኖ፡ መነሣት ፡ ያስፈልጋል። ያጠናኑም፡ ዐድቅ ፡ እንደሚከተለው፡ ነው።

1 መዠመሪያ ፡ አርእስቱን ፡ ተራ ፡ በተራ ፡ እየወሰዱ ፡ በተቻለ ፡ መጠን ፡ አሳቡን ፡ መረዳት ፤

2 ያርእስቱን ፡ አሳብ፡ አፍታቶ፡ ከተረዱ፡ በኋላ፡ በገዛ፡ራስ ፡ ማስረጃ፡ መስጠት፡

3 የሠሩትን ፡ ማስረጃ ፡ ባጸኑት ፡ መሠረት ፡ በገዛ ፡ ራስ ፡ ማረም ፤

4 እንዲሁም ፡ በጥንቃቄ ፡ ከሠሩ ፡ በኋላ ፡ ለመምህሩ ፡ ማቅረብ ፡

5 መምህሩ ፡ ባረመው ፡ አካሄድ ፡ እየመላለሱ ፡ አጣርቶ ፡ መጻፍና ፡ ስሕተትን ፡ መከታተል ፤

6 የመጽሐፉን ፡ ዐላማ ፡ እያሰቡ ፡ ወደ ፡ ግቡ ፡ ለመድረስ ፡ ዘወትር ፡ በጋለ ፡ መንፈ ፡ መሥራት ፡

7 እያንዳንዱን ፡ ክፍል ፡ ካጠኑ ፡ በኋላ ፡ የተሰጠውን ፡ መልመጃ ፡ መሥራት ፤ መልመጃው ፡ ከበድ ፡ ያለ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፤ እንደ ፡ ገና ፡ ማጥናት ፤

አንድ ፡ ተማሪ ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ በገዛ ፡ ራሱ ፡ ለመረዳት ፡ የተጣጣረ ፡ እንደ ሆነ ፡ በክፍል ፡ ውስጥ ፡ የሚነገረው ፡ ትምህርት ፡ በቀላሉ ፡ ይገባዋል ። ስለዚህ ፡ መጽሐፉ ፤ የተዘጋጀው ፡ በገዛ ፡ ራሳቸው ፡ እየተጣጣሩ፡ ለሚያጠኑ ፡ ልጆችና ፡ ሰዎች ፡ ስለ ፡ ሆነ ፤ ያስተማሪዎች ፡ ችግር ፡ በጣም ፡ ቀላል ፡ ነው ።

ተክለ ፡ ማርያም ፡ ፋንታዬ ፡

# ክፍል ፩ ሰዋስው ።

## የሐረግ ፡ በር ፡ መክፈቻ ፡ ክፍል ።

ቃላት ፡ ተገጣጥመው ፡ አንድ ፡ ሙሉ ፡ ስሜትን ፡ የሚሰጡበት ፡ ክፍል ፡ አለ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አሁን ፡ ቃላት ፡ ተገጣጥመው ፡ ሙሉ ፡ ስሜትን ፡ ሳይሰጡ ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ አንዳች ፡ ስሜትን ፡ እንደሚያተርፉ ፡ ሆነው ፡ ይገባሉ ።

ሐረግ ፡ በሰዋስው ፡ አካሄድ ፡ የቃላት ፡ እንደ ፡ ሰንሰለት ፡ እርስ ፡ በርስ ፡ መያያዝ ፡ ነው ።

ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ባለቤትና ፡ አንቀጽ ፡ የሌለው ፡ ቃላትን ፡ በዘንብረት ፡ የሚይዝ ፡ ክፍል ፡ ነው ።

ምሳሌ ፡-

በወንበር ፡ ላይ ፡ ከቤቱ ፡ በታች ፡

ከጠረጴዛው ፡ እግር ፡ ሥር ፡ ከጎሐ ፡ ጽዮን ፡ እስከ ፡ ዐባይ ፡ ድረስ ፡

አስረጅ ፡-

ድመቲቱ ፡ በወንበር ፡ ላይ ፡ ተቀምጣ ፡ ፊቷን ፡ ታባብሳለች ።

ከጠረጴዛው ፡ እግር ፡ ሥር ፡ አንድ ፡ የእግር ፡ ሹራብ ፡ ማን ፡ አነሣ ?

ቆንዦ ፡ ቆንዦ ፡ አበቦች ፡ ከፈለቀ ፡ ቤት ፡ በታች ፡ ፈክተው ፡ ጥቃቅን ፡ በራሪዎችን ፡ ወዲህ ፡ ኑ ፡ ወዲህ ፡ ኑ ፡ እያሉ ፡ ይጠቀሳሉ ።

አየለ ፡ ከጎሐ ፡ ጽዮን ፡ እስከ ፡ ዐባይ ፡ በእግሩ ፡ ወረደ ።

### ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ያለበት ፡ ዐረፍተ ፡ ነገር ።

ጠላት ፡ በታንክና ፡ በመርዝ ፡ ጪስ ፡ ባይዋጋ ፡ ኖሮ ፡ ወረራ ፡ አያደርግም ፡ ነበር። በሰው ፡ ላይ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ የጭካኔ ፡ ሥራ ፡ ማድረግ ፡ ካውሬ ፡ ያስቈጥራል ።

ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ የቃላት ፡ እንደ ፡ ሰንሰለት ፡ እርስ ፡ በርስ ፡ መተሳሰር ፡ ከንኡስ ፡ ሐረግ ፡ በለጥ ፡ ያለ ፡ ሐረግ ፡ ነው ፤ በንኡስ ፡ ሐረግና ፡ በጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ልዩነት ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ባለቤትና ፡ አንቀጽ ፡ ሲኖረው ፤ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ግን ፡ እነርሱን ፡ አልባ ፡ በመገጣጠሙ ፡ ነው ።

ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ተብሎ ፡ የሚጠራው ፡ ያንድ ፡ ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡ በጥገኛ ፡ መስተፃምር ፡ እንዳያስር ፡ ሆኖ ፡ የታገደበት ፡ ሐረግ ፡ ነው ፤ ከዚህም ፡ የተነሣ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ እንዳንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ለብቻው ፡ አይነገርም ፤ ( ሙሉ ፡ ስሜትን ፡ አይሰጥም ) ። መደበኛ ፡ ሐረግ ፡ ( ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ) ፡ አንድ ፡ ነገርን ፡ ለመናገር ፡ ስንፈልግ ፡ ቃላትን ፡ ( አገጫጭተን ) ፡ አገጣጥመን ፡ እንናገራለን ፤ ይኸ ውም ፡ ሐሳባችንን ፡ ለሰው ፡ እንዲገለጽ ፡ አድርገን ፡ የምንናገርበት ፡ ሐረግ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ይባላል። አረፍተ ፡ አገር ፡ ከንኡስና ፡ ከጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ የበለጠ ፡ ሙሉ ፡ ስሜት ፡ የሚገለጽበት ፡ ነው ።

ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ባለቤትና ፡ አንቀጽ ፡ አሉት ፤ አንቀጹም ፡ እንደ ፡ ጥገኛ፡ ሐረግ ፡ ከማሰሪያነት ፡ በጥገኛ ፡ መስተፃምር ፡ አይከለከልም ፤ እንደዚሁም ፡ አንድ ፡ስም፡ የአንቀጹ ፡ ግብር ፡ የተገለጠበት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ተሳቢ ፡ ይባላል ።

አንቀጹም ፡ የሚነገርለት ፡ ስምና ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ባለቤት ፡ ይሳላል ። ስለ ፡ ባለቤቱም ፡ የሚነገረው ፡ ነገር ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡ ይባላል ። የአንቀጹን ፡ ባለቤት ፡ ለማግኘት ፡ ማን ፡ ወይም ፡ ምን ፡ ተብሎ ፡ ይጠየቃል ።

አስረጅ ፡-

ማን ፡ አስተማረህ ? መንግሥቱ ፡ አስተማረኝ ።

ምን ፡ ፈሰሰ ፡ ወይም ፡ ወደቀ ? ወተቱ ፡ ፈሰሰ ፡ ወይም ፡ ቅሉ ፡ ወደቀ ።

ያረፍተ ፡ ነገሩንም ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡ ለማግኘት ፡ መንግሥቱ ፡ ምን ፡አደረገ?

መንግሥቱም ፡ ምን ፡ ሆነ ? ተብሎ ፡ ይጠየቃል ፤ ይኸውም ።

መንግሥቱ ፡ ቆንጆ ፡ ቆንጆ ፡ አበቦችን ፡ ቀጠፈ ።

መንግሥቱ ፡ ታሚል ፡ ተብሎ ፡ ይነገራል ፡ ማለት ፡ ነው ።

አንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገርን ፡ በሁለት ፡ ላይ ፡ እንከፍለዋለን ።

(ሀ) ባለቤትና ፡ የባለቤት ፡ ጓዝ ።

(ለ) አንቀጽና ፡ የአንቀጽ ፡ ጓዝ ።

አስረጅ ፡-

1 የመንግሥቱ ፡ ፈረስ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ጠገበ ፡ ነው ።

2 መንግሥቱ ፡ ቆንጆ ፡ ቆንጆ ፡ አበቦችን ፡ ቀጠፈ ።

| ባለቤት ፡ ከነጓዙ ፡ | አንቀጽ ፡ ከነጓዙ ፡ |
|---|---|
| 1 የመንግሥቱ ፡ ፈረስ ፡ | ሁል ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ጠገበ ፡ ነው ። |
| 2 መንግሥቱ ፡ | ቆንጆ ፡ ቆንጆ ፡ አበቦችን ፡ ቀጠፈ ። |

## የንግግር ፡ ክፍሎች ፡ አመዳደብ ።

ቃላት ፡ በሚሰጡት ፡ ትርጓሜ ፡ መሠረት ፡ በየወገን ፡ በየወገናቸው ፡ እየሆኑ ፡ በስምንት ፡ ታላላቅ ፡ ክፍሎች ፡ ይከፈላሉ ፤ እነርሱም ፡ የሚከተሉት ፡ ናቸው ።

1 ስም ፡ 3 ቅጽል ፡ 5 ተውሳከ ፡ ግስ ፡ 7 መስተፃምር፡

2 ተውላጠ ፡ ስም ፡ 4 ግስ ፡ 6 መስተዋድድ ፡ 8 ቃል ፡ አጋኖ።

እንደዚሁም ፡ እያንዳንዳቸው ፡ በደንብ ፡ እየተገለጹ ፡ በየክፍላቸው ፡ ተዘጋጅተውና ፡ ባዲስ ፡ ድርጅት ፡ ዐቅድ ፡ ተጽፈው ፡ ይገኛሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ፡ ስም ።

መግለጫ ፡-

ስም ፡ መጠሪያ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ስም ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡ ባለቤት ፡ እንደ ፡ ተሳቢ ፡ እንደ ፡ ዘርፍ ፡ ሆኖ ፡ ይገባል ። በስም ፡ ፋንታ ፡ ሆኖ ፡ የሚገባ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ የሚባል ፡ የስም ፡ ምትክ ፡ አለው ። እንደዚሁም ፡ ስምን ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የሚገልጸው ፡ ቅጽል ፡ የሚ ባል ፡ ገላጭ ፡ አለው ፤ ስለዚህ ፡ ስም ፡ እነዚህን ፡ ጓዞቹን ፡ ይዞ ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ዋና ፡ ጠቃሚ ፡ ነው ።

## ፩ኛ ፡ የስም ፡ ዐይነቶች ።

ስሞች ፡ ባምስት ይከፈላሉ ።

(ሀ) የተጸውዖ ፡ ስም ፡ (ሐ) ፡ የጥቅል ፡ ስም ፡(ሠ) የቈሳቍስ ፡ ስም ፡
(ለ) የወል ፡ ስም ፡ (መ) የነገር ፡ ስም ፡

የተጸውዖ ፡ ስም ፡

ላንድ ፡ ሰው ፡ ወይም ፡ ላንድ ፡ ነገር ፡ በተለይ ፡ የተሰጠ ፡ መጠሪያ ፡ ነው ።
ማስገንዘቢያ ፡- ያክብሮትና ፡ የማዕርግ ፡ ስም ፡ በተጸውዖ ፡ ስም ፡ ተደርቦ ፡ ይገባል ።

ምሳሌ ፤ (ሀ) የሰው ፡ ስም ፡- ተቀባ ፤ ወርቁ ፤ አበበ ፤ መንግሥቱ ፤ ወንዳፍራሽ ፤ ማሞ ፤ በቀለ ፤ ዕንቈ ፤ አየለ ፤ በለጠ ፤ በልሁ ፤ መዥሪያ ፤ ለማ ፤
(ለ) የእንስሳት ፡ ስም ፡- ቲቲ ፤ ቦቢ ፤ ሸክሊት ፤ ዳለች ፤ ቡሬ ፤ ዶጉ ።
(ሐ) የቦታ ፡ ስም ፡- ሐረር ፤ ወሎ ፤ ሸዋ ፤ ደሴ ፤ አዲስ ፡ አበባ ፤ ጎንደር ፤ ቡልጋ ፤ አዅስም ፤ መርዌ ፤ ደብረ ፡ ታቦር ።

የወል ፡ ስም ።

አንድ ፡ ዐይነት ፡ ለሆኑ ፡ ነገሮች ፡ የጋራ ፡ መጠሪያቸው ፡ ወይም ፡ ስማቸው ፡ ነው ።
ምሳሌ ፡- በሬ ፤ ላም፤ ፓሮት፤ ዝግባ፤ ሰው፤ አገር፤ ወንዝ፤ ተራራ፤ በረዶ ፤ ደመና፤ ኮከብ ፤

የጥቅል ፡ ስም ፡

ብዙ ፡ የወል ፡ ስሞችን ፡ ጠቅልሎ ፡ የሚይዝ ፡ ስም ፡ ነው ።
ምሳሌ ፡- የዱር ፡ እንስሳ ፤ የቤት ፡ እንስሳ ፤ ልብስ ፤ ምግብ ፤ መጠጥ ፤ ማዕድን ፤ ፍሬ ፤

የቈሳቍስ ፡ ስም ፡

ዕቃው ፡ ለሰው ፡ አገልግሎት ፡ የሚገባ ፡ ስም ፡ ነው ። አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ የወል፡ ስምና፡ የቈሳቍስ ፡ ስም ፡ ይወራረሳሉ ፤ ዕቃው ፡ ከምን ፡ እንደ ፡ ተሠራ ፡ ከምን ፡ እንደ ፡ ተገኘ ፡ ወይም ፡ ከምን ፡ እንደ ፡ ተበጀ ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ባመለከተ ፡ ጊዜ ፤ የዕ ቃው ፡ ስም ፡ የወል ፡ ይሆናል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ዕቃው ፡ ለሰው ፡ አገልግሎት ፡ መግባቱን ፤ ባመለከተ ፡ ጊዜ ፤ የዕቃው ፡ ስም ፡ የቈሳቍስ ፡ ስም ፡ ይሆናል ።

ልዩነታቸውንም ፡ የምናውቀው ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ገቡ፡ በማጥናት ፡ ነው ።
ምሳሌ ፡- ቤት ፤ ዋንጫ ፤ መቋሚያ ፤ ሞፈር ፡ ቀንበር ፤ ትምህርት ፡ ቤት ፤ መሰላል ፤

አስረጅ ፡

1 ቤታቸው ፡ በሚያምሩ ፡ አበቦች ፡ አጊጦ ፡ ይታይ ፡ ነበር ።
2 የጊቶችን ፡ ዋንጫ ፡ ፈልገን ፡ አጣነው ። } (የቄሳቍስ)፡

1 አንዳንድ፡ቤቶች፡ መሠረት ፡ ስለሌላቸው፡በቶሎ ፡ ይፈርሳሉ ።
2 ዋንጫ ፡ ከቀንድ ፡ ይበጃል ። } (የወል) ፡

የነገር ፡ (የረቂቅ) ፡ ስሞች ፡

በእጅ ፡ የማይዳሰሱ ፡ በዐይን ፡ የማይታዩ ፡ ዐይነትን ፡ ግብርን ፡ ሁኔታን ፡ የሚያ መለክቱ ፡ ስሞች ፡ ናቸው ።

ምሳሌ ፡-

(ሀ) ዐይነት ፡ ድንቍርና ፡ መልክ ፡ ዐዋቂነት ፡ ብልኀነት ፡ ሥልጡንነት ፡ ትልቅነት ፡
(ለ) አኳኋን ፡ ድኀነት፡ ራብ ፡ እስራት ፡ ግዞት ፡ ደስታ ፡ ኀዘን ፡ ዕርዛት ፡
(ሐ) ግብር ፡ ሌብነት ፡ ቀማኛነት ፡ ጨካኝነት ፡ ወስላታነት ፡ ደግነት ፡ ክፉነት ፡ ጠንካራነት ፡

፪ኛ ፡ በስም ፡ ፈንታ ፡ (እንደ ፡ ስም) ፡ የሚሠሩ ፡

በስም ፡ ፈንታ ፡ የሚሠሩ ፡ ዐይነቶች ፡

(ሀ) ተውላጠ ፡ ስም ።

ምሳሌ ፡- የኔ ፡ ብርዕ ፡ አዲስ ፡ ነው ፤ ያንተ ፡ (ብርዕ) ፡ ግን ፡ አሮጌ ፡ ነው፡ (ብርዕህ) ።
እርሱ ፡ ወንድሙን ፡ ያስተምራል ።

(ለ) ቅጽል ፡

ምሳሌ ፡- ደንቆሮው ፡ ተኝቷል ።

(ሐ) አርእስት ፡

ምሳሌ ፡ መንቀፍን ፡ ያበዛል ፡ (ነቀፌታን ።

(መ) መንቀፍ ፡ ጠብን ፡ ያበዛል ።

(ሠ) ሳቢ ፡ ዘር ፡

ምሳሌ ፡ ደብዳቤ ፡ አጻጻፍን ፡ ማን ፡ አስተማረህ ?

(ረ) ስማዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡

ምሳሌ ፡ ከሁሉ ፡ አስቀድሚ ፡ ደብዳቤ ፡ የጻፈልኝን ፡ አመሰግናለሁ ።

(ሰ) ዘር ፡ ሐሰትን ፡ አትናገር ።

፫ኛ ፡ ጾታ ፡

የጾታ ፡ መግለጫ ፡

ወገንነትን ፡ የሚያመለክት ፡ ቃል ፡ ነው ። ማናቸውም ፡ ሕይወት ፡ ያለው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ጾታ ፡ አለው ፤ ሕይወት ፡ የሌለው ፡ የሆነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ግን ፡ የሴትና ፡ የወንድ ፡ ጾታ ፡ ስለሌለው ፡ ግዑዝ ፡ ጾታ ፡ ተብሎ ፡ ይጠራል ።

## የጾታ ፡ ዐይነቶች ፡ ፬ ፡ ናቸው ።

(ሀ) ወንዴ ፡ ጾታ ፡ (ተባዕታይ) ፡ (ሐ) የወል ፡ ጾታ ፡

(ለ) ሴቴ ፡ ጾታ ፡ (አንስታይ) ፡ (መ) ግዑዝ ፡ ጾታ ፡

(ሀ) ወንዴ ፡ ጾታ ፡ በባሕርዩ ፡ የወንድ ፡ መለዮ ፡ ያለው ፡ ነው ።

ምሳሌ ፡- ተቀባ ፡ መንግሥቱ ፡ ማስረሻ ፡ ዘለቀ ፡ መኰንን ፡ መሸሻ ፡ ጌታቸው ፡
አባ ፡ ካሣ ፡ አማች ፡ አጎት ፡ ወንድም ፡ ወይፈን ፡ ወጠጤ ፡ ድንጉላ ፡

(ለ) ሴቴ ፡ ጾታ ፡ በባሕርዩ ፡ የሴት ፡ እንጂ ፡ የወንድነት ፡ መለዮ ፡ የሌለው ፡ ነው ።

ምሳሌ ፡- አበበች ፡ ፈለቀች ፡ በላይነሽ ፡ ከበቡሽ ፡ አያት ፡ እናት ፡
አክሥት ፡ ላም ፡ ጊደር ፡ ቄብ ፡

(ሐ) የወል ፡ ጾታ ፡ በባሕርያቸው ፡ የወንድና ፡ የሴት ፡ መለዮ ፡ ያላቸው ፡ ነገሮች ፡ ባንድነት ፡ የሚጠሩበት ፡ የጋራ ፡ ጾታ ፡ ነው ። እንደዚህ ፡ ያለው ፡ ስም ፡ በነጠላ ፡ «እኔ» ፡ ከሚለው ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ በስተቀር ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ በተገለጠ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ጾታውን ፡ ለይቶ ፡ ያስታውቃል ። በእውነተኛው ፡ ነገር ፡ የወል ፡ ጾታ ፡ የተረጋገጠ ፡ የሚሆነው ፡ በብዙ ፡ ቊጥር ፡ በተነገረ ፡ ጊዜ ፡ ነው ።

ምሳሌ ፡- አያት ፡ ጥጃ ፡ መንጋ ፡ እንስሳት ፡ ሰው ፡ ማኅበረተኛ ፡ ፈረስ ፡ ከብት ፡

(መ) ግዑዝ ፡ ጾታ ፡—በባሕርዩ ፡ (ውስጥ) ፡ የወንድና ፡ የሴት ፡ መለዮ ፡ የሌለበት ፡ ነው ። እንዲህ ፡ ከሆነ ፡ ማናቸውም ፡ ሕይወት ፡ የሌለው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በዚህ ፡ ክፍል ፡ መጠቅለል ፡ አለበት ። አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ግዑዝ ፡ ጾታ ፡ በልማድ ፡ በወንድም ፡ በሴትም ፡ ጾታ ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ይነገራል ።

<u>ምሳሌ ፡-</u>

1 ምድር ፡ ድንጋይ ፡ ተራራ ፡ መጽሐፍ ፡ ወንዝ ፡ ዝናም ፡ ደመና ፡ ባሕር ፡

2 ምድር ፡ ትዞራለች ፡ ብለው ፡ መምህራን ፡ ያስተምራሉ ።

## ፬ኛ ፡ ሙያ ፡

ሙያ ፡ ስሞች ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ገቡ ፡ የምናውቅበት ፡ ክፍል ፡ ነው ።

<u>አስረጅ ፡-</u>

1 መንግሥቱ ፡ ልብሱን ፡ ይተኵሳል ።

2 ችግኙ ፡ ዘወትር ፡ ውኃን ፡ ይፈልጋል ።

ባንደኛው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ባለቤቱ ፡ መንግሥቱ ፡ ነው ። ማን ፡ ይተኵሳል ፡ ተብሎ ፡ ለሚቀርበው ፡ ጥያቄ ፡ መልሱ ፡ «መንግሥቱ ፡ ነው» ፡ «ልብሱን ፡ ይተኵሳል» የሚባሉት ፡ ቃላት ፡ ባንድነት ፡ ያንቀጽ ፡ ወገን ፡ መሆናቸው ፡ ነው፤ ያንቀጽ ፡ ወገንም ፡ ማሠሪያ ፡ አንቀጹን ፡ ይተኵሳልን ፡ ይዟል ።

መንግሥቱ፡ ምንን ፡ ተኰሰ? ልብሱን ፡ ተኰሰ። ልብስ፡ መንግሥቱ ፡ የተኰሰው ፡ ነገር ፡ ነው ፤ ስለዚህ ፡ ልብስ ፡ ያንቀጹ ፡ ድርጊት ፡ ያረፈበት ፡ ስለ፡ሆነ ፡ ተሳቢ ፡ ይባላል።

በሁለተኛው፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ባለቤቱ፡ ችግኙ ፡ ነው። ምንን፡ ይፈልጋል፡ ተብሎ፡ ለሚጠየቀው ፡ ጥያቄ ፡ መልሱ ፡ «ውኃን» ፡ ነው ። ውኃ ፡ ተሳቢ ፡ ነው ፤ ችግኙ ፡ የሚፈልገው ፡ ነገር ፡ እርሱ ፡ ነውና ።

ባለቤት ፦ አንድ ፡ ስም ፡ (ተውላጠ ፡ ስም) ፡ ባንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ላንቀጹ ፡ ዋና ፡ የሆነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ባለቤት ፡ ይባላል ።

እንደዚሁም ፡ አንድ ፡ ስም ፡ (ተውላጠ ፡ ስም) ፡ ያንቀጹ ፡ ግብር ፡ የተገለጸበት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ (ያንቀጹ ፡ ሥራ ፡ ያረፈበት ፡ እንደ፡ ሆነ)፡ ቀጥተኛ ፡ ተሳቢ ፡ ተብሎ ፡ ይጠ ራል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ባንድ ፡ ስም ፡ ላይ ፡ ያንቀጹ ፡ ግብር ፡ ሳይገለጽበት ፡ በመስተዋድድ ፡ የተገዛ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የመስተዋድድ ፡ ተገዥ ፡ ተብሎ ፡ ይጠራል ።

አንድ ፡ ስም ፡ በመስተዋድድ ፡ ከተገዛ ፡ በኋላ ፤ ኢ-ርቱዕ ፡ ተሳቢ ፡ ተብሎ ፡ ሊነ ገር ፡ አይገባውም ። ለምሳሌ፦ አንድ ፡ ሰው ፡ ሁለት ፡ እግር ፡ አለኝ ፡ ብሎ ፡ ባንድ፡ጊዜ፡ እሁለት ፡ ዛፍ ፡ ላይ ፡ ሊወጣ ፡ አይችልም ። እንደዚሁም ፡ አንድ፡ ስም ፡ በመስተዋድድ፡ ከተገዛ ፡ በኋላ፡ ለተሻጋሪ፡ ግስ፡ ወይም፡ ለማይሻገር ፡ ግስ ፡ ተሳቢ ፡ ሊሆን፡ አይችልም ።

መስተዋድድና ፡ ስም ፡ ባንድነት ፡ ገዥና ፡ ተገዥ ፡ ሆነው ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ አገባብ ፡ አላቸው ፤ አገባባቸውም ፡ ቅጽል ፡ ወይም ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ መሆን ፡ ነው ።

ምሳሌ ፦

1 ብዙ ፡ ልጆች ፡ ከፍተኛ ፡ ትምህርትን ፡ ለማግኘት ፡ ወደ ፡ ለንደን ፡ ሄዱ ።
2 በቤት ፡ ውስጥ ፡ ልጆች ፡ ይጮሃሉ ።

እንሆ ፡ ባ፩ኛው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ «ለማግኘትና ፡ ወደ ፡ ለንደን ፡» መስ ተዋድዳን ፡ ንኡስ ፡ ሐረጎች ፡ ናቸው ። ለማግኘት፦ ለምን ፡ እንደ ፡ ሄዱና ፡ ወደ ፡ ለንደን፡ ወዴት ፡ እንደ ፡ ሄዱ ፡ ይገልጻሉ ፤ ስለዚህ ፡ ሁለቱም ፡ ተውሳካተ ፡ ግስ ፡ ናቸው ።

በ፪ኛው፡ አረፍተ ፡ ነገር፡ ውስጥ፡ በቤት ፡ ውስጥ፡ መስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ፡ ሐረግ፡ ነው ። አገባቡም ፡ እንደ ፡ ቅጽል ፡ ሆኖ ፡ ነው ። ትርጓሜውም ፡ «በቤት ፡ ውስጥ ፡ ያሉት» ፡ ልጆች ፡ ይጮሃሉ ፡ ማለት ፡ ነው ።

እንግዴህ ፡ አንድ ፡ ስም ፡ በመስተዋድድ ፡ ከተገዛ ፡ ኢ-ርቱዕ ፡ ተሳቢ ፡ ይሆናል ፡ ማለት ፡ እንዳይገባ ፡ መርምሮ ፡ መረዳት ፡ ያስፈልጋል ።

ባዲሱ ፡ ሰዋስው ፡ አካሄድ ፡ ኢ-ርቱዕ ፡ ተሳቢ ፡ የምንለው ፡ የመስተዋድድ ፡ ቃል፡ ውስጠ ፡ ታዋቂ ፡ ሆኖ ፡ የጐደለውን ፡ ነው ። አንቀጹ ፡ ተሻጋሪ ፡ ሆኖ ፡ የመስጠትን፡ምግ ባር ፡ ካላመለከተ ፡ ማናቸውም ፡ ተሻጋሪ ፡ ግስ ፡ ኢ-ርቱዕ ፡ ተሳቢን ፡ አያስገኝም ። ባንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ኢ-ርቱዕ ፡ ተሳቢ ፡ ሲገኝ ፡ የግዴታ ፡ ቀጥተኛ ፡ (ርቱዕ) ፡ተሳቢ፡ ደግሞ ፡ በውስጡ ፡ መገኘት ፡ አለበት ፤ ስለዚህ ፡ ኢ-ርቱዕ ፡ ተሳቢ ፡ የመስተዋድድ ፡ ቃል ፡

ጕድሎት ፡ የመስጠትን ፡ ምግባር ፡ በሚያመለክት ፡ ተሻጋሪ ፡ ግስ ፡ ከቀጥተኛ ፡ ተሳቢ ፡ ጋራ ፡ የሚገዛ ፡ ተሳቢ ፡ ነው ። ያልተተካከለ ፡ ድርብ ፡ ተሳቢ ፡ የሚለውን ፡ ተመልከት ።

## ስም ፡ በተጣማሪነት ።

ተጣማሪ ፡- የተጣመረለት ፡ ስም ፡ በሚዘረዘርለት ፡ ሙያ ፡ ይዘረዘራል ።

አስረጅ ፡

አቶ ፡ ማንደፍሮት ፡ ታላቁ ፡ ነጋዴ ፡ በስንት ፡ ትግል ፡ ያስመጡትን ፡ ቦንዳ፡ ላቶ፡ በፈቃዱ ፡ በርካሽ ፡ ዋጋ ፡ ሸጡለት ።

የዚህ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ባለቤት ፡ አቶ ፡ ማንደፍሮት ፡ ነው ፤ ነጋዴ ፡ የሚለውም ፡ ስም ፡ የሚያመለክተው ፡ አቶ ፡ ማንደፍሮትን ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ባለቤት፡ መሆን ፡ አለበት ።

## የስም ፡ ዝርዝር ፡ አፈታት ፡ ዘዴ ፡

ስምን ፡ መዘርዘር ፡ በሚከተሉት ፡ አኳኋን ፡ ነው ።

(፩) የስም ፡ ዐይነቱን ፡
(፪) ጾታውን ፡
(፫) ቍጥሩን ፡
(፬) ሙያውን፡- ባለቤት ፡ ቀጥተኛ ፡ ተሳቢ ፡ ኢ-ርቱዕ ፡ ተሳቢ ፡ የመስተዋድድ ፡ ተገዥ ፡
(፭) ከሌሎች ፡ ቃላት ፡ የሚዛመድበትን ፡ (ባንድነት) ፡

ምሳሌ ፡-

1 ደመቀ ፡ ዛፉን ፡ መለመለው ።

ደመቀ ፡- የተጸውዖ ፡ ስም ፡ ወንዴ ፡ ጾታ ፡ ነጠላ ፡ ቍጥር ፡ ሙያው ፡ ባለቤት ፡ ባለቤትነቱ ፡ ለማሠሪያ ፡ አንቀጹ ፡ «መለመለው» ፡ ለሚለው ፡

ዛፍ ፡- የጥቅል ፡ ስም ፡ የወል ፡ ጾታ ፡ ነጠላ ፡ ቍጥር፡ ሙያው ፡ ቀጥተኛ ፡ ተሳቢ ፡ ተሳቢነቱም ፡ ለአንቀጹ ፡ «መለመለው» ፡ ነው ።

2 ባልጋው ፡ ሥር ፡ አንዲት ፡ ጊንጥ ፡ አለፈች ።

አልጋ ፡ የቍሳቍስ ፡ ስም ፡ ግዑዝ ፡ ጾታ ፡ ነጠላ፡ ቍጥር ፡ ሙያው፡ የተደራራቢ፡ መስተዋ ድዳን ፡ ተገዥ ፡ ተገዥነቱም ፡ ለመስተዋድዶች ፡ «በ- ሥር» ፡ ነው ።

ባልጋው ፡ ሥር ፡ ባንድነት ፡ ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ተውሳከ ፡ ግስነ ቱም ፡ ለማሠሪያ ፡ አንቀጹ ፡ «አለፈች» ፡ ነው ።

## ፩ኛ ፡ መልመጃ ፡

በሚከተሉት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ የምታገኛቸውን ፡ ስሞች ፡ ሁሉ ፡ በዝ ርዝር ፡ አፈታት ፡ ደንብ ፡ ዘርዝራቸው ።

1 ትንኞችን ፡ እንፍጃቸው ።
2 ወንድሜ ፡ ባንድ ፡ ሳምንት ፡ ውስጥ ፡ ብዙ ፡ ገንዘብን ፡ አገኘ ።
3 ጌቶች ፡ በገበታ ፡ ላይ ፡ ናቸው ።

4 በልጅ ፡ ነገር ፡ ከብዙ ፡ ደርሻለሁ ።
5 አስማ ፡ ይዞ ፡ ያሠቃየኛል ፤ በዚያውም ፡ ላይ ፡ ጉንፋን ፡ ይዞኛል ።
6 መኰንን ፡ እንደ ፡ ደበበው ፡ ሁሉ ፡ የሊቅነትን ፡ ማዕርግ ፡ አገኘ ።

## ፰ኛ ፡ ቍጥር ፡

__መግለጫ__ ፡- ቍጥር፡ ማለት ፡ በዚህ ፡ ሰዋስው ፡ ክፍል ፡ ነጠላ ፡ ስም ፡ ወይም፡ አንዱ፡ ስም፡ ወደ ፡ ብዙነት ፡ የሚለወጥበትን ፡ ዘዴ ፡ የሚያስተምረን ፡ አንድ ፡ የሰዋስው ፡ ክፍል ፡ ነው ።

__አብነቶች__ ፡

ስሞች ፡ በሚከተሉት ፡ ዐይነቶች ፡ ይበዛሉ ።

ዎች-የያንዳንዱ፡ ስሞች ፡ የመጨረሻ፡ ፊደላቸው፡ ሳይለወጥ፡ «ዎችን»፡ መጨመር።

ች-የያንዳንዱን ፡ ስሞች ፡ የመጨረሻ ፡ ፊደላቸውን ፡ ወደ ፡ ራብዕ ፡ መለወጥና፡ «ችን» ፡ መጨመር ፡

«ት» ፡ በግእዝ ፡ ደንብ ፡ የመጨረሻ ፡ ፊደሉን ፡ ወደ ፡ ራብዕ ፡ ለውጦ ፡ «ት»ን ፡ መጨመር ።

__ምሳሌ__ ፡-

| | ነጠላ ፡ | ብዙ ፡ | ነጠላ ፡ | ብዙ ፡ | ነጠላ ፡ | ብዙ ፡ |
|---|---|---|---|---|---|---|
| ፩ኛ ፡ | መሪ ፡ | መሪዎች ፡ ፪ኛ ፡ | አስተያየት ፡ | አስተያየቶች ፡ | ወንፊት ፡ | ወንፊቶች ። |
| | ገበቴ ፡ | ገበቴዎች ፡ | ሚዳቋ ፡ | ሚዳቆች ፡ | እንቅብ ፡ | እንቅቦች ፡ |
| | ጸሓፊ ፡ | ጸሐፊዎች ፡ | መሶብ ፡ | መሶቦች ፡ | ሰፌድ ፡ | ሰፌዶች ፡ |
| | ዝማሪ ፡ | ዝማሪዎች ፡ | በግ ፡ | በጎች ፡ | ዐጸድ ፡ | ዐጸዶች ፡ |
| | አስተማሪ፡ | አስተማሪዎች፡ | ጥጃ ፡ | ጥጆች ፡ | ፍየል ፡ | ፍየሎች ፡ |
| | ዋንጫ ፡ | ዋንጮች፡ | ጥንቸል፡ | ጥንቸሎች፡ | ቁና ፡ | ቁናች ፡ |
| | መጥረቢያ ፡ | መጥረቢያዎች፡ | ቀበሮ ፡ | ቀበሮች ፡ | እርቦ ፡ | እርቦች ፡ |
| ፫ኛ ፤ | መንግሥት ፡ | መንግሥታት ፡ | | | ዕፅ ፡ | ዕፀዋት ፡ |
| | አንበሳ ፡ | አናብስት ፡ | | | አርዌ ፡ | አራዊት ፡ |
| | ንጉሥ ፡ | ነገሥት ፡ (ነገሥታት ፡ | | | መንፈስ፡ | መናፍስት፡ |

## ፱ኛ ፡ መልመጃ ፡

(ሀ ከዚህ ፡ በታች ፡ የተጻፉትን ፡ ስሞች ፡ በየዐይነታቸው ፡ ለያቸው ።

| | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|
| ድምፅ ፡ | ሹመት ፡ | ዛፍ ፡ | ምላጭ ፡ | አበበ ፡ | ታችበሌ ፡ | አርነት ፡ |
| መከራ ፡ | ማዕርግ ፡ | ባሕርይ ፡ | ጠባይ ፡ | በቀለ ፡ | ዓለማየሁ ፡ | አሳብ ፡ |
| መማሪያ ፡ | ጉባኤ ፡ | ዱላ ፡ | ምኞት ፡ | ዘውዴ ፡ | እጅጋየሁ ፡ | ፈቃዱ |
| ውኃ ፡ | ሊቅ ፡ | ሰንጢ ፡ | ጥጋብ ፡ | ሙላቱ ፡ | ወጋየሁ ፡ | ኀይል ፡ |
| ተቀባ ፡ | ቤት ፡ | ችግር ፡ | ረኃብ ፡ | ካሳዬ ፡ | ክብር ፡ | ቀበቶ ፡ |

ከብት ፡ ተማሪ ፡ ችግር ፡ ንዴት ፡ ወንዳፍራሽ ፡ ባለጸግነት፡ማሲኖዳ፡ አዝመራ ፡ ሕይወት ፡ መሪ ፡ እርሻ ፡ ባርኔጣ ፡ ጨቤ ፡ ነገድ ፡ ዳስ ፡ እንስሳ ፡ ጸሓፊ ፡ ቀንበር፡ መለዮ ፡ ቅትርት፡ በሽታ ፡ ደስታ ፡ ወፍ ፡ ነፍሳት ፡ ፍሬ ፡

(ለ) ከዚህ ፡ በታች ፡ ከሚገኙት ፡ አርፍተ ፡ ነገሮች ፡ ስሞችን ፡ ልቀም ።

ቍጥራቸውን ፡ ተናገር ።

ጾታቸውን ፡ ተናገር ።

(ሐ) በብዙ ፡ የተጻፉትን ፡ ወደ ፡ ነጠላ ፡ በነጠላ ፡ የተጻፉትን ፡ ወደ ፡ ብዙ ፡ ለውጣቸው ።

1 በቅሎ ፡ ጠንካራና ፡ አደጋ ፡ ቻይ ፡ በመሆኗ ፡ በቆላና ፡ በደጋ ፡ ትኖራለች ።
2 አንድ ፡ የባዕድ ፡ አገር ፡ ነጋዴ ፡ ያገራችንን ፡ ሀብት ፡ ከመዝረ ፡ በስተቀር፡ ርዳታን ፡ አያደርግም ።
3 የከፍተኛው ፡ ያባይ ፡ ፋፋቴ ፡ ዝና፡ ገኖ ፡ ባለም ፡ የሚታወቀው ፡ ሲሠራበት፡ ነው ።
4 ልጁ ፡ ሰነፍ ፡ ብጤ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የበቃ ፡ ትምህርትን ፡ አያገኝም ።
5 ቀይ ፡ ፈረስ ፡ ላይን ፡ ያስደስታል ።
6 29 ልጆች ፡ ለሁለተኛ ፡ ደረጃ ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ ታጭተዋል ።
7 አያሌ ፡ ተማሪዎች ፡ በሚመጣው ፡ ዓመት ፡ ይመረቃሉ ።
8 እነዚህ ፡ ወጣቶች ፡ በችግኝ ፡ ይመስላሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ፡ ቅጽል ፡

**መግለጫ ፦**

ቅጽል ፡ ( ቅጥያ) ፡ በስም ፡ ላይ ፡ እየተቀጠለ ፡ ስምን ፡ የሚገልጽ ፡ ነው ።

ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ያንቀጽ ፡ ባለቤት ፡ በግድግዳ ፡ ይመስላል ። አንድ ፡ ግድግዳ ፡ መዠመሪያ ፡ ቀጥ ፡ ብሎ ፡ እንዲቆም ፡ ማገርና ፡ ልጥ ፡ ወይም ፡ አረግ ፡ ያስፈ ልጉታል ። እነርሱም፡ልስቅ፡(ልጥቅ) ፡ አድርገው ፡ ከያዙት፡(ካቆሙት) ፡ በኋላ ፡ የሚያስ ፈልገው ፡ በደንብ ፡ በጭድ ፡ ተረግጦ ፡ የቦካ ፡ ጭቃ ፡ ነው ። በማገር ፡ ተገዝቶ ፡ ልክ ፡ የገባው ፡ ግድግዳ ፡ በጭቃ ፡ ተመርጎ፡ እንደ ፡ ገና፡ እየተደጋገመ፡ በተለሰነ፡ ጊዜ ፡ አባጣ፡ ጎባጣ ፡ መሆኑ ፡ ቀርቶ ፡ የተተካከለ ፡ ይሆናል ። እንዲሁም ፡ ላንድ ፡ ባለቤት ፡ እንደ ፡ ልጥና ፡ እንደ ፡ ማገር ፡ አቃንቶ ፡ ለስቆ ፡ የሚይዘው ፡ አንቀጽ ፡ ያስፈልገዋል ።

ይህ ፡ ቤት ፡ አሁን ፡ ቀዳዳና ፡ ጭላንጭል ፡ አለው ፤ ገና ፡ ፍጹም ፡ አልሆነም ፤ ስለዚህ ፡ የጐደለውን ፡ ሞልቶና ፡ ስሜቱን ፡ ከፍ ፡ አድርጎ ፡ የሚገልጸው ፡ ቅጽል ፡ የተ ባለ ፡ የቦካ ፡ ጭቃ ፡ ያስፈልጋል ።

ቅጽልን ፡ በሌላ ፡ መልክ ፡ ስንመለከተው ፡ ላንቀጽ ፡ ባለቤት ፡ እንደ ፡ ጌጠኛ ፡ ፈረስ ፡ ዕቃ ፡ ጌጡ፡እንደ ፡ ወርቀ ፡ ዘቦ፡ ካባ ፡ ሸልማቱ፡ እንዳውራሪሥ፡ ጎራዴና ፡ እንደ፡ አንበሳ ፡ ጎፈር ፡ መሰለፊያው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፤ እንዲሁም ፡ ዘርፍና ፡ ተሳቢን ፡ በደንብ ፡ እያስማማ ፡ ላንቀጹ ፡ ባለቤት ፡ የሚያደርገውን ፡ አገልግሎት ፡ ሳያጓድል ፡ ይገል ጻቸዋል ።

ቅጽል ፡ ስሞችን ፡ እየካበ ፡ እንደሚያሳድጋቸው ፡ ሁሉ ፡ እያጥፋፉ ፡ እያጥላላና፡ (እያረካከሰ) ፡ እያኪያኪያሰ ፡ ይጥላቸዋል ። ቤትን ፡ የቦካ ፡ ጭቃ ፡ እንደሚያሳምረው፡ በሚፈርስበትም ፡ ጊዜ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ማፍረሻ ፡ መሣሪያዎች ፡ ያስፈልጉታል ፤ እንደ ዚሁም ፡ ቅጽል ፡ በመካብ ፡ ፈንታ ፡ ያፈርሳል ።

ሰው ፡ ባለማስተዋልና ፡ ባለመገንዘብ ፡ የማናቸውንም ፡ ነገሮች ፡ እውነተኛ ፡ አገልግሎታቸውን ፡ በዝቅተኛነት ፡ ይገምተዋል ፡ እንጂ ፡ ቀረብ ፡ ብሎ ፡ ደኅና ፡ አድ ርጎ ፡ ለተመለከተው ፡ ሰው ፡ አንዱ ፡ ነገር ፡ ከሌላው ፡ ዘንድ ፡ የማይገኘውን ፡ ልውጥ ፡ ነገር ፡ ይዞ ፡ ይገኛል ። ልዩ ፡ ልዩ ፡ ነገሮች ፡ ባቀነባበሪያቸው ፡ ብርታት ፡ ተድራጅተው፡ (ተገጣጥመው) ፡ ሲገኙ ፡ ታላቅ ፡ ስሜትን ፡ ስለሚሰጡ ፡ ያንደኛው ፡ ጥቅም ፡ በቀላሉ ፡ ምን፡ እንደ፡ ሆነ ፡ ሊታወቅ ፡ አይቻልም ፤ ከውስጡ፡ ግን ፡ አንዳንዱን ፡ እያወጡ ፡ (እየ መዘዙ) ፡ ቢጥሉት ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ጐደለው ፡ ሊታወቅ ፡ ይችላል ። ስለዚህ ፡ ቅጽል ፡ ለስም ፡ ትክክለኛ ፡ መልክና ፡ ቅርጽ ፡ ከመስጠቱ ፡ በላይ ፡ ጌጡ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፤ እንደ ፡ ትንሽ ፡ ነገር ፡ ቅጥያ ፡ እየተባለ ፡ በትንሹ ፡ ሊገመት ፡ አያስፈልግም ።

## ፩ ፡ የቅጽል ፡ ዐይነቶች ።

የቅጽል ፡ ዐይነቶች ፡ ስድስት ፡ ናቸው ።

(ሀ) የወገን ፡ ቅጽል ፡
(ለ) ሥዕላዊ ፡ ቅጽል፡- ገላጭ፡ ቅጽል።
(ሐ) የአኃዝና ፡ የመጠን ፡ ቅጽል ፡
(መ) አመልካች ፡ ቅጽል፡
(ሠ) አደላዳይ ፡ ቅጽል ፡
(ረ) መጠይቅ ፡ ቅጽል ፡

(ሀ) የወገን ፡ ቅጽል ፡ አንድ ፡ ሰውን ፡ የማን ፡ አገር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የሚያመለክት ፡ ቅጽል ፡ ነው ።

ስሞች ፡ «ዊ» ፡ «ውያን» ፡ «ዊት» ፡ ና ፡ «ውያት» ፡ እየተጨመሩባቸው ፡ የወ ገን ፡ ቅጽል ፡ ይሆናሉ ።

ምሳሌ ፡-

(ሀ) ዊ ፡ ውያን ፡
አሜሪካዊ ፡ ( (ያሜሪካ ፡ አገር ፡ ሰው) ፡
አሜሪካውያን ፡
(ያሜሪካ ፡ ሰዎች) ፡
ዊት ፡ ውያት ፡
አሜሪካዊት ፡ (ያሜሪካ ፡ አገር ፡ ሴት) ።

አሜሪካውያት ፡
(ያሜሪካ ፡ ሴቶች ) ፡

(ለ) በተለይ ፡ በጠቅላይ ፡ ግዛቶች ፡ ባውራጃዎችና ፡ በወረዳዎች ፡ ጥቂት ፡ ይለያል ።

| | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|
| የጁ ፡ | የጁዬ ፡ | ላስታ ፡ | ላስቴ ፡ | ሲዳሞ ፡ | ዲዳሞዬ ፡ |
| ሸዋ ፡ | ሸዌ ፡ | ወሎ ፡ | ወሎዬ ፡ | ሐረር ፡ | ሐረርጌ ፡ |

(ለ) ሥዕላዊ ፡ ቅጽል ፡ (ገላጭ ፡ ቅጽል) ፡

የሰውን ፡ ወይም ፡ የእንስሳን ፡ ወይም ፡ የማናቸውንም ፡ ሥራ ፡ ( ግብር) ፡ የሚ ገልጽና ፡ መጠንንና ፡ መልክን ፡ እያጐላ ፡ የሚያሳይ ፡ ቅጽል ፡ ነው። ሥዕላዊ ፡ ቅጽል ፡ በሁለት ፡ ንኡሳን ፡ ክፍሎች ፡ ይከፈላል ።

፩ ፡ የግብር ፡

የሰውን ፡ የእንስሳንና ፡ የማናቸውንም ፡ ነገር ፡ ሥራ ፡ ( ግብር)፡ የሚያመለክት፡ ቅጽል ፡ ነው ።
ምሳሌ፡ ደግ ፡ ቸር ፡ ክፉ ፡ ንፉግ ፡ ጨካኝ ፡ ርኅሩኅ ፡ ሆዳም ፡ አሲዳም ፡ ኀጢአተኛ ፡ ባለጌ ፡ ዳተኛ ፡ ወሬኛ ፡ ጦረኛ ፡ እልከኛ ፡ ውሸታም ፡ ቅንቅናም ፡ ሥጋዊ ፡

መሰልነትን ፡ የሚመለከቱና ፡ ድጋፍን ፡ የሚፈልጉ ፡ ቃላት ፡ በዚሁ ፡ ይጠቀ ለላሉ ።

፪ ፡ ያይነት ፡ ቅጽል፡- መጠንንና ፡ መልክን ፡ እየገለጸ፡የሚያሳይ፡ቅጽል፡ነው ።

ምሳሌ ፡-

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| ቀይ ፡ | ግራጫ ፡ | ዋርዳ ፡ | አጭር ፡ | በቂ ፡ |
| ጥቁር ፡ | ቡሬ ፡ | ሳሙና ፡ | ረዥም ፡ | ጥቂት ፡ |
| ነጭ ፡ | ጡርጡሬ ፡ | ቦቃ ፡ | ወፍራም ፡ | |
| ብጫ ፡ | ጫጉማ ፡ | ዶግማ ፡ | ጐናም ፡ | |
| ቡላ ፡ | ሸክላ ፡ | አሻልማ ፡ | | |
| ቡና ፡ | ዳለቻ ፡ | የቀይ ፡ ዳማ ፡ | ፈሳሽ ፡ | |

(ሐ) የአኃዝና ፡ የመጠን ፡ ቅጽል ፡ አንድ ፡ ሁለት ፡ እያለ ፡ በትክክል ፡ የተወሰነውን ፡ ቍጥር ፡ የሚያመለክተን ፡ ወይም፡ አንድ ፡ ነገር ፡ መብዛቱን ፡ ወይም ፡ ማነሱን ፡ የሚያ መለክት ፡ የቅጽል ፡ አንድ ፡ ታናሽ ፡ ክፍል ፡ ነው ። የአኃዝና ፡ የመጠን ፡ ቅጽል ፡ በ፪፡ ንኡሳን ፡ ክፍሎች ፡ ይከፈላል ።

(ሀ) የተወሰነ ፡ የአኃዝ ፡ ቅጽል ፡ አንድ ፡ ሁለት ፡ እያለ ፡ በትክክል ፡ የተወ ሰነውን ፡ ቍጥር ፡ የሚያመለክት ፡ ቅጽል ፡ ነው ።

፩ ፡ መደበኛ ፡

ምሳሌ ፡- 1 ፡ 2 ፡ 3 ፡ 4 ፡ 5 ፡ እንደዚህ ፡ እያለ ፡ ይቀጥላል ።

፪ ፡ ሕገኛ ፡

ምሳሌ ፡- 1ኛ ፡ 2ኛ ፡ 3ኛ ፡ 4ኛ ፡ 5ኛ ፡ እንደዚህ ፡ እያለ ፡ ይቀጥላል ።

(ለ) ያልተወሰነ ፡ የአኃዝ ፡ ቅጽል ፡ (የመጠን ፡ ቅጽል) ፡

ያልተወሰነ ፡ የአኃዝ ፡ ቅጽል ፡ የሚባለው ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ መብዛቱንና ፡ ማነሱን ፡ እያመለከተ ፡ የተወሰነውን ፡ ቊጥር ፡ ለማመልከት ፡ የማይችል ፡ ነው ።

ምሳሌ ፡-

እጅግ ፡ ብዙ ፡ ጥቂት ፡ ግማሽ ፡ አያሌ ፡ ፩፪ ፡ ያህል ፡

(መ) አመልካች ፡ ቅጽል ፡

አመልካች ፡ ቅጽል ፡- ቦታን፡ በአእምሮ ፡ ውስጥ ፡ የታወቀውን ፡ ነገርና ፡ በቦታና ፡ በአእምሮ ፡ ውስጥ ፡ ያልታወቀውን ፡ የሚያመለክት ፡ ቅጽል ፡ ነው ።

አመልካች ፡ በሁለት ፡ ይከፈላል ።

(ሀ) የተወሰነ ፡ አመልካች ፡

(ለ) ያልተወሰነ ፡ አመልካች ፡

(ሀ) ፩ ፡ የተወሰነ ፡ አመልካች ፡ በቅርብና ፡ በሩቅ ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ እየለየ ፡ የሚያመለክት ፡ ቅጽል ፡ ነው ። በቦታ ፡ መቅረብና ፡ መራቅ ፡ ይወሰናል ።

ምሳሌ ፡-

| ቅርብ ፡ | ሩቅ ፡ | ቅርብ ፡ | ሩቅ ፡ |
|---|---|---|---|
| ይህ ፡ | ያ ፡ | እሊህ ፡ | እሊያ ፡ |
| ይህች ፡ | ያች ፡ | እኒህ ፡ | እኒያ ፡ |
| እነዚህ ፡ | እነዚያ ፡ | | |

ማስገንዘቢያ ፡- ቦታውንና ፡ ሰውዬውን ፡ ያሳያሉ ።

፪ ፡ በአእምሮ ፡ ውስጥ ፡ የታወቀውን ፡ ነገር ፡ የሚያመለክት ፡ ቅጽል ፡ ነው። የተጠቀሰው ፡ ነገር ፡ ወይም ፡ ሰው ፡ ያለበትን ፡ ቦታ ፡ አያመለክትም ።

ምሳሌ ፡- ካዕብ ፡ ፊደል ፡ ዮው ፡ ዬው ፡ ዮዋ ፡ ዩቱ ፡

ጠረጴዛው ፡ ወንፊቱ ፡ ልጅዮው ፡ ሰውዬው ፡ ሴትዮዋ ፡ ጎንደሬዩቱ ፡

(ለ) ያልተወሰነ ፡ አመልካች ፡ በአእምሮ ፡ ውስጥ፡ ተለይቶ ፡ ያልታወቀውን ፡ ነገር ፡ የሚያመለክት ፡ ቅጽል፡ ነው ። (በአእምሮ ፡ ውስጥ ፡ ወይም ፡ በቦታ ፡ አልተወሰነም) ።

ምሳሌ ፡-

ወንበር ፡ አንድ ፡ ወንበር ፡ ብርዕ ፡ አንድ ፡ ብርዕ ፡ ሌላ ፡ ማናቸውም ፡ አንድም

(ሠ) አደላዳይ ፡ (ተንታኝ) ፡ ቅጽል ፡

ከሁለት ፡ አንሥቶ ፡ ከሁለት ፡ የበለጡ ፡ ሰዎች ፡ እያንዳንዳቸው ፡ አንዳንድ ፡ ነገር፡ እንዳላቸው ፡ ወይም ፡ እያንዳንዳቸው ፡ አንዳንድ ፡ ሥራ ፡ እንደሚሠሩ ፡ የሚያሳይ ፡ (የሚያመለክት) ፡ ቅጽል ፡ ነው ። አንዳንድ ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ እንደሚመላለስ ፡ በትክክል ፡ ያመለክታል ። ካደላዳይ ፡ ቅጽሎች ፡ ለምሳሌ ፡ የሚሆኑ ፡ አንዳንድ ፡ ሌላ ፡ ሁለቱም ፡ አንድ ፡ እያንዳንዳቸው ፡ ናቸው ።

አስረጅ ፡-

1 ፱ ፡ ልጆች ፡ እያንዳንዳቸው ፡ አምስት ፡ አምስት ፡ መጻሕፍትን ፡ ገዙ ።

2 የያንዳንዱን ፡ ልጅ ፡ ስም ፡ በክርታሱ ፡ (በወረቀቱ) ፡ ላይ ፡ ጻፍ ።

3 ለሁለቱም ፡ ልጆች ፡ ሦስት ፡ ሦስት ፡ ብር ፡ ስጣቸው ።

4 የያንዳንዱ ፡ ልጅ ፡ አባት ፡ አንዳንድ ፡ ብር ፡ ለመክፈል ፡ ይችላል ።

5 ጢት ፡ ጢት ፡ ባሥራ ፡ ሁለት ፡ ባሥራ ፡ ሁለት ፡ ሰዓት ፡ ሰንደቅ ፡ ዓላማ ፡ ይሰቀላል ።

6 ወባዋ ፡ (እያሠለሰች) ፡ በሦስት ፡ በሦስት ፡ ቀን ፡ ትነሣበታለች ።

7 አንዳንዱን ፡ መደብ ፡ በሦስት ፡ በሦስት ፡ ብር ፡ ሸጠው ።

የማናቸውንም ፡ አገባብና ፡ ሥራ ፡ እየለየን ፡ አጥንተን ፡ በያይነቱ ፡ መከፋፈል፡ አለብን ፤ ስለዚህ ፡ አደላዳይ ፡ ቅጽል ፡ ከሌሎቹ ፡ ሁሉ ፡ ተለይቶ ፡ የግል ፡ ሥራ ፡ ስላለው፡ ከነዚያ ፡ ጋራ ፡ ተደርቦ ፡ በደባልነት ፡ ሊጠራ ፡ አይገባውም ።

(ረ) መጠይቅ ፡ ቅጽል፡- መጠይቅ ፡ ቅጽል ፡ ጥያቄን ፡ ለማቅረቢያ ፡ የሚጠቅም፡ ነው ።

ምሳሌ ፡- ምን ? የትኛው ? 1 ምን ፡ ደብዳቤ ፡ ትጽፋለህ ?

2 የትኛውን ፡ ደብዳቤ ፡ ትፈልጋለህ ?

## ፱ ፡ የቅጽል ፡ አገባብ ።

ቅጽል ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ሲገባ ፡ ሁለት ፡ ስልቶች ፡ አሉት ።

፩ ፡ ስምን ፡ ተከትሎ ፡ የሚገልጸው ፡ «ተከታይ» ፡ ቅጽል ፡ ነው ።

(ሀ) ዐመለኛ ፡ ፈረስ ፡ ባለቤቱን ፡ ያከስራል ። (ለ) እልከኛ ፡ ልጅ ፡ ወላጆቹን ፡ ያሰለቻል ።

በስም ፡ ፈንታ ፡ ገብቶ ፡ የቅጽልንና ፡ የስምን ፡ ሥራ ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ አስተባብሮ ፡ የሚሠራ ፡ ነው ። ከመሆን ፡ ግስ ፡ ጋራ ፡ ሲገባ ፡ ግን ፡ መሙሊያ ፡ ተብሎ ፡ ይጠራል ። ምክንያቱም ፡ የመሆን ፡ ግስ ፡ ረዳት ፡ ሆኖ ፡ ስሜቱን ፡ ፍጹም ፡ (ሙሉ)፡እንዲያደርግለት፡ ስለሚፈልግ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡- 1 ሰውዬው ፡ ድዳ ፡ ነው ።

2 ልጁ ፡ ንቁ ፡ ነው ።

## ፫ ፡ በቅጽል ፡ ፈንታ ፡ የሚያገለግሉ ፡ ነገሮች ።

(ሀ) ግሳዊ ፡ ቅጽል ፡- ግስን ፡ አርብቶ ፡ የሚገኝ ፡ ቅጽል ፡ ነው ።

| | | |
|---|---|---|
| አታለለ ፡ | ዐወቀ ፡ | አፈቀረ ፡ |
| ያታልላል ፡ | ያውቃል ፡ | ያፈቅራል ፡ |
| ያታልል ፡ ዘንድ | ያውቅ ፡ ዘንድ ፡ | ያፈቅር ፡ ዘንድ ፡ |
| ያታል ፡ | ይወቅ ፡ | ያፍቅር ፡ |
| ማታለል ፡ | ማወቅ ፡ | ማፍቀር ፡ |
| አታላይ ፡ | ዐዋቂ ፡ | አፍቃሪ ፡ |

አታላይ ፡ ዐዋቂ ፡ አፍቃሪ ፡ ከግስ ፡ የተገኙ ፡ ቅጽሎች ፡ ናቸው ።

በዚሁ ፡ ዐይነት ፡ ግስ ፡ ሲረባ ፡ ቅጽል ፡ ይገኛል ። ሦስቱ ፡ ከግስ ፡ የተገኙ ፡ ቅጽሎች ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ ግሳውያን ፡ ቅጽሎች ፡ ይባላሉ ።

(ለ) አርእስታዊ ፡ ቅጽል ፡- ከርእስት ፡ የሚመሠረት ፡ ቅጽል ፡ ነው ።

ምሳሌ ፡-

| | |
|---|---|
| ማታለል ፡ | ማታለያ ፡ |
| ማወቅ ፡ | ማወቂያ ፡ |
| መጻፍ ፡ | መጻፊያ ፡ |
| መስማት ፡ | መስሚያ ፡ |

(ሐ) መስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ እንደ ፡ ቅጽል ፡- መስተዋድድ ፡ በስም ፡ ወይም ፡ በተውላጠ ፡ ስም ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ ያንን ፡ የወደቀበትን ፡ ቃል ፡ ከዋናው ፡ ስም ፡ ጋራ ፡ አገናኝቶ ፡ ባለገንዘብነትን ፡ ወይም ፡ ዘርፍ ፡ አስተኔነትን ፡ እንዲያመለክት ፡ ያደረገ ፡ እንደ፡ሆነ፤ መስተዋድድ ፡ የወደቀበት ፡ ቃል ፡ ዘርፍ ፡ ወይም ፡ ዘርፍ ፡ አስተኔ ፡ ቅጽል ፡ ይሆናል ፤ ቢሆንም ፡ ቃሉ ፡ በመስተዋድድ ፡ ተገዝቷልና ፡ ንኡስ ፡ ሐረጉ ፡ ቅጽላዊ ፡ ተብሎ ፡ መጠራት ፡ ይገባዋል ። መስተዋድዱ ፡ ዘርፍ ፡ አያያዥ ፡ ሆኖ ፡ ይቀራል ፡ ከማለት ፡ መስተዋድድ ፡ መስተዋድዱ ፡ የወደቀበትን ፡ ስም ፡ ይገዛል ፡ ማለት ፡ በጣም ፡ የተሻለ ፡ ነው ።

ምሳሌ ፡-

የሰው ፡

የዕንጨት ፡

የጠፍር ፡

(መ) ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡- ጥገኛ ፡ መስተፃምር ፡ ባንቀጽ ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ካደረገው ፡ በኋላ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረጉ ፡ አንድ ፡ ስም ፡ ወይም ፡ ተውላጠ ፡ ስም፡ ለመግለጽ ፡ የቻለ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እርሱ ፡ ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ይባላል ።

ምሳሌ ፡ ወደ ፡ ሐረር ፡ ለመሄድ ፡ የተሳፈርንበት ፡ መኪና ፡ ተሰበረ ።

(ሠ) አገናዛቢ፡ዐጸፋ፡(ቅጽል)፡-አገናዛቢ፡ቅጽል፡ ባለገንዘብን፡ የሚያመለክት፡ ቅጽል፡ነው።

አገናዛቢ፡ ቅጽል፡ የሚባለውም፡ በስም፡ መድረሻ፡ ላይ፡ የሚገባው፡ ዝርዝር፡ነው።

ምሳሌ ፦

| | | | |
|---|---|---|---|
| ዬ ፡ | ደብተርዬ ፡ | የኔ ፡ ደብተር ፡ | «ዬ» ኃምስ ፡ ያደርጋል ። |
| ህ ፡ | ደብተርህ ፡ | ያንተ ፡ | ደብተር ፡ |
| ሽ ፡ | ደብተርሽ ፡ | ያንቺ ፡ | ደብተር ፡ |
| ዎ ፡ | ደብተርዎ ፡ | የእርስዎ ፡ | ደብተር ፡ |
| ካዕብ | ደብተሩ ፡ | የእርሱ ፡ | ደብተር ፡ |
| ዋ ፡ | ደብተርዋ ፡ | የእርስዋ ፡ | ደብተር ፡ |
| አችን ፡ | ደብተራችን ፡ | የኛ ፡ | ደብተር ፡ |
| አችሁ ፡ | ደብተራችው ፡ | የናንተ ፡ | ደብተር ፡ |
| አቸው ፡ | ደብተራቸው ፡ | የነርሱ ፡ | ደብተር ፡ |

## ፬ ፡ ቅጽል ፡ እንደ ፡ ስም ፡ ሲሠራ ።

ቅጽል ፡ ስለ ፡ ስም ፡ ሆኖ ፡ ለተነገረው ፡ አንቀጽ ፡ ባለቤት ፡ ወይም ፡ ተሳቢ ፡ ስለ ሚሆን ፡ በቂ ፡ ይባላል ፤ በቂ ፡ መባሉም ፡ የቅጽልነት ፡ ባሕርዩን ፡ ይዞ ፡ የስምን ፡ ሥራ ፡ ስለሚያከናውን ፡ ነው ።

አስረጅ ፦ 1 ዐመለኛ ፡ ዐመለኛው ፡ እየበጠበጠ ፡ አስቸግሯል ።

2 ብልኅ ፡ በስሕተቱ ፡ ይማራል ።

3 ዐመለኛ ፡ ዐመለኛውን ፡ እየመነጠቁ ፡ ማስወጣት ፡ ነው ። } በተሳ

4 ሰነፍን ፡ በምክር ፡ አበረታታው ፡ እንጂ ፤ ተስፋ ፡ አታስቈርጠው ። } ቢነት

## ፭ ፡ የቅጽል ፡ አበዛዝ ፡

ከአኃዝ ፡ ቅጽል ፡ በስተቀር ፡ አንዳንዶቹ ፡ ቅጽሎች በአእምሮ ፡ ውስጥ ፡ ያልተለ ዩትን ፡ ስሞች ፡ ተከትለው ፡ ሲገቡ ፡ እንደ ፡ ስም ፡ ሊበዙ ፡ አያስፈልጋቸውም ። ነገር ፡ ግን ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ቅጽሎች ፡ ለብቻቸው ፡ በበቂነት ፡ ስለሚገቡ ፡ መብዛት ፡ ይገባ ቸዋል ። በአእምሮም ፡ ውስጥ ፡ ተለይተው ፡ የሚታወቁት ፡ ስሞች ፡ በቅጽሎች ፡ የሚገ ለጹ ፡ እንደሆን ፡ ቅጽሎቹ ፡ በዝተው ፡ በመድረሻቸው ፡ ላይ ፡ የተወሰነ ፡ አመልካች ፡ ቅጽል ፡ ይጨመርባቸዋል ።

አስረጅ ፦ 1 መጥፎች ፡ ልጆች ፡ የወለደ ፡ ሰው ፡ ዘወትር ፡ እንደ ፡ ተናደደ ፡ ይኖራል ።

2 ደጋግ ፡ ልጆች ፡ ራሳቸው ፡ ከመመስገናቸው ፡ በላይ ፡ ወላጆቻቸውን ፡ ሲያስ መሰግኑ ፡ ይኖራሉ ።

3 ነጫጮቹን ፡ ፍየሎች ፡ እየመረጥህ ፡ አምጣቸው ።

4 ደጎች ፡ (ደጋጎቹ) ፡ ባመላቸው ፡ ብቻ ፡ ይመረጣሉ ።

5 ከፍየሎችህ ፡ ውስጥ ፡ ጥቋቊሮቹን ፡ እየመረጥህ ፡ ሽጣቸው ።

## ፯ ፡ አወዳዳሪ ፡ ቅጽል ፡

አወዳዳሪ ፡ ቅጽል ፡ አንዱን ፡ ነገር ፡ አብልጦ ፡ ወይም ፡ አሳንሶ ፡ የሚያሳይ ፡ ቅጽል ፡ ነው ፤ የማወዳደሩ ፡ ደረጃ ፡ በደረጃ ፡ ከፍና ፡ ዝቅ ፡ ይላል ፤ ማወዳደርን ፡ የሚያ መለክቱ ፡ ቅጽሎች ፡ ረዳት ፡ ቃላትን ፡ ይፈልጋሉ ።

ምሳሌ ፡ ተነጻጻሪ ፡ ቸር ፡ አበላላጭ ፡ { እጅግ ፡ በጣም ፡ ቸር ፡ / የቸር ፡ መጨረሻ ፡ }
አብላጭ ፡ በጣም ፡ ቸር ፡

## የቅጽል ፡ ዝርዝር ፡ አፈታት ።

ቅጽልን ፡ መዘርዘር ፡ በሚከተሉት ፡ ዐቅዶች ፡ ነው ።

1 ዐይነቱን ፡ መለየት ፡
2 ደረጃውን ፡ መለየት ፡
3 አገባቡን ፡ መለየት ፡

**አስረጅ** ፡- 1 ኀጢአተኛ ፡ ሰው ፡ ሳያሳድዱት ፡ ይሸሻል ።

**ኀጢአተኛ** ፡ የግብር ፡ ቅጽል ፡ ተከታይ ፡ ተነጻጻሪ ፡ ሰውን ፡ ይገልጻል ።

2 ፈለቀ ፡ በጣም ፡ ቀይ ፡ ልጅ ፡ ነው ።

**ቀይ** ፡ የዐይነት ፡ ቅጽል ፡ ተከታይ ፡ ተነጻጻሪ ፡ ልጅን ፡ ይገልጻል ።

3 ዶክቶር ፡ ዊልሰን ፡ አሜሪካዊ ፡ ናቸው ።

አሜሪካዊ ፡ የወገን ፡ ቅጽል ፡ መሙሊያ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ተመልሶ ፡ ዶክቶር ፡ ዊልሰንን ፡ ይገልጻል ።

## ፫ኛ ፡ መልመጃ ፡

1 የሚከተሉትን ፡ ግለጻቸው ።
  (ሀ) በቂ ፡ ቅጽል ፡
  (ለ) ተከታይ ፡ ቅጽል ፡
  (ሐ) የዐይነት ፡ ቅጽል ፡

2 በሚከተሉት ፡ ቃላት ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ ልዩነት ፡ ጻፍ ።
  (ሀ) በተወሰነ ፡ አመልካችና ፡ ባልተወሰነ ፡ አመልካች ፡ መካከል ፡
  (ለ) በግብር ፡ ቅጽልና ፡ በወገን ፡ ቅጽል ፡

3 ከግብር ፡ ቅጽል ፡ ለምሳሌ ፡ የሚሆኑ ፡ ፭ ፡ ቃላትን ፡ ጻፍና ፡ ተከታይ ፡ ቅጽል፡ እያደረግህ ፡ በያንዳንዳቸው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራ ።

4 (ሀ) ካመልካች ፡ ቅጽል ፡ ስድስት ፡ ቃላትን ፡ ጻፍ ።
  (ለ) ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ የምታስገባቸውን፡ ቅጽሎች፡ በቂ ፡ እያደረግህ ፡ ሁለት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮችን ፡ ሥራ ።
  (ሐ) የሚከተሉትን ፡ ቃላት ፡ ተከታይ ፡ ቅጽል ፡ እያደረግህ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራባቸው ።

ተልካሳ ፡ ዐመለ ፡ ቢስ ፡ ደፋር ፡ ንቁ ፡ አመስጋኝ ፡ ቸር ፡ ቀብራራ ፡ ለዋሳ ።

5 ምንባብ ፡- የቤቱ ፡ ዐቅድ ፡ እንደሚከተለው ፡ ነበር ፤ ቤቱ ፡ ሰቀልኛ ፡ ሆኖ፡ ከመካከል ፡ አንድ ፡ ሰፊ ፡ ክፍል ፡ አለው ። ከግራና ፡ ከቀኙ ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ አነስ ተኛ ፡ ክፍሎች ፡ አሉት ፤ የመካከሉ ፡ ክፍል ፡ የእንግዳ ፡ መቀበያ ፡ ነው ። በስተግራ ፡ በፀሐይ ፡ መውጫ ፡ በኩል ፡ የመኝታ ፡ ቤት ፡ ነው ፤ በስተቀኝ ፡ የጽሕፈት ፡ ቤትና ፡ የመብል ፡ ቤቶች ፡ ናቸው ። አራቱም ፡ ክፍሎች ፡ በቤቱ ፡ መጠን ፡ መስኮቶችና፡ በሮች፡ ተበጅተውላቸዋል ፤ ዋናው ፡ ደጃፍ ፡ ወደ ፡ ውስጥ ፡ ገባ ፡ ብሎ ፡ ክፍት ፡ በረንዳና ፡ ሰፊ ፡ ታዛ ፡ ያለው ፡ ሆኖ ፡ ከዠርባው ፡ ግን ፡ ክብ ፡ የሆነች ፡ የመስተዋት ፡ ቤት ፡ ከእን ግዳ ፡ ቤቱ ፡ የተያያዘች ፡ ጓዳ ፡ ነበረች ። ወለሉ ፡ በጥድ ፡ ሣንቃ ፡ ከተመታ ፡ በኋላ ፡ ጣራውን ፡ የጽሕፈት ፡ ቤቱንና ፡ የመኝታ ፡ ቤቱን ፡ ባቡጀዲድ ፡ ጨርቅ ፡ አስመታ ቸው ፤ የእንግዳ ፡ መቀበያውን ፡ ግን ፡ እንዲሁ ፡ እንዳለ ፡ እንዲሆን ፡ ፈቀደ ። እውነ ትም ፡ የጣራው ፡ ዕንጨቶች ፡ የተመረጡ ፡ ቀጥ ፡ ያሉ ፡ የጥድና ፡ የሰገድ ፡ ጠርቦች ፡ ከመሆናቸው ፡ ጋራ ፡ አልፎ ፡ አልፎ ፡ መቃና ፡ ቀርቀሃ ፡ ጣልቃ ፡ ተሳግቶባቸው ፡ ማገ ሮቹ ፡ በቀጭኑ ፡ በቃጫ ፡ ገመድ ፡ ተማግረው ፡ ሲታዩ ፡ ጣራው ፡ ላይን ፡ ደስ ፡ የሚል ፡ ውበት ፡ ነበረው ።

ግርማቸው ፡ ተክለ ፡ ሐዋርያት ፡

(ሀ) የሚከተሉትን ፡ ቅጽሎች ፡ በያይነታቸው ፡ ለያቸው ።

ሁለት ፡ ሁለት ፡ አነስተኛ ፡ አራቱም ፡ ዋናው ፡ ክፍት ፡ ሰፊ ፡ ክብ ፡

(ለ) ከሚከተሉት ፡ ውስጥ ፡ መስተዋድዳን ፡ ንኡስ ፡ ሐረጎችን ፡ እየለየህ ፡ አመልክት ።

| | | |
|---|---|---|
| የመካከሉ ፡ ክፍል ፡ | የመኝታ ፡ ቤት ፡ | ከእንግዳ ፡ ቤቱ፡ |
| የእንግዳ ፡ መቀበያ ፡ | የጽሕፈት ፡ ቤት ፡ | በጥድ ፡ ሣንቃ ፡ |
| በፀሐይ፡መውጫ፡በኩል፡ | የመብል ፡ ቤት ፡ | በአቡጀዲድ፡ ጨርቅ ፡ |
| የጣራ ፡ ዕንጨቶች ፡ | የጥድ ፡ ጠርቦች ፡ | የሰገድ ፡ ጠርቦች ፡ |

(ሐ) ከዚህ ፡ በላይ ፡ በተጻፈው ፡ ምንባብ ፡ ውስጥ ፡ በቂ ፡ ሆነው ፡ በስም ፡ ፈንታ ፡ የገቡትን ፡ እየለየህ ፡ ጻፍና ፡ ከምን ፡ እንደ ፡ ተመሠረቱ ፡ አስረዳ ።

(መ) ከተሰጠው ፡ ምንባብ ፡ ውስጥ ፡ ቅጽላውያን ፡ ጥገኛ ፡ ሐረጎችን ፡ ጻፍና ፡ የሚገልጿቸውን ፡ ቃላት ፡ አመልክት ።

(ሠ) ከምንባቡ ፡ ውስጥ ፡ ስሞችን ፡ በሙሉ ፡ ጻፍና፡ በየስም ፡ ዐይነታቸው ፡ አመልክት ።

6 የሚከተሉትን ፡ ቃላት ፡ የወገን ፡ ቅጽል ፡ አድርገህ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራባ ቸው ። ሱዳን ፡ ኬንያ ፡ ሕንድ ፡ አልጄርያ ፡ ፈረንሳይ ፡ ሆላንድ ፡ ቻይና ፡ አፍሪቃ ፡ አውሮጳ ፡

## ፬ኛ ፡ ተጨማሪ ፡ መልመጃ ።

1 መጠይቅ ፡ ቅጽል ፡ ከሚሆኑ ፡ ቃላት ፡ አራት ፡ ጻፍ ።

2 ባደላዳይ ፡ ቅጽሎች ፡ አምስት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ጻፍ ።

3 አገናዛቢ ፡ ቅጽል ፡ የሚያደርጉትን ፡ ባዕድ ፡ መድረሻዎች ፡ ጻፍና ፡ እንዴት ፡ ቅጽል ፡ እንደሚሆኑ ፡ አስረዳ ።

4 የሚከተሉትን ፡ ግሶች ፡ አርብተህ ፡ ከነርሱ ፡ ውስጥ ፡ ቅጽል ፡ የሚሆኑትን ፡ ሁሉ ፡ ጻፍ ። ቀየሰ ፡ አረመ ፡ ነሰነሰ ፡ ማረከ ፡

5 ከግስ ፡ ውስጥ ፡ ከሚገኙት ፡ ቅጽሎች ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ስም ፡ ሆነው ፡ የሚያገለግሉ ፡ የትኞቹ ፡ ናቸው ?

6 <u>ምንባብ ፡</u>

ዕንቍላል ፡ መቼም ፡ ዕንቍላል ፡ ነው ። ዳሩ ፡ ግን ፡ የተበላሸ ፡ ዕንቍላል ፡ አለ ። ዕንቍላል ፡ ቢቈይ ፡ በገዛ ፡ እግሩ ፡ ይሄዳል ፡ ይባላል ። ወድቆ ፡ የሚጨፈለቅ ፡ ዕንቍላል፡ ጥፉ ፡ ነው ። የልጅ ፡ ነገር ፡ ሁለት ፡ ፍሬ ፤ አንዱ ፡ ብስል ፡ አንዱ ፡ ጥሬ። ተስፋ ፡ መቼም ፡ ተስፋ ፡ ነው ። ከንቱ ፡ ተስፋ ፡ ግን ፡ ምናምን ፡ ባዶ ፡ ከንቱና ፡ ሸንጋይ ፡ አለኝታ ፡ ነው። ልጆች፡ የወፍን ፡ ዕንቍላል ፡ በክር ፡ እንደሚሰኩ ፤ እንዲሁ ፡ እኔም ፡ ልዩ፡ ልዩ ፡ የሆነውን ፡ ተስፋ ፡ ሰብስቤ ፡ አሳያችኋለሁ ። መልካም ፡ ከፉና ፡ ከንቱ ፡ ሞኝም ፡ አለኝታ ፡ አለ ። ነገር ፡ ግን ፡ የሚያጠግብ ፡ እንጀራ ፡ ከምጣዱ ፡ ያስታውቃል ። ከፎከረ፡ የጠጠረረ ፡ ይሻላል ። ሳል ፡ ያለበት ፡ ጉልማሳ ፡ ዘንጋዳ ፡ ያለበት ፡ ዳጉሳ ፡ ብዙ ፡ ተስፋ፡ የለውም ። ልጅ ፡ ያቦካው ፡ ለራት ፡ አይበቃ ።

አሊ ፡ ሪክሶን ።

(ሀ) ከምንባቡ ፡ ውስጥ ፡ ቅጽሎችንና ፡ እንደ ፡ ቅጽሎች ፡ የሚሠሩትን ፡ ቃላት ፡ እየለቀምህ ፡ ጻፋቸው ።

(ለ) ቅጽላውያን ፡ ጥገኛ ፡ ሐረጎችን ፡ ሕገኛ ፡ ቅጽሎች ፡ አድርጋቸው ።

(ሐ) ቅጽላውያን ፡ ንኡስ ፡ ሐረጎችን ፡ እየለየህ ፡ ጻፍ ።

(መ) የወል ፡ ስሞችን ፡ እየለየህ ፡ ጻፍ ።

(ሠ) ዕንቍላል ፡ ቢቈይ ፡ በእግሩ ፡ ይሄዳል ፡ የሚባለውን ፡ ተረት ፡ አስፋፍተህ ፡ ጻፍ ።

(ረ) ከፎከረ ፡ የጠረጠረ ፡ ይሻላል ፡ የሚለውን ፡ አርእስት ፡ አድርገህ ፡ ድርሰት ፡ ጻፍ ።

## <u>ምዕራፍ ፡ ፫ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡</u>

ተውላጠ ፡ ስም ፡ ማለት ፡ የስም ፡ ምትክ ፡ ወይም ፡ የስም ፡ ለዋጭ ፡ ማለት ፡ ነው ። ማንኛውም ፡ ነገር ፡ በስም ፡ ፈንታ ፡ ተተክቶ ፡ የሚያገለግል ፡ ከሆነ ፡ የስም ፡ ምትክ ፡ ይባላል ።

ተውላጠ ፡ ስም ፡ ባራት ፡ ታላላቅ ፡ ክፍሎች ፡ ይከፈላል ።

(ሀ) ምድብ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡
(ለ) ዐጸፋ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡
(ሐ) አመልካች ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡
(መ) መጠይቅ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡

## ፩ ፡ ምድብ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡

(ሀ) <u>ሰብአዊ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡</u>— በሦስት ፡ ላይ ፡ ተመድበው ፡ የሚነገሩትን፡ ተውላጠ፡ ስሞች ፡ የሚይዝ ፡ ነው ። ድርብና ፡ መዘከር ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ በዚሁ ፡ ክፍል ፡ ተጠቅልለው ፡ ይነገራሉ ።

| <u>ምሳሌ ፡</u> | <u>ነጠላ ፡</u> | <u>ብዙ ፡</u> | <u>ነጠላ ፡</u> | <u>ብዙ ፡</u> | <u>ነጠላ ፡</u> | <u>ብዙ ፡</u> |
|---|---|---|---|---|---|---|
| ፩ኛ፡ መደብ፡ | እኔ፡ | እኛ፡ | ፪ኛ፡ መደብ፡ አንተ፡<br>አንቺ ፡<br>እርስዎ ፡ | እናንተ ፡ | ፫ኛ ፡ መደብ ፡ እርሱ ፡<br>እርስዋ ፡ | እነርሱ ፡ |

(ለ) <u>ድርብ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡</u>-ድርብ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ የሚባለው ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ተደግሞ ፡ ሲነገር ፡ ነው ።

| <u>ምሳሌ ፡-</u> | ፩ኛ ፡ መደብ ፡ | ፪ኛ ፡ መደብ ፡ | ፫ኛ ፡ መደብ ፡ |
|---|---|---|---|
| ነጠላ ፡ | እኔ ፡ ራሴ ፡ | አንተ ፡ ራስህ ፡<br>አንቺ ፡ ራስሽ ፡ | እርሱ ፡ ራሱ ፡<br>እርሷ ፡ ራሷ ፡ |
| ብዙ ፡ | እኛ ፡ ራሳችን ፡ | እናንተ ፡ ራሳችሁ ፡ | እነርሱ ፡ ራሳቸው ፡ |

(ሐ) <u>ድርብርብ፡ተውላጠ፡ስም፡</u>- ድርብርብ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ የሚባለው፡ የተደገመው ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ተደግሞ ፡ ሲነገር ፡ ነው። አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ዕጽፍ ፡ ድርብ ፡ ተውላጠ፡ ስም ፡ ይባላል ።

<u>ምሳሌ ፡-</u> ፩ኛ ፡ መደብ ፡ ፪ኛ ፡ መደብ ፡

| <u>ነጠላ ፡</u> | <u>ብዙ ፡</u> | <u>ነጠላ ፡</u> | <u>ብዙ ፡</u> |
|---|---|---|---|
| እኔ፡ ራሴ፡ በገዛ፡ እጄ፡ | እኛ ፡ ራሳችን ፡<br>በገዛ ፡ እጃችን ፡ | አንተ ፡ ራስህ ፡ በገዛ ፡ እጅህ፡<br>አንቺ፡ ራስሽ፡ በገዛ፡ እጅሽ ፡ | እናንተ፡ ራሳችሁ፡<br>በገዛ ፡ እጃችሁ ፡ |

፫ኛ ፡ መደብ ፡

| <u>ነጠላ ፡</u> | <u>ብዙ ፡</u> |
|---|---|
| እርሱ ፡ ራሱ ፡ በገዛ ፡ እጁ፡<br>እርሷ፡ ራሷ ፡ በገዛ፡ እጅዋ ፡ | እነርሱ ፡ ራሳቸው ፡ በገዛ ፡ እጃቸው ፡ |

(መ) <u>መዘክር ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡</u>- ልንጠራው ፡ የምንፈልገውን ፡ ስም ፡ ለጊዜው ፡ ያላስታወስነው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፤ ስሙን ፡ ለማሰላሰል ፡ እንዲመቸን ፡ ስንል ፡ (በማለት)፡ የምጨምረው ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ነው ።

<u>ምሳሌ ፡-</u> ፪ኛ ፡ መደብ ፡ ለሰው ፡ ፫ኛ ፡ መደብ ፡ ለሰው ፡

| ነጠላ ፡ | ብዙ ፡ | ነጠላ ፡ | ብዙ ፡ |
|---|---|---|---|
| እንተን ፡ | እነእንተን ፡ | እገሌ ፡<br>እገሊት ፡ | እነእገሌ ፡<br>እነእገሊት ፡ |
| ፫ኛ ፡ መደብ ፡ | ለነገር ፡<br>ለቦታ ፡ | እንትን ፡<br>እንትና ፡ | እንትኖች ፡ |

## ፪ ፡ ዐጸፋ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡

ዐጸፋ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡- ዐጸፋ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ የሚባለው፡ በግሱ ፡ መድረሻ፡ ላይ ፡ ገብቶ ፡ አስቀድሞ ፡ ለተነገረው ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ወይም ፡ ስም ፡ ድጋሚ ፡ የሚ ሆን ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ነው ። ድጋሚነቱም ፡ ለምድብ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ነው ። ዐጸፋ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ በ፪ ፡ ንኡሳን ፡ ክፍሎች ፡ ይከፈላል ።

(ሀ) የተሳቢ ፡ ዐጸፋ፡- ለገቢሩ ፡ ግስ ፡ ተሳቢ ፡ የሚሆነውን ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ የሚያመ ለክት ፡ ዐጸፋዊ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ነው ።

| | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|
| ነጠላ ፡ | ኝ | ህ | ሽ | አት | ው |
| ብዙ ፡ | ን | አችሁ | | አቸው | |

እነዚህ ፡ ዐጸፋውያን ፡ ተውላጣተ ፡ ስም ፡ በገቢር ፡ ግስ ፡ ተውላጣት ፡ ስምን ፡ ሲያመ ለክቱ ፡

| | | |
|---|---|---|
| ፩ኛ ፡ መደብ ፡ | አደለኝ ፡ | አደለን ፡ |
| ፪ኛ ፡ መደብ ፡ | አደለህ ፡ አደለሽ ፡ | አደላችሁ ፡ |
| ፫ኛ ፡ መደብ ፡ | አደለው ፡ አደላት ፡ | አደላቸው ፡ |

| | ነጠላ ፡ | ብዙ ፡ |
|---|---|---|
| ፩ኛ ፡ መደብ ፡ | መከረኝ ፡=እኔን ፡ መከረ ፡ | መከረን ፡ =እኛን ፡ መከረ ፡ |
| ፪ኛ ፡ መደብ ፡ | መከረህ ፡=አንተን ፡ መከረ ፡<br>መከረሽ ፡=አንቺን ፡ መከረ፡ | መከራችሁ፡=እናንተን ፡ መከረ ፡ |
| ፫ኛ ፡ መደብ ፡ | መከረው፡=እርሱን ፡ መከረ፡<br>መከራት ፡=እርሷን ፡ መከረ፡ | መከራቸው፡=እነርሱን ፡ መከረ ፡ |

(ለ) የባለቤት ፡ ዝርዝር ፡- በግሱ ፡ መድረሻ ፡ ላይ ፡ ገብቶ፡ ባለቤትን ፡ የሚያመለክት ፡ የባለቤት ፡ ዝርዝር ፡ ይባላል ።

የባለቤት ፡ ዝርዝሮች ፡ በገቢር ፡ ግስ ፡ ባለቤቶቹን ፡ ሲያመለክቱ ።

| | ነጠላ ፡ | | ብዙ ፡ | |
|---|---|---|---|---|
| ፩ኛ ፡ መደብ ፡ | ጻፍሁ ፡ | ሁ፡ | ጻፍን ፡ | ን |
| ፪ኛ ፡ መደብ ፡ | ጻፍህ ፡ | ህ | ጻፉችሁ ፡ | አችሁ ፡ |
| | ጻፍሽ ፡ | ሽ | | |

፫ኛ ፡ መደብ ፡ ጸሬች ፡ (አ) ት ግዕዝ ፡ ወይም ፡ ራብዕ ፡ ጸፊ ፡ } ጸፉ ፡ ካዕብ ፡

ምሳሌ ፡- ፩ኛ ፡ መደብ ፡ ነጠላ ፡ ብዙ ፡

መከርሁ ፡ እኔ ፡ መከርሁ ፡ መከርን ፡- እኛ ፡ መከርን ፡

፪ኛ ፡ መደብ ፤ ነጠላ ፡ ብዙ ፡

መከርህ ፡=አንተ ፡ መከርህ ፡ መከራችሁ ፡=እናንተ ፡ መከራችሁ ፡

መከርሽ ፡=አንቺ ፡ መከርሽ ፡ » » »

መከሩ ፡=እርስዎ ፡ መከሩ ፡ » » »

፫ኛ ፡ መደብ ፤ መከረ ፡=እርሱ ፡ መከረ ፡ መከሩ ፡=እነርሱ ፡ መከሩ ፡

መከረች ፡=እርሷ ፡ መከረች ፡ » » »

(ሐ) አገናዛቢ ፡ ዐጸፋ ፡- ከዚህ ፡ በፊት ፡ በቅጽል ፡ ውስጥ ፡ ስለ ፡ ተነገረ ፡ አሁን ፡ ደግሞ ፡ በዚህ ፡ ውስጥ ፡ አንጽፈውምና ፡ በተነገረበት ፡ ስፍራ ፡ ደኅና ፡ አድርጎ ፡ መመልከት ፡ ነው ።

## ፫ኛ ፡ አመልካች ፡ ተውላጠ ፡ ስም ።

አመልካች ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ በሁለት ፡ ይከፈላል ።

(ሀ) የተወሰነ ፡ አመልካች ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡-አንድ ፡ ስም ፡ አስቀድሞ ፡ ከተነገረ ፡ በኋላ ፡ እንዳይደገም ፡ ስንፈልግ ፡ የምንጨምረው ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ የተነገረው ፡ ስም ፡ በቅርብና ፡ በሩቅ ፡ መሆኑን ፡ ያመለክታል ።

ምሳሌ ፡

| የቅርብ ፡ | | የሩቅ ፡ | |
|---|---|---|---|
| ይህ ፡ | እነዚህ ፡ | ያ ፡ | እነዚያ ፡ |
| ይህች ፡ | እኒህ ፡ | ያች ፡ | እኒያ ፡ |
| | እሊህ ፡ | | እሊያ ፡ |

አስረጅ ፡-1 ፡ እኔ ፡ ለመግዛት ፡ የምፈልገው ፡ ይህን ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ገንዘብ ፡ አነሰኝ።

2 እኒህ ፡ እጅ ፡ መንሻን ፡ አመጡለት ፤ እኒያ ፡ ግን ፡ ምስጋናን ፡ አቀረቡለት ።

(ለ) ያልተወሰነ ፡ አመልካች ፡ ተውላጠ፡ ስም ፡=በጠቅላላው ፡ ስንመለከት፡ ያልተወሰነ፡ አመልካች ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ምትክ ፡ የሚሆንላቸው ፡ ስሞች ፡ ባሳብ ፡ ውስጥ፡ የተወሰኑ፡ ሆነው ፡ አይታወቁም ፤ ስለዚህ ፡ አ፡ ተ፡ ስ፡ ባሳብ ፡ ውስጥ ፡ ላልተወሰነ ፡ ስም፡ ምትክ ፡ የሚሆን ፡ ነው ።

ምሳሌ ፡- አንድ ፡ ሌላ ፡ ማናቸውም ፡ አንድም ፡ ማንኛውም ፡

<u>**አስረጅ ፡**</u>

1 ሌላ ፡ ካልፈለግህልኝ ፡ በስተቀር ፡ ይህ ፡ አይሆነኝም ።
2 ማንኛውም ፡ ቢያወራ ፡ አትቀበል ።
3 አንዳንድ ፡ ካልሰጠኸን ፡ ይቅርብን ።
4 አንድም ፡ አላየሁም ።
5 እየመራረጡ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ማንኛውንም ፡ ማግበስበስ ፡ አይገባም ።

<u>**ማስገንዘቢያ ፡**</u>

በተወሰነና ፡ ባልተወሰነ ፡ አመልካች ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ ልዩነት ፡ ለማወቅ ፡ ብንፈልግ ፡ <u>በተወሰነው ፡ አመልካች ፡ ተውላጠ ፡ ስም</u> ፡ ያንን ፡ አምጣ ፡ በተባለ ፡ ጊዜ ፡ የሚያመጣው ፡ ነገር ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አምጪው ፡ ትእዛዙን ፡ ገና ፡ ካዛዡ ፡ አፍ ፡ ሲወጣ ፡ ያውቀዋል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ <u>ባልተወሰነ ፡ አመልካች ፡ ተውላጠ ፡ ስም</u> ፡ ሌላ ፡ አምጣ ፡ በተባለ ፡ ጊዜ ፡ ከፊተኛው ፡ ልዩ ፡ መሆኑ ፡ ቢታወቅ ፡ ስንኳ ፡ በእርግጠኛው ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ለማወቅ ፡ አንችልም ፤ ቢሆንም ፡ አመልካች ፡ ቅጽል ፡ ባልተወሰነ ፡ አመልካች ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ላይ ፡ ሲወድቅ ፡ ያልተወሰነውን ፡ የተወሰነ ፡ አመልካች ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ያደርገውና ፡ ባዛዡና ፡ በታዛዡ ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ግልጽ ፡ ሲሆን ፡ ታዛዡ ፡ የተሰጠውን ፡ ትእዛዝ ፡ በቶሎ ፡ ያከናውናል ።

<u>አመልካች ፡ ተውላጠ</u> ፡- ስም ፡ ስምን ፡ ተከትሎ ፡ የገባ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አመልካች ፡ ቅጽል ፡ ይሆናል ፤ ስምን ፡ ሳይከተል ፡ የገባ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ግን ፡ አመልካች ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ይሆናል ።

እንግዲህ ፡ ልዩነታቸው ፡ ስምን ፡ በመከተልና ፡ ባለመከተል ፡ ነው ።

## <u>፬ ፡ መጠይቅ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡</u>

መጠይቅ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ በስም ፡ ፈንታ ፡ እየገባ ፡ ጥያቄን ፡ ለማቅረቢያ ፡ የሚጠቅም ፡ ነው ። መጠይቃን ፡ የሚከተሉት ፡ ናቸው ።

| ለሰው ፡ | | ለነገር ፡ | |
|---|---|---|---|
| ነጠላ ፡ | ብዙ ፡ | ነጠላ ፡ | ብዙ ፡ |
| ማን ፡ | እነማን ፡ | ምን ፡ | ምኖች ፡ |
| የቱ ፡ | የትኞች ፡ | የቱ ፡ | የትኞች ፡ |

## <u>፭ኛ ፡ መልመጃ ፡</u>

1 ተውላጠ ፡ ስም ፡ ባረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ ምን ፡ ለማድረግ ፡ ይጠቅመናል ?
2 ምድብ ፡ ተውላጣተ ፡ ስሞችን ፡ ጻፋቸው ።
(ሀ) በየመደባቸው ፡ አስገባቸው ።
(ለ) ላክብሮት ፡ የሚሆኑትን ፡ ለብቻቸው ፡ ጻፋቸው ።
(ሐ) ጾታቸውን ፡ አመልክት ።

3 ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ተውላጠ ፡ ስምን ፡ ድርብ ፡ ወይም ፡ ዕጽፍ ፡ ድርብ ፡ እያደረግን ፡ ለምን ፡ እናስገባለን ?

4 በመዘክር ፡ ተውላጠ ፡ ስምና ፡ በድርብ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ መካከል ፡ ምን ፡ ልዩነት ፡ አለ ?

5 (ሀ) ለሰው ፡ በሚገቡት ፡ መጠይቃን ፡ ተውላጣተ ፡ ስም ፡ ሁለት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮችን ፡ ሥራ ።

(ለ) ለነገር ፡ በሚገቡት ፡ መጠይቃን ፡ ተውላጣተ ፡ ስም ፡ ሦስት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮችን ፡ ሥራ ።

## የተውላጣተ ፡ ስም ፡ ዝርዝር ፡ አፈታት ፡

ተውላጠ ፡ ስምን ፡ ስንዘረዝር ፡ የሚከተሉትን ፡ ማሰብ ፡ አለብን ።

ዐይነቱን ፡ ጾታውን ፡ ሙያውን ፡
መደቡን ፡ ቊጥሩን ፡

ምሳሌ ፡-

1 እርሱም ፡ ወደ ፡ እንትና ፡ ይሄዳል ።

እርሱ ፡ ምድብ ፡ ተ ፡ ስ ፡ ወንዴ ፡ ጾታ ፡ ፫ኛ ፡ መደብ ፡ ነጠላ ፡ ሙያው ፡ ባለቤት ፡ ባለቤትነቱም ፡ ለማሰሪያ ፡ አንቀጹ ፡ ይሄዳል ፡ ነው ።

እንትና ፡ በምድብ ፡ ክፍል ፡ መዘክር ፡ ተ ፡ ስ ፡ ግዑዝ ፡ ጾታ ፡ ፫ኛ ፡ መደብ፡ ነጠላ፡ ሙያው ፡ የመስተዋድድ ፡ ተገዥ ፡ ተገዥነቱም ፡ ለመገሥገሻው ፡ መስተዋድድ፡ ለወደ ፡ ነው ። ወደ ፡ እንትና ፡ ባንድነት ፡ የቦታ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ተውሳከ ፡ ግስነቱም ፡ ለማሰሪያ ፡ አንቀጹ ፡ ለይሄዳል ፡ ነው ።

2 እኛን ፡ አስተምረን ።

ባለቤቱ ፡ በውስጠ ፡ ታዋቂነት ፡ ቀርቶ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ አንተ ፡ ነው ።
አንተ ፡—ምድብ ፡ ተ ፡ ስ ፡ ፪ኛ ፡ መደብ ፡ ወንዴ ፡ ጾታ ፡ ሙያው ፡ ባለቤት ፡ ባለቤትነቱም፡ ለማሰሪያ ፡ አንቀጹ ፡ ላስተምረን ፡ ነው ።

እኛ ፡—ምድብ ፡ ተ ፡ ስ ፡ ፩ኛ ፡ መደብ ፡ የወል ፡ ጾታ ፡ ብዙ ፡ ሙያው ፡ ተሳቢ ፡ ተሳቢነቱም ፡ ለማሰሪያ ፡ አንቀጹ ፡ ላስተምረን ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ፡ ግስ ።

ግስ ፡

ግስ ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ እንስሳና ፡ ስለ ፡ ዕፅ ፡ ወይም ፡ ስላንድ ፡ ሕይወት፡ ስለሌለው ፡ ነገር ፡ አንዳች ፡ ነገር ፡ መደረጉን ፡ (መሆኑን) ፡ ወይም ፡ ማድረጉን ፡ የሚገልጽ ፡ ነው ።

## ፩ ፡ የግስ ፡ ዐይነቶች ፡

የግስ ፡ ዐይነቶች ፡ ሁለት ፡ ናቸው ።

(ሀ) ተሻጋሪ ፡ ግስ ፡

አስረጅ ፡

መምህር ፡ ፋንታዬ ፡ ልጃቸውን ፡ ለመጠየቅ ፡ ወዳዲስ ፡ አበባ ፡ መጥተው ፡ ኩል ፡ የመሰለ ፡ በርኖስን ፡ ገዝተው ፡ ሸለሙት ።

(ለ) የማይሻገር ፡ ግስ ፡

አቶ ፡ በላይነህ ፡ ከትናንት ፡ ወዲያ ፡ ባይሮፕላን ፡ ወደ ፡ ካይሮ ፡ ተሳፈሩ ።

ተሻጋሪ ፡ ግስ ፡ ያድራጊውን ፡ ሥራ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ሳያስቀር ፡ ወደ ፡ ተደራጊው፡ የሚያስተላልፍ ፡ ግስ ፡ ነው ፤ ወይም ፡ ያድራጊው ፡ ሥራ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ሳይወሰን፡ ወደ ሌላ ፡ መተላለፉን ፡ የሚያመለክት ፡ ግስ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

1 ደመቀ ፡ ዱሩን ፡ መንጥሮ ፡ ጤፍን ፡ ዘራ ።

2 ፈለቀ ፡ ሰውን ፡ ያከብራል ።

3 ልጁ ፡ ይህንን ፡ ሥራ ፡ በመሥራት ፡ እንደ ፡ ደከመ ፡ ሰምቻለሁ ።

ምን ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፡ ተሻጋሪ ፡ ግስ ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ የግዴታ፡ ተሳቢ፡ ያስፈልገዋል ። አለበለዚያ ፡ ያንቀጹ ፡ ግብር ፡ የተሟላ፡ አይሆንም ። ስለዚህ ፡ የማስሪያው ፡ አንቀጽ ፡ ግብር ፡ የሚገለጽበት ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ተሳቢ ፡ ተብሎ ፡ ይጠራል ።

የማይሻገር ፡ ግስ ፡ ያድራጊው ፡ ሥራ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ሳይሻገር ፡ በሠሪው ፡ ላይ ፡ (ባድራጊው ፡ ላይ) ፡ መወሰኑን ፡ ወይም ፡ መቅረቱን ፡ የሚገልጽ ፡ ግስ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

1 መንግሥቱ ፡ በመደቡ ፡ ላይ ፡ ተኝቷል ።

2 ዘንድሮ ፡ አዝመራው ፡ ሁሉ ፡ መልካም ፡ ነው ።

3 ልጁ ፡ እየከሳ ፡ እየከሳ ፡ ሄደ ።

እንሆ ፡ በተሰጠው ፡ ማስረጃ ፡ መንግሥቱ ፡ ራሱ ፡ መተኛቱን ፡ አዝመራው ፡ መልካም ፡ መሆኑንና ፡ ልጁ ፡ መክሳቱን ፡ እናያለን፡ (እናውቃለን) እንጂ ፤ መንግሥቱና፡ አዝመራው ፡ ልጁም ፡ ተላልፈው ፡ አንዳንድ ፡ ነገር ፡ መሥራታቸውን፡ አናይም ፡ (አናውቅም) ። እንዲህ ፡ ከሆነ ፡ እነዚህን ፡ የመሳሰሉ ፡ ግሶች ፡ የማይሻገሩ ፡ መሆናቸውን ፡ ለይቶ ፡ ማወቅ ፡ ያስፈልጋል ።

ረዳት ፡ ግስ ፡ ጊዜያትን ፡ ለመለወጥ ፡ ወይም ፡ ግስ ፡ ባልሆኑት ፡ ቃላት ፡ ላይ ፡ ተጨምሮ ፡ ሙሉ ፡ ስሚትን ፡ ለመስጠት ፡ እንድንችል ፡ የምናስገባው ፡ ቃል ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

1 ከበደ ፡ መጥቷል ።
2 » መጥቶ ፡ ነበር ።
3 ልጁ ፡ በቤት ፡ ስላልተመቸውም ፡ እንደሆነም ፡ እንጃ ፡ ይሰንፍ ፡ ዠመር ።

ባማርኛችን ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ፡ ረዳት ፡ ግሶች፡ የሚሆኑት፡ «አለ»፡ ና፡ «ነበር» ናቸው ። እነዚህ ፡ ረዳት ፡ ግሶች ፡ ግሶችን ፡ የቅርብ ፡ ኀላፊ ፡ የሩቅ ፡ ኀላፊ ፡ ያሁንና፡ የትንቢት ፡ ጊዚያትን ፡ እንዲገልጹ ፡ ይረዷቸዋል ።

አለ ፡ ግስ ፡ ያልሆኑትን ፡ ቃላት ፡ እንዳንድ ፡ ግስ ፡ ሆነው ፡ ሙሉ ፡ ስሜትን ፡ እንዲሰጡ ፡ ያደርጋቸዋል ፤ እነርሱም ፡ የሚከተሉት ፡ ናቸው ።

(ሀ) ነጠላ ፡ ቃላት ፡-

ለጥ ፡ ሰጥ ፡ ብቅ ፡ ጥልቅ ፡ ዝንቅ ፡ ውሽቅ ፡ ድቅቅ ፡ ላም ፡ ብድግ ፡ ግልፍ፡ ሳብ ፡ ለቀቅ ፡ መንጠቅ ፡ መለስ ፡ ቀስቀስ ።

ምሳሌ ፡-

1 ሌሊት ፡ ታላቅ ፡ ዝናም ፡ ስለ ፡ ዘነመ ፡ ማሽላው ፡ ለጥ ፡ አለ ፡ (ለሽ ፡ አለ) ።
2 ዱሮ ፡ ያስቸግር ፡ የነበረው ፡ ሕዝብ ፡ ዛሬ ፡ ሰጥ ፡ አለ ።
3 ዓሣ ፡ በውኃ ፡ ውስጥ ፡ ብቅ ፡ ጥልቅ ፡ አለ ።
4 መንግሥቱ ፡ በማያገባው ፡ ነገር ፡ ዝንቅ ፡ አለ ።

(ለ) ድርብ ፡ ቃላት ፡-መስተዋድድ ፡ በገዛው ፡ አርእስት ፡ መድረሻ ፡ ላይ ፡ አለ ፡ ገብቶ ፡ እንደ ፡ ሕገኛ ፡ ሲሠራ ፡-

እንደ ፡ መደንገጥ ፡ እንደ ፡ መጥገብ ፡ እንደ ፡ መታመም ፡ እንደ ፡ መተው ፡ እንደ፡ መልቀቅ ፡ እንደ ፡ መዝፈን ፡ እንደ ፡ መሰልቸት ፤

ምሳሌ ፡-

1 ልጁ ፡ ሲያጠፋ ፡ በድንገት ፡ ስለ ፡ ደረስሁበት ፡ እንደ ፡ መደንገጥ ፡ አለ ።

2 ወባዋ ፡ እንደ ፡ መልቀቅ ፡ ብላኛለች ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ ራሴን፡ ማዞሯን ፡ አል ተወችኝም ።

3 ልጁ ፡ ዛሬ ፡ እንደ ፡ መፍዘዝ ፡ ብሏል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ነካው ፡ አላውቅም ።

4 ይህን ፡ ሥራ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ስለምሠራው ፡ እንደ ፡ መሰልቸት ፡ አለኝ ።

አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ሁለት ፡ ግሶች ፡ ባንድነት ፡ ሲገጣጠሙ ፡ ከሁለቱም ፡ የተለየ ፡ ትርጓሜን ፡ ይሰጣሉ ። እንደዚህ ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ አንደኛው፡ ግስ ፡ ላንደኛው ፡ ግስ፡ ረዳት፡ ነው ፡ ለማለት ፡ አያስደፍርም ።

ምክንያቱም ፡ አንደኛውን ፡ ግስ ፡ እያገዘ ፡ (እየረዳ) ፡ ስሜቱን ፡ ሊያጐላለት፡ባለ መቻሉ ፡ ነው ።

3*

አስረጅ ፡-         ቈየ ፡         አገኘ ፡

1 ፈለቀን ፡ ለመጠየቅ ፡ ወደ ፡ ሆስፒታል ፡ ብሄድ ፡ ወጥቶ ፡ ቈየኝ። ትርጓሜው፡ ፈለቀን ፡ ለመጠየቅ ፡ ወደ ፡ ሆስፒታል ፡ ብሄድ ፡ አጣሁት ፡ ማለት ፡ ነው ።

2 ፈለቀን ፡ ለመጠየቅ ፡ ወደ ፡ ሆስፒታል ፡ ብሄድ ፡ ወጥቶ ፡ አገኘሁት ። ትርጓሜው ፡ ፈለቀን ፡ ለመጠየቅ ፡ ወደ ፡ ሆስፒታል ፡ ብሄድ ፡ አጣሁት ፡ ማለት ፡ ነው ።

ስለዚህ ፡ እንደዚህ ፡ ያሉትን ፡ ግሶች ፡ ረዳት ፡ ናቸው ፡ ማለት ፡ የረዳት ፡ ግሶችን ፡ ሕግ ፡ መቃወም ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ብንተወው ፡ ይሻላል ።

ነባር ፡ ግስ ፡ እንደ ፡ ሌሎቹ ፡ ግሶች ፡ በሦስቱም ፡ ጊዜያት ፡ ለመረባት ፡ የማይችል ፡ ግስ ፡ ነው ። እርሱም ፡ ባሁን ፡ ጊዜያት ፡ ብቻ ፡ ይነገራል ፤ በኀላፊና ፡ በትንቢት ፡ ጊዚያት ፡ ግን ፡ ስለርሱ ፡ ሆነው ፡ የሚሠሩለትን ፡ ቃላት ፡ ይፈልጋል ።

አስረጅ ፡-

(ሀ) ጠብቆ ፡

1 ፈለቀ፡ አንድ ፡ መጽሐፍ ፡ አለው ።
2 » » » ነበረው ።
3 » » » ኖሮታል ።
4 » » » ኖሮት ፡ ነበር ።
5 » » » ይኖረዋል ።

(ለ) አለ ፡ ጠብቆ ፡

1 መንግሥቱ ፡ በዚህ ፡ አገር ፡ አለ ።
2 » » » ኖረ ።
3 » » » ኖሯል ።
4 » » » ኖሮ ፡ ነበር ።
5 » » » ይኖር ፡ ነበር ።

(ሐ)

1 ልጁ ፡ ጎበዝ ፡ ነው ።
2 » » ነበር ።
3 » » ይሆናል ።
4 » » ሆኗል ።
5 » » ሆኖ ፡ ነበር ።

ነባር ፡ ግስ ፡ በግብሩ ፡ ከተሻጋሪ ፡ ወይም ፡ ከማይሻገር ፡ ግስ ፡ ስለማይወጣ ፡ለብቻው ፡ እንዳንድ ፡ የግስ ፡ ዐይነት ፡ ሊቈጠር ፡ አይገባውም ። እኛ ፡ ለተማሪዎች ፡ ማስረዳት ፡ የሚገባን ፡ በግስ ፡ ዐይነቶች ፡ ውስጥ ፡ ተጠቅልሎ ፡ መነገሩንና ፡ እንደ ፡ ሕገኛው፡ ግስ ፡ በጊዜያቱ ፡ ሁሉ ፡ ለመርባት ፡ አለመቻሉን ፡ ነው ።

## ፬ ፡ የማይሻገር ፡ ግስ ፡

የማይሻገር ፡ ግስ ፡ ራሱን ፡ የቻለና ፡ ራሱን ፡ ያልቻለ ፡ ተብሎ ፡ በሁለት ፡ ይከፈላል ። ራሱን ፡ የቻለ ፡ የማይሻገር ፡ ግስ ፡ ፍጹም ፡ የሚያደርጉትን ፡ መሙሊያ ፡ ቃላት ፡ ሳይፈልግ ፡ በገዛ ፡ ራሱ ፡ ሙሉ ፡ ስሜትን ፡ ለመስጠት ፡ የሚችል ፡ ነው ።

አስረጅ ፡-

1 ከበደ ፡ ከዛፍ ፡ ወደቀ ።
2 ወርቅነህ ፡ በአልጋው ፡ ላይ ፡ ተኛ ።
3 ፈለቀች ፡ ወደ ፡ ገበያ ፡ ሄደች ።
4 መኰንን ፡ በወንበር ፡ ላይ ፡ ተቀመጠ ።

ራሱን ፡ ያልቻለ ፡ የማይሻገር ፡ ግስ ፡—በገዛ ፡ ራሱ ፡ ሙሉ ፡ ስሜትን ፡ ለመስጠት ፡ ስለማይችል ፡ ፍጹም ፡ የሚያደርጉትን ፡ መሙሊያ ፡ ቃላት ፡ የሚፈልግ ፡ ግስ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡-

1 ፈለቀ ፡ ሰነፍ ፡ ልጅ ፡ ነው ።

2 ፈለቀ ፡ ይህን ፡ ሥራ ፡ ያጣው ፡ ባለመታገሡ ፡ ነው ።

3 እናንት ፡ ወጣቶች ፡ የኢትዮጵያ ፡ አበቦች ፡ ናችሁ ፤ ስለዚህ ፡ እያንዳንዳችሁን ፡ እንደ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ አበቦች ፡ እንቈጥራችኋለን ።

4 የዘለቀ ፡ ዐመል ፡ ወርቅ ፡ ነው ።

ነው ፡ ከሚል ፡ ግስ ፡ ጋራ ፡ የሚገባ ፡ ስም ፡ ወይም ፡ ቅጽል ፡ አንቀጹን ፡ በጐደለ ፡ ሞልቶ ፡ ፍጹም ፡ ከማድረጉ ፡ በላይ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ተመልሶ ፡ ያንቀጹን ፡ ባለቤት ፡ ይገልጻል ። እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ አረጋጋጭ ፡ ወይም ፡ አንቀጹን ፡ ፍጹም ፡ አድራጊ ፡ እያሉ ፡ ከመጥራት ፡ መሙሊያ ፡ ማለት ፡ የጐደለውን ፡ ማስተካከያ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የመሆንን ፡ ግስ ፡ መሙሊያ ፡ ብለን ፡ ብንጠራው ፡ በጣም ፡ የተሻለ ፡ ነው ። በተውሳከ ፡ ግስ ፡ ክፍል ፡ ያንቀጽ ፡ ተጨማሪ ፡ የሚባል ፡ የተስማማ ፡ ስም ፡ ስላለ ፡ መሙሊያ ፡ የሚባለውን ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ተገቢው ፡ ቦታ ፡ ማዞር ፡ አለብን ፤ ስለዚህ ፡ በዚች ፡ መጽሐፍ ፡ መሙሊያ ፡ የምንለው ፡ ላንቀጹ ፡ ተጨማሪ ፡ አለመሆኑንና ፡ ለመሆን ፡ ግስ ፡ ግን ፡ መሙሊያ ፡ መሆኑን ፡ ማስተዋል ፡ አለብን ።

የማይሻገር ፡ ግስ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ዘመዳዊ ፡ ተሳቢን ፡ ሲስብ ፡ ይገኛል ። ዘመዳዊ ፡ ተሳቢ ፡ ማለትም ፡ ተሳቢው ፡ ከዚያው ፡ ከማሰሪያው ፡ አንቀጽ ፡ የመጣ ፡ ማለት ፡ ነው ። ዘመዳዊ ፡ ተሳቢ ፡ ለማይሻገር ፡ ግስ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ ለተሻጋሪ ፡ ግስም ፡ ይኖረዋል ።

አስረጅ ፡ ዘመዳዊ ፡ ተሳቢ ፡ በማይሻገር ፡ ግስ ፡

1 ዛሬ ፡ ታላቅ ፡ አወዳደቅን ፡ ወደቅሁ ።
2 መንግሥቱ ፡ ክፉ ፡ አሟሟትን ፡ ሞተ ።

በሚሻገር ፡ ግስ ፡

1 አንድ ፡ ትልቅ ፡ ቅርጽን ፡ አሳምሮ ፡ ቀረጸ ።
2 እንደ ፡ ደረሰ ፡ ምግቡን ፡ ተመገበ ።

የማይሻገር ፡ ግስ ፡ በባዕድ ፡ መነሻ ፡ ረዳትነት ፡ ተሻጋሪ ፡ ይሆናል ። የማይሻገረውን ፡ ግስ ፡ ተሻጋሪ ፡ የሚያደርጉት ፡ ፊደላት ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ አ ፡ አስ ፡ አስተ ፡ ናቸው ።

<u>ምሳሌ</u> ፦ ወረደ ፡ አወረደ፡ አስወረደ ፡ ተቀመጠ ፡ አስቀመጠ ፡ አደረ ፡ አሳደረ ፡ አስተዳደረ፡ ተኛ ፡ አስተኛ ፡ ሞተ ፡ አሞተ ፡ አስተሞተ ፡

<u>አስረጅ ፦</u>

1 አየለ ፡ በጧት ፡ ወደ ፡ ቆላ ፡ ወረደ ።

2 መንገሻ ፡ ከዛፉ ፡ ላይ ፡ የወፉን ፡ ጎጆ ፡ አፍርሶ ፡ አወረደው ።

3 ባለፈው ፡ ዓመት ፡ ወይዘሮ ፡ ፈለቀችን ፡ ምች ፡ ክፉኛ ፡ አስወረዳት ።

የማይሻገር ፡ ግስን ፡ ተገብሮ ፡ ብለን ፡ ልንጠራው ፡ አይገባም ። በተገብሮና ፡ በማይሻገር ፡ ግስ ፡ መካከል ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ልዩነት ፡ አለ ። ተገብሮ ፡ ግስ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ወይም ፡ አንድ ፡ እንስሳ ፡ ወይም ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ባንድ ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ ወይም ፡ ባንድ ፡ ነገር ፡ እንደ፡ ተጎዳ ፡ ወይም ፡ እንደ ፡ ተመታ ፡ ወይም ፡ እንደ ፡ ተመከረ ፡ ወይም ፡ እንደ፡ ተሰደበ ፡ ወይም ፡ እንደ ፡ ተሰበረ ፡ ወይም ፡ እንደ ፡ ተሠራ ፡ ወይም ፡ እንደ ፡ ተቈጠረ ፡ የሚያመለክት ፡ ግስ ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ ተገብሮ ፡ ግስ ፡ የሰውን ፡ ወይም ፡ ያንዳች ፡ ነገርን፡ ሥራ ፡ (ድርጊት) ፡ ተቀባይ ፡ መሆኑን ፡ ያመለክታል ፡ እንጂ ፤ እርሱ ፡ ራሱ ፡ ሠርቶ ፡ ድርጊቱ ፡ በገዛ ፡ ራሱ ፡ ላይ ፡ መቅረቱን ፡ አያመለክትም ።

ነገር ፡ ግን ፡ የማይሻገር ፡ ግስ ፡ ሠራተኛው ፡ (አድራጊው)፡ ሰው ፡ ወይም ፡ ነገር፡ የሌላውን ፡ ሰው ፡ ወይም ፡ የሌላውን ፡ ነገር ፡ ሥራ ፡ ተቀባይ ፡ ሳይሆን ፡ ራሱ ፡ በገዛ ፡ እጁ ፡ መሄድም ፡ መቀመጥም ፡ መነሣትም ፡ መተኛትም ፡ መገላበጥም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሠርቶ ፡ እንደምናየው ፡ ሥራው ፡ በገዛ ፡ ራሱ ፡ ላይ ፡ መቅረቱን ፡ የሚያመለክት ፡ ግስ ፡ ነው ። እንግዴህ ፡ በተሻጋሪነት ፡ ሳይሆን ፡ ሥራውን ፡ ሠርቶ ፡ ድርጊቱን ፡ ከባለቤቱ ፡ አልፎ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ መተላለፍን ፡ የማያሳየውን ፡ ግስ ፡ የማይሻገር ፡ ብለን ፡ መጥራት፡ አለብን ።

<u>አስረጅ ፦</u>

1 ቅዱስ ፡ ጴጥሮስ ፡ ታላቁ ፡ የኢትዮጵያ ፡ አርበኛ፡ (በመንፈሳዊና ፡ በሥጋዊ)፡ እንዳንድ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ላይ ፡ በጥይት ፡ ተደበደቡ ።

2 መኰንን፡ በጧት፡ (ከንጋቱ)፡ ባሥራ፡ ሁለት፡ ሰዓት፡ ተኲል ፡ ከእንቅልፉ፡ነቃ።

እንሆ ፡ ባንደኛውና ፡ በሁለተኛው ፡ የተነገሩት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ብዙ ፡ ልዩነት ፡ እንዳላቸው፡ እናያለን ። አንደኛው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ አባታችን ፡ <u>ብፁዕ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ</u> ፡ በጣሊያኖች ፡ እጅ ፡ ተደብድበው ፡ መሞታቸውን ፡ ያሳያል ።

ሁለተኛው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ደግሞ ፡ መኰንን ፡ ራሱ ፡ ከእንቅልፉ፡ በገዛ፡ ራሱ ፡ እንደ ፡ ነቃ ፡ ያመለክታል ፤ ስለዚህ ፡ ልዩነታቸውን ፡ በዚሁ ፡ ዐይነት ፡ መመልከት ፡ ያስፈልጋል ።

ማስገንዘቢያ ፡- ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ጽሑፉን ፡ አንብቦ ፡ የጸሓፊውን ፡ አሳብ፡ ሳይረዳ ፡ መንቀፍና ፡ ማመስገን ፡ አይገባውም ። ስለዚህ ፡ በሁለት ፡ ነገሮች ፡ መካከል ፡ ልዩነት ፡ አለ ፡ ተብሎ ፡ በተነገረ ፡ ጊዜ ፡ የሁለቱን ፡ ልዩነት ፡ ለማወቅ ፡ መጣጣር ፡ አለ በት ።

## ፫፡ ተሻጋሪ፡ ግስ ፡

ተሻጋሪ ፡ ግስ ፡ ድርጊቱ ፡ በገዛ ፡ ራሱ ፡ ላይ ፡ ተወስኖ ፡ ስለማይቀር ፡ የግዴታ ፡ ተሳቢ ፡ የሚሆነውን ፡ ነገር ፡ ይፈልጋል ።

### የተሳቢ ፡ ዐይነቶች ፡

(ሀ) ፡ ነጠላ ፡ ተሳቢ ፡

| | | |
|---|---|---|
| ፩፡ ስም ፡ | ፬ ፡ ጥሬ ፡ ዘር ፡ | ፯ ፡ ስማዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ |
| ፪፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ | ፭ ፡ በቂ ፡ ቅጽል፡ | ፰ ፡ በጥቅስ ፡ ሙሉው ፡ አ ፡ ነ ፡ |
| ፫፡ አርእስት ፡ | ፮ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ | ፱ ፡ ሳቢ ፡ ዘር ፡ |

(ለ) ድርብ ፡ ተሳቢ ፡

ድርብ ፡ ተሳቢ ፡ በሁለት ፡ ይከፈላል ።

(፩) ያልተተካከለ ፡ ድርብ ፡ ተሳቢ ፡ ሁለት ፡ ቃላት ፡ በወደረኛ ፡ መስተፃምር ፡ ሳይጫ ፈሩ ፡ ሁለቱም ፡ ላንቀጹ ፡ የሚገዙ ፡ ናቸው ።

(፪) ተተካካይ ፡ ድርብ ፡ ተሳቢ ፡ ሁለት ፡ ወይም ፡ ከሁለት ፡ የበለጡ ፡ ስሞች ፡ በወደረኛ፡ መስተፃምር ፡ እየተያያዙ ፡ ለተሻጋሪው ፡ አንቀጽ ፡ የሚገዙ ፡ ናቸው ።

አስረጅ ፡- መዠመሪያ ፡ ነጠላ ፡ ተሳቢን ፡ እናሳያለን ።

(ሀ) ነጠላ ፡ ተሳቢ ፡

1 ልጁ ፡ ጠረጴዛውን ፡ አሳምሮ ፡ (ደኅና ፡ አድርጎ) ፡ ወለወለው ።
2 አሁን ፡ እናንተን ፡ አላሠራችሁም ።
3 ልጆቼ ፡ ሆይ ፡ መንገላወድን ፡ አትውደዱ ።
4 ምክርን ፡ ባገባቧ ፡ ከለሰለሰ ፡ እንጀራ ፡ የምትመረጥ ፡ አድርጋችሁ፡ ውደዷት።
5 አቶ ፡ ማንደፍሮት ፡ አነጋገርን ፡ ያሳምራል ።
6 ኰራት ፡ ወዳጆቿን ፡ ኰሩዎቹን ፡ ይጥላቸዋል ።
7 ክረምት ፡ ከመግባቱ ፡ በፊት፡ ማገዶ፡ መሰብሰብን ፡ (ማጠራቀምን)፡እወዳለሁ።
8 ዛሬ ፡ ከናንተ ፡ መካከል ፡ ወዳዲስ ፡ አበባ ፡ የሚሳፈረውን ፡ ጥራው ።

(ለ) ያልተተካከለ ፡ ድርብ ፡ ተሳቢ ፡

መጽሐፉን ፡ መልሼለታለሁ ። (መጽሐፉን ፡ ለርሱ ፡ መልሼለታለሁ)፡ ማለት ፡ ነው ። ባለቤቱ ፡ እኔ ፡ የሚለው ፡ ቃል ፡ ነው ፤ ቀጥተኛ ፡ ተሳቢው ፡ ደግሞ ፡ መጽሐፉ ፡

ነው ። ኢ.ርቱዕ ፡ ተሳቢ.ውም ፡ እርሱ ፡ ነው ፤ ኢ.ርቱዕና ፡ ርቱዕ፡ ባንድነት ፡ ለግሱ ፡ ስለሚ ገዙ ፡ ያልተተካከለ ፡ ድርብ ፡ ተሳቢ. ፡ ይባላሉ ።

(ሐ) ተተካካይ ፡ ድርበ ፡ ተሳቢ. ፡

1 አሰፋ ፡ በቀለንና ፡ ተስፋዬን ፡ በባቡር ፡ ወደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ አሳፈራቸው ።

2 በቀለንና ፡ ተስፋዬን ፡ እንደሻውንም ፡ ወደ ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ ላከኋቸው ።

እንሆ ፡ ባንደኛውና ፡ በሁለተኛው ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ስሞቹ ፡ በርግጥ ፡ በወደ ረኛ ፡ መስተፃምር ፡ ተያይዘው ፡ ድርብ ፡ ተሳቢ ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ አስተውል ።

## ፩ ፡ የገቢርና ፡ የተገብሮ ፡ ግሶች ፡

ከተሻጋሪ ፡ ላይ ፡ ተገብሮ ፡ ግስ ፡ ይመሠረታል ።

ገቢር ፡ ግስ ፡ ያድራጊው ፡ ግብር ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ሳይወሰን ፡ ወደ ፡ ተደራጊው ፡ ማለፍን ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

1 በቀለ ፡ የመንግሥቱን ፡ ልብስ ፡ ተኰሰ ።

2 ደመቀ ፡ ሲንቀጠቀጥ ፡ ብልቃጡን ፡ ሰበረው ።

3 ተክለ አብ ቀለሙን አፈሰሰው ።

ተገብሮ ፡ ግስ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ወይም ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ (እንደ ተደረገ) ፡የሚያመለክት ፡ ግስ ፡ ነው ።

<u>አስረጅ</u> ፡-

1 ጤፉ ፡ ታጨደ ።

2 ወገቡ ፡ ተሰበረ ።

3 የበቀለ ፡ ልብስ ፡ በመንግሥቱ ፡ እጅ ፡ ተተኰሰ ።

በገቢር ፡ የተነገረው ፡ ነጠላ ፡ ተሳቢ ፡ ያለበት ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ተገብሮ ፡ ይለወጣል ።

የሚከተሉት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ተለወጡ ፡ አስተውል ።

<u>አስረጅ</u> ፡-

1 እንዳለች ፡ ብርጭቆውን ፡ ሰበረችው ።

2 ደመቀ ፡ መስኰቱን ፡ ከፈተው ።

## የተለወጠው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡

1 ብርጭቆው ፡ በእንዳለች ፡ እጅ ፡ ተሰበረ ።

2 መስኰቱ ፡ በደመቀ ፡ እጅ ፡ ተከፈተ ።

ያልተተካከለ ፡ ድርብ ፡ ተሳቢ ፡ ያለበት ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ከገቢርነት፡ ወደ ፡ ተገብሮነት ፡ ከተገብሮነት ፡ ወደ ፡ ገቢርነት ፡ ይለወጣል ።

አስረጅ ፡-

1 ቆንጆ ፡ መጽሐፍን ፡ ሸለምሁት ።

2 ትናንትና ፡ ቆንጆ ፡ ደብዳቤን ፡ ጻፍኩለት ።

3 ከእኔ ፡ እጅ ፡ ቆንጆ ፡ መጽሐፍን ፡ ተሸለመ ።

4 ትናንትና ፡ ከእኔ ፡ አንድ ፡ ደብዳቤ ፡ ተጻፈለት ።

የተተካከለ ፡ ድርብ ፡ ተሳቢ ፡ ያለበት ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ከተገብሮነት ፡ ወደ ፡ ገቢርነት ፡ ከገቢርነት ፡ ወደ ፡ ተገብሮነት ፡ ሊለወጥ ፡ ይቻላል ።

አስረጅ ፡-

1 ደመቀና ፡ ፈለቀ ፡ ባስተማሪያችን ፡ አንደበት ፡ ተመከሩ ።

2 ቀለሚና ፡ ወርቅነህ ፡ በለጠችም ፡ ባባታችን ፡ እጅ ፡ ተቀጡ ።

3 አስተማሪያችን ፡ ደመቀንና ፡ ፈለቀን ፡ መከሯቸው ።

4 አባታችን ፡ ቀለሚንና ፡ ወርቅነህን ፡ በለጠችንም ፡ ቀጧቸው ።

## የገቢርና ፡ የተገብሮ ፡ አለዋወጥ ፡ ዘዴ ፡

(ሀ) ከገቢርነት ፡ ወደ ፡ ተገብሮነት ፡ አንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሲለወጥ ፡ ባንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ተሳቢው ፡ ነጠላ ፡ ወይም ፡ ተተካካይ ፡ ድርብ ፡ የሆነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ተሳቢው ፡ ወይም ፡ ተሳቢዎቹ ፡ ላንቀጹ ፡ ባለቤት ፡ ይሆናሉ ። ዋናው ፡ ባለቤትም ፡ የመስተዋድድ ፡ ተገዥ ፡ ይሆናል ። አንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ከገቢርነት ፡ ወደ ፡ ተገብሮነት ፡ ሲለወጥ ፡ ተሳቢው ፡ ያልተተካከለ ፡ ድርብ ፡ ተሳቢ ፡ የሆነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ግን ፡ መስተዋድድ ፡ የጎደለው ፡ ቃል ፡ ባለቤት ፡ ይሆንና ፡ ላንቀጹ ፡ ባለቤት ፡ የሆነው ፡ ቃል ፡ የመስተዋድድ ፡ ተገዥ ፡ ይሆናል ፤ ርቱዕ ፡ (ቀጥተኛ) ፡ ተሳቢ ፡ የነበረው ፡ ቃል ፡ ግን ፡ ሳይለወጥ ፡ እንዳለ ፡ ላንቀጹ ፡ ይሳባል ።

(ለ) ከተገብሮነት ፡ ወደ ፡ ገቢርነት ፡ አንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሲለወጥ ፡ የመስተዋድድ ፡ ተገዢ ፡ የነበረው ፡ ባለቤት ፤ ባለቤት ፡ የነበረውም፡ ቀጥተኛ ፡ ተሳቢ፡ ይሆናል። የመስጠትን ፡ ምግባር ፡ የሚያመለክተው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሲለወጥ ፡ ግን ፡ የተሰጠው ፡ ነገር ፡ እንዳለ ፡ ተሳቢ ፡ ሆኖ ፡ የመስተዋድድ ፡ ተገዢ ፡ የነበረው ፡ ባለቤት ፡ ባለቤት ፡ የነበረው ፡ የመስተዋድድ ፡ ቃል ፡ ውስጠ ፡ ታዋቂ ፡ ሆኖለት ፡ ኢርቱዕ ፡ ተሳቢ ፡ ይሆናል።

## ፭ ፡ የግስ ፡ ስልት ፡

የግስ ፡ ስልት ፡- አንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ በምን ፡ ዐይነት ፡ አኳኋን ፡ እንደ ፡ ተነገረ ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

(ሀ) የስልት ፡ ዐይነቶች ፡

፩ የሚያስሩ ፡ አንቀጾች ፡

1 ዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡

2 ትእዛዛዊ ፡ አንቀጽ ፡

3 አዋዋይ ፡ አንቀጽ ፡ በተምኔታዊ ፡ ብቻ ፡

፪ ፡ የማያስሩ ፡ አንቀጾች ፡

ንኡስ ፡ አንቀጽ ፡ ከነጅሮቹ ፡

ዐቢይ፡ አንቀጽ፡- ሐተታዊ፡ (ተራኪ)፡አረፍተ፡ ነገርን፡ የሚገልጽ፡ አንቀጽ፡ ነው።

ትእዛዛዊ ፡ አንቀጽ ፡- የማዘዝን ፡ ምግባር ፡ የሚገልጽ ፡ ስልት ፡ ነው ።

አዋዋይ ፡ አንቀጽ ፡- ጸጸንት ፡ ምኞትን ፡ ዐላማንና ፡ ውለታን ፡ የሚያመለክት ፡ አንቀጽ፡ ነው ።

ንኡስ ፡ አንቀጽ ፡- ብዙ ፡ አንቀጽን ፡ ጥሬ ፡ ዘርን ፡ ሳቢ ፡ ዘርን ፡ አርእስትንና ፡ ግሳዊ ፡ ቅጽልን ፡ ይዞ ፡ ለማሰር ፡ የማይችል ፡ ግስ፡ ነው ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ ማንኛውንም ፡ የሥራ ፡ ዐይነት ፡ ለመግለጽ ፡ የሚችል ፡ ግስ ፡ ነው ።

(ለ) የግስ ፡ ጊዜያት ፡- አንድ ፡ ግስ ፡ የሥራን ፡ ጊዜ ፡ የሚያመለክትበት ፡ ነው ።

1 ያሁን ፡ ጊዜያት ፡- ፈለቀ ፡ ምሳውን ፡ ይበላል ፤ ትርጕሙ ፡ ፈለቀ ፡ ምሳውን ፡ በመብላት ፡ ላይ ፡ ነው ፡ ማለት ፡ ነው ።

2 ኀላፊ ፡ ጊዜያት ፡ መንግሥቱ ፡ ፈሰሱን ፡ አበጀው ።

3 የትንቢት ፡ ጊዜያት ፡- ፈለቀ ፡ ከነገ ፡ ወዲያ ፡ ይመጣል ።

ግስ ፡ ሦስት ፡ ጊዜያት ፡ አሉት። እርነሱም ፡ ያሁን ፡ የትንቢትና ፡ ኀላፊ ፡ ጊዜ ፡ ያት ፡ ናቸው ። የግስ ፡ ጊዜያት ፡ እያንዳንዳቸው ፡ ሦስት ፡ ባህሎች ፡ አሏቸው ።

፩ኛ ፡ ያልተወሰነ ።

1 ያሁን ፡ ጊዜያት ፡- አሁን ፡ የሚደረገውን ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

(ሀ) ልጁ ፡ እራቱን ፡ ይበላል ። መምህሩ ፡ በሰሌዳው ፡ ላይ ፡ ይጽፋል ።

(ለ) መንግሥቱና ፡ አሸናፊ ፡ በገበታ ፡ ላይ ፡ ይደባደባሉ ።

(ሐ) መንግሥቱ ፡ አበባ ፡ ቅጠፍና ፡ አምጣልኝ ።

(መ) ሁላችንም ፡ ባንድነት ፡ ሆነን ፡ እንለምነው ።

(ሠ) አሸናፊ ፡ በመጥረቢያው ፡ ድግር ፡ ይጠርብበታል ።

2 ኀላፊ ፡ ጊዜያት ፡- ባለፈው ፡ ጊዜ ፡ የተደረገውን ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።
በየነ ፡ ልጆቹን ፡ መከራቸው ።
ደነቀ ፡ ያልለከ ፡ በጣም ፡ ተከራከረ ።

3 ትንቢታዊ ፡ ጊዜያት ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ የሚሆነውን ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።
መንገሻ ፡ ነገ ፡ ወደ ፡ ጎንደር ፡ ይሄዳል ፡ (ይሳፈራል) ።
ወይዘሮ ፡ ፈለቀች ፡ ከነገ ፡ ወዲያ ፡ ጥልፍን ፡ ታስተምራለች ።

ባማርኛችን ፡ ያሁንና ፡ የትንቢት ፡ ጊዚያት ፡ አንድ ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ የጊዚያት ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ካልተጨመሩባቸው ፡ አይለዩም ።

ሦስቱ ፡ ጊዚያት ፡ ያልተወሰኑ ፡ የሚሆኑበት ፡ ምክንያት ፡ ግሶቹን ፡ የሚገልጹ ፡ ቃላት ፡ ካልተጨመሩ ፡ የተወሰነውን ፡ ሰዓት ፡ ወይም ፡ ቀን ፡ ወይም ፡ ወርና ፡ ዓመት ፡ ስለማያመለክቱ ፡ ነው ።

፪ኛ ፡ የማያቋርጥ ፡ ግስ ፡

የማያቋርጥ ፡ ግስ ፡ የተዠመረው ፡ ሥራ ፡ ባለማቋረጥ ፡ መሠራቱን ፡ የሚነግር ፡ ግስ ነው ።

ባማርኛችን ፡ ባሁንና ፡ በትንቢት ፡ ጊዚያት ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ የሚሠራበት ፡ የማያ ቋርጥ ፡ የለንም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ይሄድ ፡ ዠመር ፡ ይበላ ፡ ዠመር ፡ እየተባለ ፡ ይነገራል ። ይህም ፡ አድራጊው ፡ ከጥቂት ፡ ቀኖች ፡ ወዲህ ፡ ዠምሮ ፡ በቀን ፡ በቀኑ፡ ይሠራል፡ ማለት ፡ ነው ። ቢሆንም ፡ መብላትን ፡ ይዟል ፡ (ይበላል) ፡ ማለትና ፡ ይበላ ፡ ዠመር ፡ ማለት ፡ አንድ ፡ አይደሉም ፡ ይባላል። (መብላትን፡ ይዟል)፡ ወይም፡ በገበታ፡ ላይ ፡ ነው ፡ ማለት ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ ያሁንና ፡ የትንቢት ፡ ጊዚያት ፡ ባማርኛችን ፡ እንደማያቋርጥ ፡ ጭምር ፡ ይሠራሉ ።

<u>አስረጅ</u> ፡-

| ባሁን ፡ ጊዚያት ፡ | በኀላፊ ፡ ጊዚያት ፡ |
|---|---|
| መንግሥቱ ፡ አልጋውን ፡ ያነጥፋል ። | መንግሥቱ፡ አልጋውን ፡ ያነጥፍ፡ ነበር ። |
| ፈለቀ ፡ ራቱን ፡ ይበላል ። | ፈለቀ ፡ ራቱን ፡ ይበላ ፡ ነበር ። |

አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ወይም ፡ አልፎ ፡ አልፎ ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ መሥራትን ፡ የሚያ መለክት ፡ (የሚያስታውቅ) ፡ ግስ ፡ የማያቋርጥ ፡ ግስ ፡ እየተባለ ፡ የሚጠራ ፡ አለ ። ይኸውም ፡ ግስ ፡ የመድረሻ ፡ ፊደሉን ፡ እየደገመ ፡ የሚነገር ፡ ግስ ፡ ነው ። ከሌሎቹ፡ ግሶች ፡ ተለይቶ ፡ የሚታወቅበት ፡ ከመጨረሻ፡ ፊደሉ ፡ ሁለተኛው ፡ ራብዕ ፡ ስለሚሆን ፡ ነው ።

<u>አስረጅ</u> ፡- በሁሉም ፡ ጊዚያት ፡ ሊረባ ፡ ይችላል ።

ልጁ ፡ ወደ ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ ይሂያሂዳል ።

እንሆ ፡ ልጁ ፡ ካንድ ፡ ቀን ፡ ወይም ፡ ካንድ ፡ የሚበልጡ፡ ቀኖች ፡ እየቀረ ፡ ወደ ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ መሄዱን ፡ ያመለክታል ፡ እንጂ ፤ ሳያሠልስ ፡ መሄ ዱን ፡ አያስረዳም ። ስለዚህ ፡ እንደዚህ ፡ ያለው ፡ ግስ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ሥራውን ፡ ያዝ ፡ ለቀቅ ፡ ማድረጉን ፡ ስለሚያሳይ ፡ <u>ጣልቃ ፡ አስገቢ</u> ፡ ቢባል ፡ በጣም ፡ የተሻለ ፡ ነው ።

<u>፫ኛ ፡ ሥራን ፡ በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የሚያሳይ</u> ፡

፩ ፤ የቅርብ ፡ ኀላፊ ፡ ከጥቂት ፡ ጊዜ ፡ በፊት ፡ የተደረገውን ፡ ነገር ፡ የሚገልጽ ፡ ጊዜ ፡ ነው ። ይሁን ፡ እንጂ ፤ የዋለ ፡ ያደረ ፡ ሥራን ፡ አያመለክትምና ፤ ትናንት ፡ መጥቻ ለሁ ፡ እንዳንል ፡ መጠንቀቅ ፡ አለብን ።

አስረጅ ፡

1 ይህ ፡ ልጅ ፡ ሃያ ፡ ዓመት ፡ ሆኖታል ።

2 ምሳዬን ፡ አሁን ፡ በልቻለሁ ፤ ስለዚህ ፡ አታስቢ ።

፪ ፡ የሩቅ ፡ ኅላፊ ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ የተደረገበትን ፡ ጊዜ ፡ ከቅርብ ፡ ኅላፊ ፡ ይልቅ ፡ ቀደም ፡ ያለ ፡ ወይም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ የቈየ ፡ መሆኑን ፡ የሚያመለክት ፡ ጊዜ ፡ ነው ።

አስረጅ፡- 1 በቀለን ፡ ለመጥራት ፡ (ለመፈለግ) ፡ መጥቶ ፡ ነበር ።

2 የዛሬ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ድሬ ፡ ዳዋ ፡ ላይ ፡ አይቼዎት ፡ ነበር ።

## ፯ ፡ የግስ ፡ ቍጥርና ፡ መደብ ፡

የግስ ፡ ቍጥር ፡ በባለቤቱ ፡ ይወሰናል ።

፩ ፡ ባለቤቱ ፡ ነጠላ ፡ ሲሆን ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጹም ፡ ነጠላ ፡ ይሆናል ።

(ሀ) ወደ ፡ ቤቴ ፡ እሄዳለሁ ።

(ለ) ፈለቀ ፡ ከወዴት ፡ ትመጣለህ ?

(ሐ) ደመቀ ፡ በፈተና ፡ አንደኛ ፡ ሆነ ።

፪ ፡ ባለቤቱ ፡ የብዙ ፡ ሲሆን ፡ ማሠሪያ ፡ አንቀጹም ፡ የብዙ ፡ ቍጥር፡ ይሆናል ።

(መ) ትናንትና ፡ በዚህ ፡ ሰዓት ፡ ሥራችንን ፡ አልጨረስንም ፡ ነበር ።

(ሠ) እናንተ ፡ ከሥራ ፡ እስክትመለሱ ፡ ይህን ፡ መጽሐፍ ፡ እያነበብሁ ፡ እጠብቃችኋለሁ ።

(ረ) መኰንንና ፡ ፈለቀ ፡ በክፍል ፡ ውስጥ ፡ ያጠናሉ ።

የግስ ፡ መደብ ፡ በተውላጠ ፡ ስሞች ፡ መወሰን ፡ አለበት ።

### ፩ኛ ፡ መደብ ፡

(ሀ) ዛሬ ፡ ምሳዬን ፡ ሳልበላ ፡ ዋልሁ ።

(ለ) የገና ፡ በዓል ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ቤታችንን ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ አበቦች ፡ እናስጌጣለን ።

### ፪ኛ ፡ መደብ ፡

(ሀ) ወደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ መቼ ፡ ትሄዳለህ ?

(ለ) በቀለች ፡ ምሳሽን ፡ ነዪና ፡ ብዪ ።

(ሐ) እናንተ ፡ ልጆች ፡ ዐርፋችሁ ፡ ተኙ ።

(መ) ረዳት ፡ አያስፈልግዎትም ፤ እርስዎ ፡ ራስዎ ፡ ይሠሩታል ።

### ፫ኛ ፡ መደብ ።

1 ደመቀ ፡ ቤቱን ፡ ወልውሎታል ።

2 ፈለቀች ፡ ምሳዋን ፡ አልበላችም ።

3 እርሳቸው ፡ ዘወትር ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ መቅረትን ፡ ይወዳሉ ።

4 እነአየለ ፡ ከሰዓት ፡ በኋላ ፡ ይመለሳሉ ።

5 ይህን ፡ ዕቃ ፡ እንዳንወስድ ፡ የከለከሉን ፡ እነሱ ፡ ናቸው ።

## ፯ ዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡

ሦስቱ ፡ የዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡ ጊዜያት ፡

(ሀ) ገቢር ፡ ግስ ፡ ኀላፊ ፡ ጊዜያት ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| መረቀ ፡ | አስመረቀ ፡ | አመራረቀ ፡ | አማረቀ ፡ |
| መርቋል ፡ | አስመርቋል ፡ | አመራርቋል ፡ | አማርቋል ፡ |
| መርቆ ፡ ነበር፡ | አስመርቆ ፡ ነበር ፡ | አመራርቆ፡ ነበር ፡ | አማርቆ፡ነበር ፡ |

(ለ) ገቢር ፡ ግስ ፡ ያሁንና ፡ የትንቢት ፡ ጊዜያት ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| ይመርቃል ፡ | ያስመርቃል፡ | ያመራርቃል ፡ | ያማርቃል ፡ |
| ሊመርቅ፡ ነው፡ | ሊያስመርቅ፡ ነው፡ | ሊያመራርቅ፡ ነው፡ | ሊያማርቅ፡ ነው ። |

ማናቸውም፡ ተራ ፡ ግስ፡ ተሻጋሪ፡ ወይም ፡ የማይሻገር፡ ሆኖ፡ እያንዳንዱ ፡ ዐምድ፡ ነው ። ካንዱ ፡ ተሻጋሪ ፡ ዐምድ ፡ ላይ ፡ በባዕድ ፡ መነሻ ፡ ረዳትነት ፡ አስደራጊ ፡ አደራራጊ ፡ አዳራጊ ፡ ተደራጊ ፡ ተደራራጊ ፡ ተዳራጊ ፡ ይመሠረታሉ ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ አደራራጊና ፡ ተዳራጊ ፡ ካንዳንድ ፡ ግሶች ፡ ላይ ፡ ይታጣሉ ።

ምሳሌ ፡-

ደረደረ፡ አስደረደረ፡ አደራደረ፡ ተደረደረ፡ ተደራደረ፡
ጠረገ፡ አስጠረገ፡ አጠራረገ ፡ አጣረገ፡ ተጠረገ ፡ ተጠራረገ፡ ተጣረገ ፡

ማስገንዘቢያ ፡- ጠረገ ፡ ከሚባለው ፡ ካንዱ ፡ ግስ ፡ ላይ ፡ በባዕድ ፡ መነሻ ፡ ረዳትነት ፡ ስድስት ፡ ግሶች ፡ እንደ ፡ ተመሠረቱ ፡ አስተውል ።

ካንዱ ፡ ከማይሻገር ፡ ዐምድ ፡ ላይ ፡ በባዕድ ፡ መነሻ ፡ ረዳትነት ፡ አስደራጊና ፡ አዳራጊ ፡ ይመሠረታሉ ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ አስደራጊ ፡ ብቻ ፡ ይመሠረታል ።

ምሳሌ ፡-

| | | | |
|---|---|---|---|
| ጠነከረ ፡ | አጠነከረ ፡ | | |
| መጣ ፡ | አመጣ ፡ | አስመጣ ፡ | አማጣ ፡ |

ማስገንዘቢያ ፡- ከማይሻገር ፡ ዐምድ ፡ ላይ ፡ በባዕድ ፡ መነሻ ፡ አንድ ፡ ወይም ፡ ሁለት ፡ ግሶች ፡ ሊመሠረቱ ፡ እንደ ፡ ተቻለ ፡ አስተውል ።

ከተሻጋሪ ፡ ዐምድና ፡ ከማይሻገር ፡ ዐምድ ፡ ላይ ፡ አዳዲስ ፡ ግሶች ፡ በባዕድ ፡ መነሻ ፡ ረዳትነት ፡ ለመመሥረት ፡ መቻላቸውን ፡ ልጆች ፡ በደንብ ፡ እንዲያውቁት ፡ ማድረግ ፡ በጣም ፡ ትልቅ ፡ ነገር ፡ ነው። ምክንያቱም ፡ ለልጆች ፡ በቀላሉ ፡ ግልጽ ፡ ሆኖ፡ ሊታያቸው ፡ በመቻሉ ፡ ነው ።

አንድ ፡ አስተማሪ ፡ ማድረግ ፡ የሚገባው ፡ የሚያስተምረው ፡ አርእስት ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ንኡሳን ፡ ክፍሎች ፡ እየተከፈለ ፡ መሄዱንና ፡ የያንዳንዱን ፡ ንኡስ ፡ ክፍል ፡ መጣ

ለጫና ፡ ባረፍት ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ አገባቡን ፡ መለየት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አንዱን ፡ ትንሹን ፡ ንኡስ ፡ ክፍል ፡ እንዳንድ ፡ ትልቅ ፡ ክፍል ፡ አስመስሎ ፡ መድቦ ፡ ልጆቹን ፡ ማስቸገር ፡ አስፈላጊ ፡ አይደለም ፡ (አይገባም) ።

እንኳን ፡ ባንድ ፡ አርእስት ፡ ክፍል ፡ ውስጥ ፡ ያሉትንና ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ አርእስት ፡ ክፍል ፡ ያሉትንም ፡ ትምህርቶች ፡ ቢሆን ፡ የሚዛመዱበትን ፡ ዘዴ ፡ እየፈለጉ ፡ ማስተማር ፡ ይገባል ፤ እንዲያውም ፡ አንድ ፡ አስተማሪ ፡ ትናንትና ፡ ያስተማረውን ፡ ለዛሬ ፡ አዲስ ፡ ትምህርትን ፡ ከመጀመሩ ፡ በፊት ፡ በጥቂት ፡ ደቂቆች ፡ ውስጥ ፡ እንዲከልስላቸው ፡ ያስፈልጋል ።

ተሻጋሪ ፡ ዐምድ ፡ ዐቢይ ፡ አንቀጽና ፡ የማይሻገር ፡ ዐምድ ፡ ዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡ ከነውሉዳኑ ፡ ግሶቻቸው ፡ በ፫ ፡ መደቦች ፡ ተውላጣተ ፡ ስሞች ፡ ሲረቡ ፡

## ፩ኛ ፡ መደብ ፡ በተሻጋሪ ፡ ግስ ፡

ያልተወሰነ ፡ የዋህ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| | አስወቀርሁ ፡ | አወቃቀርሁ ፡ | አዋቀርሁ ፡ |
| ወቀርሁ ፡ | ተወቀርሁ ፡ | ተወቃቀርሁ ፡ | ተዋቀርሁ ፡ |
| | አስወቀርን ፡ | አወቃቀርን ፡ | አዋቀርን ፡ |
| ወቀርን ፡ | ተወቀርን ፡ | ተወቃቀርን ፡ | ተዋቀርን ፡ |

በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የተሠራውን ፡ ሥራ ፡ የሚያሳይ ፡ የቅርብ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| ወቅሪያለሁ ፡ | አስወቅሪያለሁ ፡ | አወቃቅሬያለሁ ፡ | አዋቅሪያለሁ ፡ |
| | ተወቅሪያለሁ ፡ | ተወቃቅሪያለሁ ፡ | ተዋቅሪያለሁ ፡ |
| ወቅረናል ፡ | አስወቅረናል ፡ | አወቃቅረናል ፡ | አዋቅረናል ፡ |
| | ተወቅረናል ፡ | ተወቃቅረናል ፡ | ተዋቅረናል ፡ |

በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የተሠራውን ፡ ሥራ ፡ የሚያሳይ ፡ የሩቅ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| ወቅሬ ፡ ነበር ፡ | አስወቅሬ ፡ ነበር ፡ | አወቃቅሬ ፡ ነበር ፡ | አዋቅሬ ፡ ነበር ፡ |
| | ተወቅሬ ፡ ነበር ፡ | ተወቃቅሬ ፡ ነበር ፡ | ተዋቅሬ ፡ ነበር ፡ |
| ወቅረን ፡ ነበር ፡ | አስወቅረን ፡ ነበር ፡ | አወቃቅረን ፡ ነበር ፡ | አዋቅረን ፡ ነበር ፡ |
| | ተወቅረን ፡ ነበር ፡ | ተወቃቅረን ፡ ነበር | ተዋቅረን ፡ ነበር ፡ |

ያልተወሰነ ፡ ያሁንና ፡ የትንቢት ፡ ጊዜያት ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| እወቅራለሁ ፡ | አስወቅራለሁ ፡ | አወቃቅራለሁ ፡ | አዋቅራለሁ ፡ |
| | እወቀራለሁ ፡ | እወቃቀራለሁ ፡ | እዋቀራለሁ ፡ |
| እንወቅራለን ፡ | እናስወቅራለን ፡ | እናወቃቅራለን ፡ | እናዋቅራለን ፡ |
| | እንወቀራለን ፡ | እንወቃቀራለን ፡ | እንዋቀራለን ፡ |

## በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የሚሠራውን ፡ የሚያሳይ ፡ የቅርብ ፡ ትንቢት ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| ልወቅር ፡ ነው ፡ | ላስወቅር ፡ ነው ፡ | ላወቃቅር ፡ ነው ፡ | ላዋቅር ፡ ነው ፡ |
| | ልወቀር ፡ ነው ፡ | ልወቃቀር፡ ነው ፡ | ልዋቀር ፡ ነው ፡ |
| ልንወቅር፡ ነው ፡ | ልናስወቅር፡ ነው፡ | ልናወቃቅር፡ነው፡ | ልናዋቅር ፡ ነው ፡ |
| | ልንወቀር ፡ ነው ፡ | ልንወቃቀር፡ነው፡ | ልንዋቀር ፡ ነው ፡ |

## ፭ኛ ፡ መደብ ፡ በማይሻገር ፡ ግስ ፡

### ያልተወሰነ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| መጣሁ ፡ | አመጣሁ ፡ | አስመጣሁ ፡ | ደነገጥሁ ፡ | አስደነገጥሁ ፡ |
| መጣን ፡ | አመጣን ፡ | አስመጣን ፡ | ደነገጥን ፡ | አስደነገጥን ፡ |

### በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የሚሠራውን ፡ የሚያሳይ ፡ የቅርብ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| መጥቻለሁ ፡ | አምጥቻለሁ ፡ | አስመጥቻለሁ ፡ | ደንግጫለሁ ፡ | አስደንግጫለሁ ፡ |
| መጥተናል ፡ | አምጥተናል ፡ | አስመጥተናል ፡ | ደንግጠናል ፡ | አስደንግጠናል ፡ |

### በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የሚሠራውን ፡ የሚያሳይ ፡ የሩቅ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| መጥቼ ፡ ነበር ፡ | አምጥቼ ፡ ነበር ፡ | አስመጥቼ፡ ነበር ፡ | ደንግጬ፡ ነበር ፡ | አስደንግጬ፡ነበር |
| መጥተን፡ነበር፡ | አምጥተን ፡ ነበር፡ | አስመጥተን፡ ነበር | ደንግጠን ፡ ነበር ፡ | አስደንግጠንነበር |

### ያልተወሰነ ፡ ያሁንና ፡ የትንቢት ፡ ጊዜያት ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| እመጣለሁ ፡ | አመጣለሁ ፡ | አስመጣለሁ ፡ | እደነግጣለሁ ፡ | አስደነግጣለሁ ፡ |
| እንመጣለን ፡ | እናመጣለን ፡ | እናስመጣለን ፡ | እንደነግጣለን ፡ | እናስደነግጣለን ፡ |

### በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የሚሠራውን ፡ የሚያሳይ ፡ የቅርብ ፡ ትንቢት ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| ልመጣ ፡ ነው ፡ | ላመጣ ፡ ነው ፡ | ላስመጣ ፡ ነው ፡ | ልደነግጥ ፡ ነው ፡ | ላስደነግጥ ፡ ነው ፡ |
| ልንመጣ፡ነው፡ | ልናመጣ ፡ ነው ፡ | ልናስመጣ ፡ ነው፡ | ልንደነግጥ፡ ነው ፡ | ልናስደነግጥ፡ ነው |

## ፮ኛ ፡ መደብ ፡ በተሻጋሪ ፡ ግስ ፡

### ያልተወሰነ ፡ የዋህ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| ወቀርህ ፡ | አስወቀርህ ፡ | አወቃቀርህ ፡ | አዋቀርህ ፡ |
| | ተወቀርህ ፡ | ተወቃቀርህ ፡ | ተዋቀርህ ፡ |
| ወቀርሽ ፡ | አስወቀርሽ ፡ | አወቃቀርሽ ፡ | አዋቀርሽ ፡ |
| | ተወቀርሽ ፡ | ተወቃቀርሽ ፡ | ተዋቀርሽ ፡ |
| ወቀራችሁ ፡ | አስወቀራችሁ ፡ | አወቃቀራችሁ ፡ | አዋቀራችሁ ፡ |

| | | | |
|---|---|---|---|
| ወቀሩ ፡ | ተወቀራችሁ ፡<br>አስወቀሩ ፡<br>ተወቀሩ ፡ | ተወቃቀራችሁ ፡<br>አወቃቀሩ ፡<br>ተወቃቀሩ ፡ | ተዋቀራችሁ ፡<br>አዋቀሩ ፡<br>ተዋቀሩ ፡ |

**በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የተሠራውን ፡ ሥራ ፡ የሚያሳይ ፡ የቅርብ ፡ ኀላፊ ፡**

| | | | |
|---|---|---|---|
| ወቅረሃል ፡ | አስወቅረሃል ፡<br>ተወቅረሃል ፡ | አወቃቅረሃል ፡<br>ተወቃቅረሃል ፡ | አዋቅረሃል ፡<br>ተዋቅረሃል ፡ |
| ወቅረሻል ፡ | አስወቅረሻል ፡<br>ተወቅረሻል ፡ | አወቃቅረሻል ፡<br>ተወቃቅረሻል ፡ | አዋቅረሻል ፡<br>ተዋቅረሻል ፡ |
| ወቅራችኋል ፡ | አስወቅራችኋል ፡<br>ተወቅራችኋል ፡ | አወቃቅራችኋል ፡<br>ተወቃቅራችኋል ፡ | አዋቅራችኋል ፡<br>ተዋቅራችኋል ፡ |
| ወቅረዋል ፡ | አስወቅረዋል ፡<br>ተወቅረዋል ፡ | አወቃቅረዋል ፡<br>ተወቃቅረዋል ፡ | አዋቅረዋል ፡<br>ተዋቅረዋል ፡ |

**በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የተሠራውን ፡ ሥራ ፡ የሚያሳይ ፡ የሩቅ ፡ ኀላፊ ፡**

| | | | |
|---|---|---|---|
| ወቅረህ ፡ ነበር ፡ | አስወቅረህ፡ ነበር ፡<br>ተወቅረህ ፡ ነበር ፡ | አወቃቅረህ፡ ነበር፡<br>ተወቃቅረህ፡ ነበር ፡ | አዋቅረህ ፡ ነበር ፡<br>ተዋቅረህ፡ ነበር ፡ |
| ወቅረሽ ፡ ነበር ፡ | አስወቅረሽ ፡ ነበር ፡<br>ተወቅረሽ ፡ ነበር ፡ | አወቃቅረሽ ፡ ነበር ፡<br>ተወቃቅረሽ ፡ ነበር ፡ | አዋቅረሽ ፡ ነበር ፡<br>ተዋቅረሽ ፡ ነበር ፡ |
| ወቅራችሁ ፡ ነበር ፡ | አስወቅራችሁ፡ነበር፡<br>ተወቅራችሁ ፡ ነበር፡ | አወቃቅራችሁ ፡ ነበር ፡<br>ተወቃቅራችሁ፡ ነበር ፡ | አዋቅራችሁ ፡ ነበር፡<br>ተዋቅራችሁ፡ ነበር፡ |
| ወቅረው ፡ ነበር ፡ | አስወቅረው ፡ ነበር፡<br>ተወቅረው ፡ ነበር ፡ | አወቃቅረው ፡ ነበር ፡<br>ተወቃቅረው ፡ ነበር ፡ | አዋቅረው ፡ ነበር ፡<br>ተዋቅረው ፡ ነበር ፡ |

**ያልተወሰነ ፡ ያሁንና ፡ የትንቢት ፡ ጊዜያት ፡**

| | | | |
|---|---|---|---|
| ትወቅራለህ ፡ | ታስወቅራለህ ፡<br>ትወቀራለህ ፡ | ታወቃቅራለህ ፡<br>ትወቃቀራለህ ፡ | ታዋቅራለህ ፡<br>ትዋቀራለህ ፡ |
| ትወቅሪያለሽ ፡ | ታስወቅሪያለሽ ፡<br>ትወቀሪያለሽ ፡ | ታወቃቅሪያለሽ ፡<br>ትወቃቀሪያለሽ ፡ | ታዋቅሪያለሽ ፡<br>ትዋቀሪያለሽ ፡ |
| ትወቅራላችሁ ፡ | ታስወቅራላችሁ ፡<br>ትወቀራላችሁ ፡ | ታወቃቅራላችሁ ፡<br>ትወቃቀራላችሁ ፡ | ታዋቅራላችሁ ፡<br>ትዋቀራላችሁ ፡ |
| ይወቅራሉ ፡ | ያስወቅራሉ ፡<br>ይወቀራሉ ፡ | ያወቃቅራሉ ፡<br>ይወቃቀራሉ ፡ | ያዋቅራሉ ፡<br>ይዋቀራሉ ፡ |

**በቅርብ ፡ ጊዜ፡ የሚሠራውን ፡ የሚያሳይ ፡ የቅርብ፡ ትንቢት ፡**

| | | | |
|---|---|---|---|
| ልትወቅር ፡ ነው ፡ | ልታስወቅር ፡ ነው ፡<br>ልትወቀር ፡ ነው ፡ | ልታወቃቅር ፡ ነው ፡<br>ልትወቃቀር ፡ ነው ፡ | ልታዋቅር ፡ ነው ፡<br>ልትዋቀር ፡ ነው ፡ |
| ልትወቅሪ ፡ነው ፡ | ልታስወቅሪ ፡ ነው ፡<br>ልትወቀሪ ፡ ነው፡ | ልታወቃቀሪ ፡ ነው ፡<br>ልትወቃቀሪ ፡ ነው ፡ | ልታዋቅሪ ፡ ነው ፡<br>ልትዋቀሪ ፡ ነው ፡ |

| | | | |
|---|---|---|---|
| ልትወቅሩ ፡ ነው ፡ | ል ታስወቅሩ ፡ ነው ፡ | ል ታወቃቅሩ ፡ ነው ፡ | ል ታዋቅሩ ፡ ነው ፡ |
| | ልትወቀሩ ፡ ነው ፡ | ልትወቃቀሩ ፡ ነው ፡ | ልትዋቀሩ ፡ ነው ፡ |
| ሊወቅሩ ፡ ነው ፡ | ሊያስወቅሩ ፡ ነው ፡ | ሊያወቃቅሩ ፡ ነው ፡ | ሊያዋቅሩ ፡ ነው ፡ |
| | ሊወቀሩ ፡ ነው ፡ | ሊወቃቀሩ ፡ ነው ፡ | ሊዋቀሩ ፡ ነው ፡ |

## ፪ኛ ፡ መደብ ፡ በማይሻገር ፡ ግስ ፡

### ያልተወሰነ ፡ የዋህ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| መጣህ ፡ | አመጣህ ፡ | አስመጣህ ፡ | ደነገጥህ ፡ | አስደነገጥህ ፡ |
| መጣሽ ፡ | አመጣሽ ፡ | አስመጣሽ ፡ | ደነገጥሽ ፡ | አስደነገጥሽ ፡ |
| መጣችሁ ፡ | አመጣችሁ ፡ | አስመጣችሁ ፡ | ደነገጣችሁ ፡ | አስደነገጣችሁ |
| መጡ ፡ | አመጡ ፡ | አስመጡ ፡ | ደነገጡ ፡ | አስደነገጡ ፡ |

በሁለተኛው ፡ መደብ ፡ የግስ ፡ ርባታ ፡ ባራተኛው ፡ መሥመር ፡ ላይ ፡ በሦስተኛው ፡ መደብ ፡ በብዙ ፡ ቍጥር ፡ የተረባው ፡ ለሁለተኛው ፡ መደብ ፡ ለነጠላው ፡ ቍጥር ፡ ባክብሮት ፡ ረገድ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አስተውል ።

### በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የተሠራውን ፡ የሚያሳይ ፡ የቅርብ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| መጥተሃል ፡ | አምጥተሃል ፡ | አስመጥተሃል ፡ | ደንግጠሃል ፡ | አስደንግጠሃል ፡ |
| መጥተሻል ፡ | አምጥችሻል ፡ | አስመጥተሻል ፡ | ደንግጠሻል ፡ | አስደንግጠሻል ፡ |
| መጥታችኋል ፡ | አምጥታችኋል ፡ | አስመጥታችኋል ፡ | ደንግጣችኋል ፡ | አስደንግጣችኋል ፡ |
| መጥተዋል ፡ | አምጥተዋል ፡ | አስመጥተዋል ፡ | ደንግጠዋል ፡ | አስደንግጠዋል ፡ |

### በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የተሠራውን ፡ የሚያሳይ ፡ የሩቅ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| መጥተህ ፡ ነበር ፡ | አምጥተህ ፡ ነበር ፡ | አስመጥተህ ፡ ነበር ፡ | ደንግጠህ ፡ ነበር ፡ | አስደንግጠህ ፡ ነበር ፡ |
| መጥተሽ ፡ ነበር ፡ | አምጥተሽ ፡ ነበር ፡ | አስመጥተሽ ፡ ነበር ፡ | ደንግጠሽ ፡ ነበር ፡ | አስደንግጠሽ ፡ ነበር ፡ |
| መጥታችሁ ፡ ነበር ፡ | አምጥታችሁ ፡ ነበር ፡ | አስመጥታችሁ ፡ ነበር ፡ | ደንግጣችሁ ፡ ነበር ፡ | አስደንግጣችሁ ፡ ነበር ፡ |
| መጥተው ፡ ነበር ፡ | አምጥተው ፡ ነበር ፡ | አስመጥተው ፡ ነበር ፡ | ደንግጠው ፡ ነበር ፡ | አስደንግጠው ፡ ነበር ፡ |

### ያልተወሰነ ፡ ያሁንና ፡ የትንቢት ፡ ጊዜያት ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| ትመጣለህ ፡ | ታመጣለህ ፡ | ታስመጣለህ ፡ | ትደነግጣለህ ፡ | ታስደነግጣለህ ፡ |
| ትመጪለሽ ፡ | ታመጪለሽ ፡ | ታስመጪለሽ ፡ | ትደነግጪለሽ ፡ | ታስደነግጪለሽ ፡ |
| ትመጣላችሁ ፡ | ታመጣላችሁ ፡ | ታስመጣላችሁ ፡ | ትደነግጣላችሁ ፡ | ታስደነግጣላችሁ ፡ |
| ይመጣሉ ፡ | ያመጣሉ ፡ | ያስመጣሉ ፡ | ይደነግጣሉ ፡ | ያስደነግጣሉ ፡ |

### በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የተሠራውን ፡ የሚያሳይ ፡ የቅርብ ፡ ትንቢት ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| ልትመጣ ፡ ነው ፡ | ልታመጣ ፡ ነው ፡ | ልታስመጣ ፡ ነው ፡ | ልትደነግጥ ፡ ነው ፡ | ልታስደነግጥ ፡ ነው ፡ |
| ልትመጪ ፡ ነው ፡ | ልታመጪ ፡ ነው ፡ | ልታስመጪ ፡ ነው ፡ | ልትደነግጪ ፡ ነው ፡ | ልታስደነግጪ ፡ ነው ፡ |
| ልትመጡ ፡ ነው ፡ | ልታመጡ ፡ ነው ፡ | ልታስመጡ ፡ ነው ፡ | ልትደነግጡ ፡ ነው ፡ | ልታስደነግጡ ፡ ነው ፡ |
| ሊመጡ ፡ ነው ፡ | ሊያመጡ ፡ ነው ፡ | ሊያስመጡ ፡ ነው ፡ | ሊደነግጡ ፡ ነው ፡ | ሊያስደነግጡ ፡ ነው ፡ |

## ፫ኛ ፡ መደብ ፡ በተሻጋሪ ፡ ግስ ፡

### ያልተወሰነ ፡ የዋህ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| ወቀረ ፡ | አስወቀረ ፡ | አወቃቀረ ፡ | አዋቀረ ፡ |
| | ተወቀረ ፡ | ተወቃቀረ ፡ | ተዋቀረ ፡ |
| ወቀረች ፡ | አስወቀረች ፡ | አወቃቀረች ፡ | አዋቀረች ፡ |
| | ተወቀረች ፡ | ተወቃቀረች ፡ | ተዋቀረች ፡ |
| ወቀሩ ፡ | አስወቀሩ ፡ | አወቃቀሩ ፡ | አዋቀሩ ፡ |
| | ተወቀሩ ፡ | ተወቃቀሩ ፡ | ተዋቀሩ ፡ |

### በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የተሠራውን ፡ የሚያሳይ፡ የቅርብ፡ ኀላፊ ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| ወቅሯል ፡ | አስወቅሯል ፡ | አወቃቅሯል ፡ | አዋቅሯል ፡ |
| | ተወቅሯል ፡ | ተወቃቅሯል ፡ | ተዋቅሯል ፡ |
| ወቅራለች ፡ | አስወቅራለች ፡ | አወቃቅራለች ፡ | አዋቅራለች ፡ |
| | ተወቅራለች ፡ | ተወቃቅራለች ፡ | ተዋቅራለች ፡ |
| ወቅረዋል ፡ | አስወቅረዋል ፡ | አወቃቅረዋል ፡ | አዋቅረዋል ፡ |
| | ተወቅረዋል ፡ | ተወቃቅረዋል ፡ | ተዋቅረዋል ፡ |

### በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የተሠራውን ፡ የሚያሳይ ፡ የሩቅ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| ወቅሮ ፡ ነበር ፡ | አስወቅሮ፡ ነበር ፡ | አወቃቅሮ፡ ነበር ፡ | አዋቅሮ ፡ ነበር ፡ |
| | ተወቅሮ ፡ ነበር ፡ | ተወቃቅሮ ፡ ነበር ፡ | ተዋቅሮ ፡ ነበር ፡ |
| ወቅራ ፡ ነበር ፡ | አስወቅራ፡ ነበር ፡ | አወቃቅራ፡ ነበር ፡ | አዋቅራ ፡ ነበር ፡ |
| | ተወቅራ ፡ ነበር ፡ | ተወቃቅራ፡ ነበር ፡ | ተዋቅራ ፡ ነበር ፡ |
| ወቅረው፡ ነበር ፡ | አስወቅረው ፡ ነበር ፡ | አወቃቅረው ፡ ነበር ፡ | አዋቅረው ፡ ነበር ፡ |
| | ተወቅረው ፡ ነበር ፡ | ተወቃቅረው፡ ነበር ፡ | ተዋቅረው፡ ነበር ፡ |

### ያልተወሰነ ፡ ያሁንና ፡ የትንቢት ፡ ጊዚያት ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| ይወቅራል ፡ | ያስወቅራል ፡ | ያወቃቅራል ፡ | ያዋቅራል ፡ |
| | ይወቀራል ፡ | ይወቃቀራል ፡ | ይዋቀራል ፡ |
| ትወቅራለች ፡ | ታስወቅራለች ፡ | ታወቃቅራለች ፡ | ታዋቅራለች ፡ |
| | ትወቀራለች ፡ | ትወቃቀራለች ፡ | ትዋቀራለች ፡ |
| ይወቅራሉ ፡ | ያስወቅራሉ ፡ | ያወቃቅራሉ ፡ | ያዋቅራሉ ፡ |
| | ይወቀራሉ ፡ | ይወቃቀራሉ ፡ | ይዋቀራሉ ፡ |

## በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የሚሠራውን ፡ የሚያሳይ ፡ የቅርብ ፡ ትንቢት ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| ሊወቅር ፡ ነው ፡ | ሊያስወቅር ፡ ነው ፡ | ሊያወቃቅር ፡ ነው ፡ | ሊያዋቅር ፡ ነው ፡ |
| | ሊወቀር ፡ ነው ፡ | ሊወቃቀር ፡ ነው ፡ | ሊዋቀር ፡ ነው ፡ |
| ልትወቅር ፡ ነው ፡ | ልታስወቅር ፡ ነው ፡ | ልታወቃቅር ፡ ነው ፡ | ልታዋቅር ፡ ነው ፡ |
| | ልትወቀር ፡ ነው ፡ | ልትወቃቀር ፡ ነው ፡ | ልትዋቀር ፡ ነው ፡ |
| ሊወቅሩ ፡ ነው ፡ | ሊያስወቅሩ ፡ ነው ፡ | ሊያወቃቅሩ ፡ ነው ፡ | ሊያዋቅሩ ፡ ነው ፡ |
| | ሊወቀሩ ፡ ነው ፡ | ሊወቃቀሩ ፡ ነው ፡ | ሊዋቀሩ ፡ ነው ፡ |

## ፫ኛ ፡ መደብ ፡ በማይሻገር ፡ ግስ ፡

### ያልተወሰነ ፡ የዋህ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| መጣ ፡ | አመጣ ፡ | አስመጣ ፡ | ደነገጠ ፡ | አስደነገጠ ፡ |
| መጣች ፡ | አመጣች ፡ | አስመጣች ፡ | ደነገጠች ፡ | አስደነገጠች ፡ |
| መጡ ፡ | አመጡ ፡ | አስመጡ ፡ | ደነገጡ ፡ | አስደነገጡ ፡ |

### በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የተሠራውን ፡ የሚያሳይ ፡ የቅርብ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| መጥቷል ፡ | አምጥቷል ፡ | አስመጥቷል ፡ | ደንግጧል ፡ | አስደንግጧል ፡ |
| መጥታለች ፡ | አምጥታለች ፡ | አስመጥታለች ፡ | ደንግጣለች ፡ | አስደንግጣለች ፡ |
| መጥተዋል ፡ | አምጥተዋል ፡ | አስመጥተዋል ፡ | ደንግጠዋል ፡ | አስደንግጠዋል ፡ |

### በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የተሠራውን ፡ ሥራ ፡ የሚያሳይ ፡ የሩቅ ፡ ኀላፊ ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| መጥቶ ፡ ነበር ፡ | አምጥቶ ፡ ነበር ፡ | አስመጥቶ ፡ ነበር ፡ | ደንግጦ ፡ ነበር ፡ | አስደንግጦ ፡ ነበር ፡ |
| መጥታ ፡ ነበር ፡ | አምጥታ ፡ ነበር ፡ | አስመጥታ ፡ ነበር ፡ | ደንግጣ ፡ ነበር ፡ | አስደንግጣ ፡ ነበር ፡ |
| መጥተው ፡ ነበር ፡ | አምጥተው ፡ ነበር ፡ | አስመጥተው ፡ ነበር ፡ | ደንግጠው ፡ ነበር ፡ | አስደንግጠው ፡ ነበር ፡ |

### ያልተወሰነ ፡ ያሁንና ፡ የትንቢት ፡ ጊዜያት ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| ይመጣል ፡ | ያመጣል ፡ | ያስመጣል ፡ | ይደነግጣል ፡ | ያስደነግጣል ፡ |
| ትመጣለች ፡ | ታመጣለች ፡ | ታስመጣለች ፡ | ትደነግጣለች ፡ | ታስደነግጣለች ፡ |
| ይመጣሉ ፡ | ያመጣሉ ፡ | ያስመጣሉ ፡ | ይደነግጣሉ ፡ | ያስደነግጣሉ ፡ |

### በተወሰነ ፡ ሰዓት ፡ የሚሠራውን ፡ የሚያሳይ ፡ የቅርብ ፡ ትንቢት ፡

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| ሊመጣ ፡ ነው ፡ | ሊያመጣ ፡ ነው ፡ | ሊያስመጣ ፡ ነው ፡ | ሊደነግጥ ፡ ነው ፡ | ሊያስደነግጥ ፡ ነው ፡ |
| ልትመጣ ፡ ነው ፡ | ልታመጣ ፡ ነው ፡ | ልታስመጣ ፡ ነው ፡ | ልትደነግጥ ፡ ነው ፡ | ልታስደነግጥ ፡ ነው ፡ |
| ሊመጡ ፡ ነው ፡ | ሊያመጡ ፡ ነው ፡ | ሊያስመጡ ፡ ነው ፡ | ሊደነግጡ ፡ ነው ፡ | ሊያስደነግጡ ፡ ነው ፡ |

የማያቋርጥ ፡ ግስ ፡

በስምንቱ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ የሚረባ ፡ ኀላፊ ፡ የማያቋርጥ ፡ ግስ ፡ አለ ።

አስረጅ ፦ ከዚህ ፡ በፊት ፡ በድሬ ፡ ዳዋ ፡ ይኖር ፡ ነበር፤ አሁን ፡ ግን ፡ በሐረር ፡ ከተማ፡ ይኖራል ።

ከዚህ ፡ በላይ ፡ በተነገረው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ የምናገኘው ፡ ስሜት ፡ ሰውዬው ፡ ያለማቋረጥ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ በድሬ ፡ ዳዋ ፡ ተቀምጦ ፡ ወደ ፡ ሐረር ፡ ተዛውሮ ፡ መቀመጡን ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ በዚህ ፡ መንገድ ፡ የሚሠሩትን፡ ግሶች ፡ ባዋዋይ ፡ አንቀጽ፡ ውስጥ ፡ መጻፍ ፡ አያስፈልግም ፡ አንድ ፡ ተሻጋሪ ፡ ግስ ፡ ባለቤቱንም ፡ ተሳቢውንም ፡ ይዞ ፡ ሲገኝ ፡ ዝርዝር ፡ ርባታ ፡ ይባላል ።

፩ኛ ፡ መደብ ።

| ነጠላ ፡ (አድራጊ) ፡ | | አክብሮት ፡ | |
|---|---|---|---|
| መከርሁህ ፡ | መከርሁሽ ፡ | መከርሁዎ ፡ | መከርኋችሁ ፡ |
| መከርሁት ፡ | መከርኋት ፡ | መከርኋቸው ፡ | መከርኋቸው ፡ |
| ብዙ ፡ (አድራጊ) ፡ | | | |
| መከርንህ ፡ | መከርንሽ ፡ | መከርንዎ ፡ | መከርናችሁ ፡ |
| መከርነው ፡ | መከርናት ፡ | መከርናቸው ፡ | መከርናቸው ፡ |

፪ኛ ፡ መደብ ።

| ነጠላ ፡ (አድራጊ) ፡ ተባዕታይ ፡ | | አክብሮት ፡ | |
|---|---|---|---|
| መከርኸኝ ፡ | መከርኸን ፡ | | |
| መከርኸው ፡ | መከርሃት ፡ | መከርሃቸው ፡ | መከርሃቸው ፡ |
| ነጠላ ፡ (አድራጊ) ፡ ሴቴ ፡ | | | |
| መከርሽኝ ፡ | መከርሽን ፡ | | |
| መከርሽው ፡ | መከርሻት ፡ | መከርሻቸው ፡ | መከርሻቸው ፡ |
| ብዙ ፡ (አድራጊ) ፡ | | | |
| መከራችሁኝ ፡ | መከራችሁን ፡ | | |
| መከራችሁት ፡ | መከራችኋት ፡ | መከራችኋቸው ፡ | መከራችኋቸው ፡ |
| መከሩት፡ | መከሯት ፡ | መከሯቸው ፡ | መከሯቸው ፡ |

፫ኛ ፡ መደብ ።

ነጠላ ፡ (አድራጊ) ፡ ወንዴ ፡

መከረኝ ፡ መከረን ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| መከረህ ፡ | መከረሽ ፡ | መከረዎ ፡ | መከራችሁ ፡ |
| መከረው ፡ | መከራት ፡ | መከራቸው ፡ | መከራቸው ፡ |

ነጠላ ፡ (አድራጊ) ፡ አንስታይ ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| መከረችኝ፡ | መከረችን ፡ | | |
| መከረችህ ፡ | መከረችሽ ፡ | መከረችዎ ፡ | መከረቻችሁ ፡ |
| መከረችው ፡ | መከረቻት ፡ | መከረቻቸው ፡ | መከረቻቸው ፡ |

ብዙ ፡ (አድራጊ) ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| መከሩኝ ፡ | መከሩን ፡ | | |
| መከሩህ ፡ | መከሩሽ ፡ | መከሩዎ ፡ | መከሯችሁ ፡ |
| መከሩት ፡ | መከሯት ፡ | መከሯቸው ፡ | መከሯቸው ፡ |

## ፫ ፡ ትእዛዝ ፡ አንቀጽ ።

ትእዛዝ ፡ አንቀጽ ፡ ባሁንና ፡ በትንቢት ፡ ጊዜያት ፡ ይነገራል ። ቀጥተኛው ፡ ትእዛዝ ፡ የሚሰጠው ፡ በ፪ኛ ፡ መደብ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ በተዘዋዋሪ ፡ መንገድ ፡ ግን ፡ ባ፩ኛና ፡ በ፫ኛ ፡ መደብ ፡ ይነገራል ፤ ኢ.ርቱዕ ፡ ትእዛዝ ፡ ቢ.ባል ፡ የሚያስነውር ፡ ወይም ፡ የሚያስነቅፍ ፡ አይደለም ።

## ትእዛዝ አንቀጽ ።

| ፩ኛ ፡ መደብ ። | ፪ኛ ፡ መደብ ። | ፫ኛ ፡ መደብ ። |
|---|---|---|
| ነጠላ ፡ | ነጠላ ፡ | ነጠላ ፡ |
| ልሞክር ፡ | ሞክር ፡ | ይሞክር ፡ |
| | ሞክሪ ፡ | ትሞክር ፡ |
| እንድሞክር ፡ ይሁን ፡ | እንድትሞክር ፡ ይሁን ፡ | እንዲሞክር፡ ይሁን ፡ |
| | እንድትሞክሪ ፡ ይሁን ፡ | እንድትሞክር ፡ ይሁን ፡ |
| ብዙ ፡ | ብዙ ፡ | ብዙ ፡ |
| እንሞክር ፡ | ሞክሩ ፡ | ይሞክሩ ፡ |
| እንድንሞክር ፡ ይሁን ፡ | እንድትሞክሩ ፡ ይሁን ፡ | እንዲሞክሩ ፡ ይሁን ። |

## ፬ ፡ አዋዋይ ፡ አንቀጽ ።

አዋዋይ ፡ አንቀጽ ፡ የተባለበት ፡ አንቀጹ ፡ ከጥገኛው ፡ መስተፃምር ፡ ጋራ ፡ ባንድነት ፡ ስለሚገባ ፡ ነው ። ከጥገኛው ፡ መስተፃምር ፡ ጋራ ፡ የሚረባው ፡ ግስ ፡ በመጣ ፡ ነበር ፤ በተቀመጠ ፡ ነበር ፤ በተነገረ ፡ ነበር ፡ ከሚባሉት ፡ ዐይነቶች ፡ በስተቀር ፡ ለመደበኛው ፡ ሐረግ ፡ ተጨማሪ ፡ ሆኖ ፡ ይገባል ፡ እንጂ ፤ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡ አይሆንም ።

**ማስገንዘቢያ ፡**

አዋዋይ ፡ አንቀጽ ፡ ማሰሪያ ፡ ይሆናል ፡ የምንለው ፡ በመጣ ፡ ነበር ፡ በተቀመጠ ፡ ነበር ፡ በተናገረ ፡ ነበር ፡ እየተባሉ ፡ የሚረቡት ፡ ግሶች ፡ ለማሰር ፡ መቻላቸውን ፡ በመመልከት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አስተውል ።

## የአዋዋይ ፡ አንቀጽ ፡ አረባብ ፡

| ፩ኛ ፡ መደብ ። | ፪ኛ ፡ መደብ ። ( ተባዕታይ ) ፡ | አንስታይ ፡ |
|---|---|---|
| **ነጠላ ፡** | **ነጠላ ፡** | **ነጠላ ፡** |
| ብሞክር፡ኖሮ፡ያለጥርጥር፡ አልፈው፡ነበር ። | ብትሞክር ፡ ኖሮ ፡ | ብትሞክሪ ፡ ኖሮ ፡ |
| ሞክሬ ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ ባለፍሁት ፡ ነበር ። | ሞክረህ፡ ቢሆን፡ኖሮ፡ | ሞክረሽ፡ ቢሆን፡ኖሮ፡ |
| ብሞክር ፡ አልፈዋለሁ ። | ብትሞክር ፡ | ብትሞክሪ ፡ |
| እንድሞክር ፡ አልተፈቀደልኝም ። | እንድትሞክር ፡ | እንድትሞክሪ ፡ |
| ልሞክር ፡ አልተፈቀደልኝም ። | ልትሞክር ፡ | ልትሞክሪ ፡ |
| እሞክር ፡ ዘንድ ፡ አልተፈቀደልኝም ። | ትሞክር ፡ ዘንድ ፡ | ትሞክሪ ፡ ዘንድ ፡ |
| በሞከርሁ ፡ ነበር ። | በሞከርህ ፡ ነበር ፡ | በሞከርሽ ፡ ነበር ፡ |
| **ብዙ ፡** | **አክብሮት ፡** | **ብዙ ፡** |
| ብንሞክር ፡ ኖሮ ፡ እናልፈው ፡ ነበር ። | ቢሞክሩ ፡ ኖሮ ፡ | ብትሞክሩ ፡ ኖሮ ፡ |
| ሞክረን ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ፡ ባለፍነው ፡ ነበር ። | ሞክረው፡ቢሆን፡ኖሮ | ሞክራችሁቢሆንኖሮ |
| ብንሞክር ፡ እናልፈዋለን ። | ቢሞክሩ ፡ | ብትሞክሩ ፡ |
| እንድንሞክር ፡ አልተፈቀደልንም ። | እንዲሞክሩ ፡ | እንድትሞክሩ ፡ |
| ልንሞክር ፡ አልተፈቀደልንም ። | ሊሞክሩ ፡ | ትሞክሩ ፡ |
| እንሞክር ፡ ዘንድ ፡ | ይሞክሩ ፡ ዘንድ ፡ | ትሞክሩ ፡ ዘንድ ፡ |
| በሞከርን ፡ ነበር ። | በሞከሩ ፡ ነበር ። | በሞከራችሁ፡ ነበር ። |

## ፫ኛ ፡ መደብ ።

| | | |
|---|---|---|
| ቢሞክር ፡ ኖሮ ፡ | ብትሞክር ፡ ኖሮ ፡ | ቢሞክሩ ፡ ኖሮ፡ |
| ሞክሮ ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ | ሞክራ፡ ቢሆን፡ ኖሮ ፡ | ሞክረው፡ቢሆን፡ኖሮ |
| ቢሞክር ፡ | ብትሞክር ፡ | ቢሞክሩ ፡ |
| እንዲሞክር ፡ | እንድትሞክር ፡ | እንዲሞክሩ ፡ |
| ሊሞክር ፡ | ልትሞክር ፡ | ሊሞክሩ ፡ |
| ይሞክር ፡ ዘንድ ፡ | ትሞክር ፡ ዘንድ ፡ | ይሞክሩ ፡ ዘንድ ፡ |
| በሞከረ ፡ ነበር ። | በሞከረች ፡ ነበር ። | በሞከሩ ፡ ነበር ። |

**የአረፍተ ፡ ነገር ፡ አመዳደብ ፡**

ግስ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ስልቶች ፡ እንዳሉት ፡ ከዚህ ፡ በፊት ፡ ጽፌና ፡ ገልጬ ፡ ማስረጃም ፡ ጭምር ፡ ሰጥቼ ፡ አስረድቻለሁ ። እያንዳንዱም ፡ ስልት ፡ አገላለጽ ፡ ስላለው ፡ በዚህ ፡ አካሄድ ፡ የአረፍተ ፡ ነገር ፡ ስልት ፡ ተብሎ ፡ ተመድቧል ።

፩ ፤ ሐተታዊ ፡ አረፍተ፡ ነገር ፡
፪ ፤ ትእዛዛዊ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡
፫ ፤ አጋናኝ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡
፬ ፤ ጥያቄያዊ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡

አስረጅ ፡-

ሐተታዊ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡

1 ሁል ፡ ጊዜ ፡ ወገኔ ፡ የሚሠለጥንበትን ፡ ዘዴ ፡ መፈለግ ፡አለብኝ ።
2 ለሰው ፡ ልጅ ፡ መወለድ ፡ ግድ ፡ የተፈጥሮ ፡ ልምዱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፣ እንዲሁም ፡ መሞት ፡ የተፈጥሮ ፡ ልምዱ ፡ ነው ።

3 ሐሰት ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትደፍራለች ፤ ሰውን ፡ ግን ፡ ትፈራለች ።
4 የእውነት ፡ ውጤቱ ፡ ሐሰት ፡ የሆነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እውነት ፡ መጽናናትን ፡ ልትሰጥ ፡ አለመቻሏን ፡ መገንዘብ ፡ ይገባናል ።

ትእዛዛዊ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡

1 የሰጠሁህን ፡ መጽሐፍ ፡ አምጣ ።
2 ነገ ፡ ልብሳችሁን ፡ ተኰሳችሁ ፡ እንድትመጡ ፡ ይሁን ።
3 ከበደን ፡ ካለበት ፡ ፈልገህ ፡ አሁኑኑ ፡ ጥራው ።
4 ለነገ ፡ ይህን ፡ ዕቃ ፡ ይዘህ ፡ እንድትመጣ ፡ ይሁን ።

አጋናኝ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ።

1 ይገርማል ! ይህን ፡ የመሰለ ፡ ብርዕ ፡ ማን ፡ ይሰጣል !
2 እፎይ ! ገና ፡ አሁን ፡ ትንሽ ፡ ሻል ፡ አለኝ ።
3 እሰይ ! ዝናሙ ፡ ከወደ ፡ ጋራው ፡ በኩል ፡ መጣ ።
4 እኔ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ አልወድም !

ጥያቄያዊ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡

1 አቶ ፡ አየለ ፡ ከወዴት ፡ ትመጣለህ ?
2 ይህንን ፡ ኮት ፡ ማን ፡ አሰፋልህ ?
3 ወደ ፡ አባትህ ፡ ዘንድ ፡ ልውሰድህ ፡ ወይ ?
4 ዛሬ ፡ ልብስህን ፡ ታጥባለህ ፡ ወይ ?

፲ ፡ ንኡስ ፡ አንቀጽ ፡

ንኡስ ፡ አንቀጽ ፡ የግስ ፡ አነስተኛ ፡ ወይም ፡ ዝቅተኛ ፡ ክፍል ፡ ነው ። ንኡስ ፡ አንቀጽ ፡ እንደ ፡ ሌሎቹ ፡ የግስ ፡ ስልቶች ፡ ለማሰር ፡ አይችልም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በውስጡ ፡ ቦዝ ፡ አንቀጽ ፡ የሚባለው ፡ ግስ ፡ ከሌሎቹ ፡ ረዳት ፡ ግሶች ፡ ጋራ ፡ እየገባ ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡ ይሆናል ። ንኡስ ፡ አንቀጽ ፡ ባምስት ፡ ክፍል ፡ ይከፈላል ።

፩ ፡ ቦዝ ፡ ፪ ፡ አርእስት ፡ ፫ ፡ ግሳዊ ፡ ቅጽል ፡ ፬ ፡ ሳቢ ፡ ዘር ፡ ፭ ፡ ጥሬ ፡ ዘር ፡

ቦዝ ፡ ለማሰር ፡ የማይችል ፡ ፍጉዝ ፡ ግስ ፡ ነው ። በቦዝ ፡ አንቀጽ ፡ ላይ ፡ ረዳት ፡ ግስ ፡ እየተጨመረ ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡ እንደሚሆን ፡ ስለ ፡ ረዳት ፡ ግሶች ፡ በተጻፈው ፡ ላይ ፡ ተገልጿል ።

ባቢይ ፡ አንቀጽ ፡ ክፍል ፡ የቅርብ ፡ ኀላፊንና ፡ የሩቅ ፡ ኀላፊን ፡ ለማግኘት፡ በኀላፊ፡ ቦዝ ፡ ላይ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ረዳት ፡ ግሶች ፡ እንጨምራለን ፤ እንደዚሁም ፡ የአሁንና ፡ የትንቢት ፡ ጊዜያትን ፡ ለማግኘት ፡ በትንቢታዊ ፡ ቦዝ ፡ ላይ ፡ ረዳት ፡ ግስን ፡ እንጨምራለን ።

ግስን ፡ አርብተን ፡ በቀጥታ ፡ ቦዝን ፡ ለማግኘት ፡ አንችልም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የየቀሁን ፡ ኀላፊ ፡ ግስ ፡ መድረሻ ፡ በልዩ ፡ ዐቅድ ፡ እየለወጥን ፡ ያረባነው ፡ እንደሆን ፡ ቦዝን ፡ ለማግኘት ፡ እንችላለን ።

አስረጅ ፡

ኀላፊ ፡ ጊዜያት ፡

| ፩ኛ ፡ መደብ ፡ | ፪ኛ ፡ መደብ ፡ | ፫ኛ ፡ መደብ ፡ |
|---|---|---|
| ተናግሬ ፡ | ተናግረህ ፡ | ተናግሮ ፡ |
| ተናግረን ፡ | ተናግረሽ ፡ | ተናግራ ፡ |
| | ተናግራችሁ ፡ | ተናግረው ፡ |

የአሁንና ፡ የትንቢት ፡ ጊዜያት ፡

| ፩ኛ ፡ መደብ ፡ | ፪ኛ ፡ መደብ ፡ | ፫ኛ ፡ መደብ ፡ |
|---|---|---|
| እናገር ፡ | ትናገር ፡ | ይናገር ፡ |
| እንናገር ፡ | ትናገሪ ፡ | ትናገር ፡ |
| | ትናገሩ ፡ | ይናገሩ ፡ |

ቦዝ ፡ አርእስትን ፡ ለመግለጽ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ትርጓሜውን ፡ ይለውጣል ፤ ይኸውም ፡ ቅጽል ፡ በመሆን ፡ ፋንታ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ይሆናል ፡ ማለት ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

1 ጠንክሮ ፡ ማጥናት ፡ ለቁም ፡ ነገር ፡ እንደሚያበቃ ፡ መተማመን ፡ አለባችሁ ።

2 በጣም ፡ በትጋት ፡ ማጥናት ፡ ለቁም ፡ ነገር ፡ እንደሚያበቃ ፡ መተማመን ፡ አለባችሁ ። አጓጠ ፡ መናገር ፡ ከውርደት ፡ ላይ ፡ እንጂ ፡ ከደግ ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ ሲጥል ፡ አላየሁም ።

ቦዛዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ አርእስትን ፡ ለመግለጽ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ አገባቡ ፡ ልክ ፡ እንደ ፡ ተራ ፡ ቦዝ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

1 እጅግ ፡ በጣም ፡ ተራቆ ፡ መመራመር ፡ ከመንገድ ፡ ያወጣል ።
እጅግ ፡ በጣም ፡ በርቀት ፡ መመራመር ፡ ከመንገድ ፡ ያወጣል ።

2 ገንዘብን ፡ ቀምቶ ፡ መበልጸግ ፡ በራስ ፡ ላይ ፡ ፍምን ፡ ወይም፡ ረመጥን፡ እንደ፡ ማዘጋጀት ፡ ያለ ፡ ነው ።

በቅሚያ ፡ ገንዘብ ፡ መበልጸግ ፡ በራስ ፡ ላይ ፡ ፍምን ፡ ወይም ፡ ረመጥን ፡ እንደ ማዘጋጀት ፡ ያለ ፡ ነው ።

ቦዝ ፡ ያለረዳት ፡ ግስ ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ይገባል ፤ በዚህም ፡ ጊዜ ፡ መደ ቦችን ፡ እየለየ ፡ ያመለክታል ፤ ስለዚህ ፡ ቦዝ ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ያለውን ፡ ስም ፡ እየለየ ፡ ከማመልከቱ ፡ በላይ ፡ ምንን ፡ እንደሚሠራ ፡ ይገልጻልና ፤ በቅጽል ፡ ሥር ፡ መጠ ቅለል ፡ ይገባዋል ።

ሕገኛ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ስምንቱን ፡ ተውላጠ ፡ ስሞች ፡ አያመለክትም ፤ ቦዝ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ አይደለም ፤ ምክንያቱም ፡ ያንቀጹን ፡ ባለቤት ፡ ስለሚገልጽ፡ ነው ። ከእንግዴህ ፡ ወዲህ ፡ ቦዝ ፡ በተውሳከ ፡ ግስ ፡ ሥር ፡ መጠቅለል ፡ የለበትም ።

<u>አስረጅ ፡</u>

1 አየለ ፡ ምሳውን ፡ በልቶ ፡ ተኛ ።
2 ደመቀ ፡ ክፍሉን ፡ ጠርጎ ፡ ሄደ ።

እንሆ ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ የተሰጡት ፡ ማስረጃዎች ፡ አየለና ፡ ደመቀ ፡ አንዳንድ ፡ ነገር ፡ መሥራታቸውን ፡ ያመለክታሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ ቦዞቹ ፡ ሥራው ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ተሠራ ፡ በፍጹም ፡ አያመለክቱም ።

## ፲፯ኛ ፡ መልመጃ ።

አጼ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ከፋህላ ፡ ተነሥተው ፡ የተረፏቸውን ፡ ጥቂቶች ፡ ወታደሮች ፡ አስከትለው ፡ እመቅደላ ፡ ምሽግ ፡ ገብተው ፡ በመድፍና ፡ በጥይት ፡ ከእንግሊዞች ፡ ጋራ ፡ ጦርነት ፡ ገጠሙ ። በዚሁ ፡ ጦርነት ፡ ከእንግሊዝ ፡ የጦር ፡ ሰፈር ፡ የተተኰሰ ፡ የመድፍ ፡ ጥይት ፡ የነበሩበትን ፡ መዝጊያ ፡ ሰብሮ ፡ ጣለው ። እንግሊዞችም ፡ ይዘውት ፡ የነበረው ፡ መድፍና ፡ መትረየስ ፡ አዲስ ፡ የመጣ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የመድፉ ፡ ጥይት ፡ ተተኵሶ ፡ እመ ሬት ፡ ካረፈ ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ እየፈነዳ ፡ የመጣውን ፡ ያህል ፡ ደግሞ ፡ እየሄደ ፡ ጠላ ትን ፡ የሚጎዳ ፡ ነበር ፡ ይባላል ። ንጉሡም ፡ በመጨረሻ ፡ ባላቸው ፡ ኀይል፡ከጠላታቸው ፡ ተዋግተው ፡ ድል ፡ ስለ፡ ሆኑ ፡ ባጠገባቸው ፡ የቆሙትን ፡ የሚወዷቸውን ፡ ወታደሮች ፡ ስመው ፡ እንዲሸሹ ፡ ካሰናበቷቸው ፡ በኋላ ፡ እንግሊዞች ፡ ለመማረክ ፡ ታችኛውን ፡ በር ፡ ሰብረው ፡ እየተጋፉ ፡ ሲገቡ ፡ ወደ ፡ ላይኛው ፡ በር ፡ አልፈው ፡ በጨበጡት ፡ በገዛ ፡ ሽጉጣቸው ፡ ራሳቸውን ፡ ገድለው ፡ ወድቀው ፡ ተገኙ ።

ተክለ ፡ ጻድቅ ፡ መኵሪያ ።

1 ከተሰጠው ፡ ምንባብ ፡ ውስጥ ፡ ቦዛውያን ፡ አንቀጾችን ፡ እየለቀምህ ፡ ጻፍ ።
2 አገባባቸውን ፡ በጥንቃቄ ፡ እየለየህ ፡ አመልክት ።
3 ጊዚያታቸውንና ፡ መደባቸውን ፡ ጻፍ ።
4 ተራ ፡ ቦዝ ፡ የሆኑትን ፡ ቃላት ፡ ለብቻቸው ፡ አመልክት ።
5 ቦዛውያን ፡ ንኡስ ፡ ሐረጎችንም ፡ ለብቻቸው ፡ አመልክት ።

6 ቅጽላውያን ፡ ጥገኛ ፡ ሐረጎችን ፡ ልቀምና ፡ ጻፍ ።

7 ስሞችን ፡ ልቀምና ፡ ዐይነታቸውን ፡ አመልከት ።

8 ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡ የሆኑትን ፡ ሁሉ ፡ ጻፍና ፡ ጊዜያቸውን ፡ አመልከት ።

9 እንግሊዞች ፡ በምን ፡ ምክንያት ፡ ከአጼ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ተዋጉ ፡ ደኅና ፡ አድርገህ ፡ አስረዳ ።

10 አጼ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ለምንድር ፡ ነው ፡ ራሳቸውን ፡ በሽጉጥ ፡ የገደሉ ?

አርእስት ፡ ከግስ ፡ የተገኘ ፡ ስም ፡ ነው ። በግስነቱ ፡ ይስባል ፡ እንደ ፡ ነገር ፡ ስምነቱ ፡ ደግሞ ፡ የስምን ፡ ሙያ ፡ ይከተላል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ጾታና ፡ ብዛት ፡ የለውም ።

አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ አርእስት ፡ የግስ ፡ እናት ፡ ተብሎ ፡ ይጠራል ። ይኸውም ፡ እርሱን ፡ ካገኙ ፡ በኋላ ፡ እርሱን ፡ ይዞ ፡ እየፈለጉ ፡ ግስን ፡ ለማግኘት ፡ የሚቻል ፡ ስለ፡ ሆነ፡ ነው ።

**አስረጅ ፡** **አርእስት ፡ እንደ ፡ ባለቤት ።**

1 በዕድሜ ፡ መሰንበት ፡ ብዙ ፡ ነገርን ፡ እንደሚያሳይ ፡ የተረጋገጠ ፡ ነው ።

2 መሥራት ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ የብልጽግና ፡ አክሊልን ፡ ያወርሳል ።

**እንደ ፡ ተሳቢ ።**

3 ንቦች ፡ እንኳ ፡ ሳይማሩ ፡ በተፈጥሮ ፡ ጠባያቸው ፡ አበባን ፡ ቀሥመው ፡ ማር ፡ መሥራትን ፡ ያውቃሉ ።

4 አንድ ፡ ወታደር ፡ አነጣጥሮ ፡ መተኰስን ፡ ካላወቀ ፡ ምኑን ፡ ወታደር ፡ ሆነው ?

**እየሳበ ፡ ባለቤት ፡ ሲሆን ።**

5 እንቅልፍን ፡ ማብዛት ፡ ያደኸያል ።

6 ሰውን ፡ ማፍቀር ፡ የእግዚአብሔር ፡ የባሕርይ ፡ ገንዘቡ ፡ ነው ።

**የመስተዋድድ ፡ ተገዥ ፡ ሲሆን ።**

7 በማግኘት ፡ ላይ ፡ ማጣት ፡ እንዳለ ፡ ማሰብ ፡ አለብን ።

8 የማግኘት ፡ ጥቅሙ ፡ ሊሠራበት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በከንቱ ፡ ሊሻግት ፡ አይደለም።

9 ንቦች ፡ ለመሥራት ፡ እንጂ ፡ ለመብላት ፡ አይቾሉም ።

**፯ኛ ፡ መልመጃ ።**

1 ደረደረ ፡ የሚለውን ፡ ግስ ፡ በግስ ፡ ደንብ ፡ አርባና ፡ አርእስቱን ፡ አግኝ ።

2 ያገኘኸውን ፡ አርእስት ፡ የመስተዋድድ ፡ ተገዥ ፡ እንደሚሆን ፡ አድርገህ ፡ አረፍተ ፡ ነገርን ፡ ሥራ ።

3 ይህኑ ፡ አርእስት ፡ ቅጽል ፡ አድርገው ።

4 አርእስትን ፡ ተራ ፡ ቦዝ ፡ እንደሚገልጸው ፡ አድርገህ ፡ አንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገርን ፡ ሥራ ።

5 አርእስትን ፡ በዛዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ እንደሚገልጸው ፡ አድርገህ ፡ አንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራ ።

6 የሚከተሉትን ፡ አርእስት ፡ ግለጻቸው ።

(ሀ) መሞላቀቅ ፡ (ለ) መቀባጠር ፡ (ሐ) መርጋት (መ) ማፍቀር ፡

ግሳዊ ፡ ቅጽል ፡- ግሳዊ ፡ ቅጽል ፡ የምንለው ፡ ግስን ፡ በግእዝ ፡ ደንብ ፡ አርብተን ፡ የምናገኘው ፡ ቅጽል ፡ ነው ። እንደዚህ ፡ ያለው ፡ ቅጽል ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ በሣልስ ፡ ፊደል፡ ይጨርሳል ።

ምሳሌ ፡- ፈሪ ፡ ደባቂ ፡ መሪ ፡ መርማሪ ፡ ቈፋሪ ፡ ተናጋሪ ፡ አስተናባሪ ፡ ፈላጊ ፡ ገዢ ፡

ግሳዊ ፡ ቅጽል ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ በስም ፡ ፋንታ ፡ እየገባ ፡ የስምን ፡ ስፍራ ፡ ሲይዝ ፡ ይታያል ። ለምሳሌ ፡ ሰባኪ ፡ ተላላኪ ፡ መሪ ፡ መርማሪ ፡ ተናጋሪ ፡ ፈላጊ ፡ ፈሪ ፡ ወጊ ፡ ሰባቂ ፡ ኆሮ ፡ ጠቢ ፡ ጠራጊ ፡

በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ግሳዊ ፡ ቅጽል ፡ የስምን ፡ ሥራ ፡ በሚሠራበት ፡ ጊዜ ፡ ግሳዊ፡ ስም፡ መባል ፡ አለበት ። ነገር ፡ ግን ፡ በበቂ ፡ ቅጽልነት ፡ ይጠራል ፡ እንጂ ፡ ግሳዊ ፡ ስም ፡ መባል ፡ አይገባም ፡ የሚሉ ፡ ይኖሩ ፡ ይሆናል ። ቢሆንም ፡ ሥራው ፡ በሚያመዝንበት ፡ በኩል ፡ መጠራት፡ አለበት ። ግሳዊ ፡ ስም፡ወይም፡ ግሳዊ፡ ቅጽል፡ ጊዚያት፡ የለውም ።

ግሳዊ ፡ ስም ፡ ወይም ፡ ግሳዊ ፡ ቅጽል ፡ እንደ ፡ ግስ ፡ ይሰባል ።

አስረጅ ፡-

አቶ ፡ በድሉ ፡ ሰውን ፡ አክባሪና ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈሪ ፡ ነው ።

ክብሩን ፡ ፈላጊ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ከሰው ፡ በላይ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ከሰው ፡ በታች ፡ ይውላል ።

ሳቢ ፡ ዘር፡-ሳቢ ፡ ዘር ፡ በስም ፡ ደንብ ፡ ከመብዛቱ ፡ በስተቀር ፡ ልክ ፡ እንደ ፡ አርእስት ፡ ነው ። ሳቢ ፡ ዘር ፡ እንደ ፡ ግስ ፡ ጾታና ፡ ርባታ ፡ የለውም ፤ በግስነቱ ፡ ግን ፡ ይስባል ።

አስረጅ ፡-

<u>ሳቢ ፡ ዘር ፡ ባለቤት ፡ ሲሆን ፡</u>

1 አስተያየትህ ፡ አያምረኝም ።

2 አነጋገሩ ፡ ለብቻው ፡ ነው ።

<u>ሳቢ ፡ ዘር ፡ ሲስብና ፡ ሲሳብ ፡</u>

3 ደብዳቤ ፡ አጻጻፍን ፡ ከየት ፡ ተማርክ ?

4 ወይዘሮ ፡ ፈለቀች ፡ ከመፍተሏ ፡ በላይ ፡ እንዝርት ፡ አያያዝን ፡ ( ስታሳምር ፡ ለብቻዋ ፡ ናት) ፡ ታስተምራለች ።

ምሳሌ ፡- አነጋገር ፡ አያያዝ ፡ አስተያየት ፡ አለባበስ ፡

**ጥሬ ፡ ዘር ፡**-ጥሬ ፡ ዘር ፡ ማለት ፡ ተረብቶ ፡ የወጣለት ፡ ወዲያና፡ ወዲህ ፡ የማይል፡ ከግስ ፡ የተገኘ ፡ የቊሳቊስ ፡ ወይም ፡ የነገር ፡ ስም ፡ ነው ።

**አስረጅ ፡-**

**ጥሬ ፡ ዘር ፡ እንደ ፡ ባለቤት ፡ ሲገባ ።**

1 ምርቃት ፡ ዕድሜን ፡ ያስረዝማል ።
2 ጥሩ ፡ ጥሩ ፡ ምግብ ፡ ብቻ ፡ ሰውን ፡ አያወፍርም ።

**ጥሬ ፡ ዘር ፡ እንደ ፡ ተሳቢ ።**

3 ሥንቃችንን ፡ ሌባ ፡ ወሰደብን ።
4 ልመናችንን ፡ አይንቅም ።

| | | | |
|---|---|---|---|
| የንኡስ፡ አንቀጽን ፡ ክፍሎች ፡ በግእዝ ፡ ደንብ፡ እያረባሁ፡ በሚከተለው ፡ አሳያለሁ ። | | | |
| መረቀ ፡ | የዋህ ፡ ኀላፊ ፡ ዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡ | መራቂ ፡ | ግሳዊ፡ቅጽል፡ ወይም፡ስም። |
| ይመርቃል ፡ | ያሁንና፡ የትንቢት፡ ጊዜያት፡ ዐ፡አ፡ | አመራረቅ፡ | ሳቢ ፡ ዘር ። |
| ይመርቅ ፡ ዘንድ ፡ | አዋዋይ ፡ አንቀጽ ፡ | ምርቃት ፡ | ጥሬ ፡ ዘር ፡ |
| ይመርቅ፡ | ትእዛዝ ፡ አንቀጽ ፡ | | |
| መመረቅ ፡ | አርእስት ፡ | | |

**በግዕዝና ፡ ባማርኛ ፡ ደንብ ፡ የግስ ፡ ርባታ ፡**

**በሦስተኛ ፡ መደብ ፡ ወንዴ ፡ ጾታ ፡**

| በግዕዝ ፡ ደንብ ፡ | | በአማርኛ ፡ ደንብ ፡ | |
|---|---|---|---|
| ፈለቀ ፡ | የዋህ ፡ ኀላፊ ፡ | ፈለቀ ፡<br>ፈልቋል ፡<br>ፈልቆ ፡ ነበር ፡ | የዋህ ፡ ኀላፊ ፡<br>የቅርብ ፡ ኀላፊ ፡<br>የሩቅ ፡ ኀላፊ ፡ |
| ይፈልቃል ፡<br>ይፈልቃል ፡ | ያሁን ፡ ጊዜያት ፡<br>የትንቢት ፡ ጊዜያት ፡ | ይፈልቃል ፡<br>ይፈልቃል ፡<br>ሊመርቅ ፡ ነው ፤ | ያሁን ፡ ጊዜያት ፡<br>የትንቢት ፡ ጊዜያት፡<br>የቅርብ ፡ ትንቢት ፡ |
| ይመርቅ ፡ ዘንድ ፡<br>ይመርቅ ፡ | አዋዋይ ፡ አንቀጽ ፡<br>ትእዛዝ ፡ አንቀጽ ፡ | ቢመርቅ ፡ ኖሮ ፡<br>መርቆ፡ ቢሆን፡ ኖሮ ፡<br>ቢመርቅ ፡<br>ይመርቅ ፡ ዘንድ ፡<br>ሊመርቅ ፡<br>እንዲመርቅ ፡<br>በመረቀ ፡ ነበር ፡ | አዋዋይ ፡ አንቀጽ ፡ |

| | | | |
|---|---|---|---|
| | | ይመርቅ ፡ | ያሁን ፡ ትእዛዝ ፡ |
| | | እንዲመርቅ፡ ይሁን፡- | የትንቢት፡ ትእዛዝ ፡ |
| መመረቅ ፡ | አርእስት ፡ | መመረቅ ፡ | አርእስት ፡ |
| መራቂ ፡ | ግሳዊ፡ቅጽል፡ወይም፡ስም፡ | መራቂ ፡ | ግሳዊ ፡ ቅ፡ ወይም፡ ስም፡ |
| አመራረቅ ፡ | ሳቢ ፡ ዘር ፡ | አመራረቅ ፡ | ሳቢ ፡ ዘር ፡ |
| ምርቃት ፡ | ጥሬ ፡ ዘር ፡ | ምርቃት ፡ | ጥሬ ፡ ዘር ፡ |

በግዕዝና ፡ ባማርኛ ፡ ደንብ ፡ አንድ ፡ ግስ ፡ እንዴት ፡ እንደሚረባ ፡ አርብቼ ፡ አሳ ይቻለሁ ፤ ልዩነታቸውንም ፡ ለማወቅ ፡ አስቸጋሪ ፡ አይደለም ፤ ብቻ ፡ አረባባቸውን ፡ ደኅና ፡ አድርጎ ፡ መመልከት ፡ ነው ።

## ፳ኛ ፡ መልመጃ ፡

1 የሚከተሉትን ፡ ቃላት ፡ ግለጻቸው ።

(ሀ) ተሻጋሪ ፡ ዐምድ ፡
(ለ) የማይሻገር ፡ ዐምድ ፡
(ሐ) ገቢር ፡
(መ) ተገብሮ ፡

2 በሚከተሉት ፡ ቃላት ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮችን ፡ ሥራ ።

(ሀ) ዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡ (በሩቅ) ፡ ኀላፊ ፡
(ለ) ትእዛዛዊ ፡ አንቀጽ ፡ (ባሁን ፡ ጊዜያት) ፡
(ሐ) አዋዋይ ፡ አንቀጽ ፡ (በሚያስረው) ፡
(መ) ንኡስ ፡ አንቀጽ ፡ (በአርእስትና ፡ በሳቢ ፡ ዘር ፡ እንደ ፡ ባለቤት) ፡

3 የሚከተሉትን ፡ አረፍተ፡ ነገሮች፡ ከገቢርነት፡ ወደ፡ ተገብሮነት፡ ለውጣቸው።

(ሀ) አየለ ፡ አዝመራውን ፡ ይሰበስባል ።
(ለ) ፈለቀች ፡ ቤቷን ፡ ታሳምራለች ።
(ሐ) አቶ፡ማን፡ደፍሮት፡ መሐንዲሱ፡የዓለም፡ ገበያን፡ ከተማ፡ ፕላን፡አነሡ።

4 «አለ» ፡ የሚባለው ፡ ግስ ፡ አራት ፡ ባህሎች ፡ አሉት ፤ በነርሱም ፡ አንዳንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሠርተህ ፡ አሳይ ።

5 መራን ፡ ባራቱም ፡ የግስ ፡ ስልቶች ፡ ጊዜያት፡ አርባው ፤ አስደራጊ ፡ አደራራ ጊና ፡ አዳራጊን ፡ ልትሠራባቸው ፡ አያስፈልግም ።

## ፲፩ ፡ ከተሻጋሪና ፡ ከማይሻገር፡ የሚነሡ፡ ግሶች ፡ ስምና ፡ መግለጫ ፡

ከተሻጋሪ ፡ ወይም ፡ ከማይሻገር ፡ ዐምድ ፡ ላይ ፡ በባዕድ ፡ መነሻ ፡ ረዳትነት ፡ የሚመሠረቱት ፡ ግሶች ፡ አስደራጊ ፡ አደራራጊ ፡ አዳራጊ ፡ ተደራጊ ፡ ተደራራጊ ፡ ተብ

ለው ፡ ይጠራሉ ። ባንዳንድ ፡ ግሶች ፡ ላይ ፡ አዳራጊና ፡ ተዳራጊ ፡ የማይገኙበት ፡ ጊዜ ፡ አለ ። አድራጊ ፦ አድራጊ ፡ ማለት ፡ ራሱ ፡ ሠራተኛ ፡ ሆኖ ፡ ሊሠራው ፡ የሚገባውን ፡ ነገር ፡ የሚሠራ ፡ ነው ።

አስደራጊ ፦ አስደራጊ ፡ ማለት ፡ እርሱ ፡ ምክንያት ፡ ሆኖ ፡ ሌላውን ፡ ነገር ፡ የሚያሠራ ፡ ነው ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ጉዳይ ፡ አስፈጻሚ ፡ ሆኖ ፡ ይሠራል ።

አደራራጊ ፦ እርሱ ፡ ምክንያት ፡ ሆኖ ፡ አንዱንና ፡ ሌላውን ፡ የሚያጣላ ፡ ወይም ፡ የሚያፋቅር ፡ ነው ።

አዳራጊ ፦ ካንዱ ፡ ጋራ ፡ አብሮ ፡ ረዳት ፡ ሆኖ ፡ የሚሠራ ፡ ነው ፤ በፍቅርም ፡ ሆነ ፡ ወይም ፡ በጠብ ፡ በሁለቱም ፡ በኩል ፡ ረዳት ፡ እንደሚሆን ፡ ያስረዳል ።

ተደራጊ ፦ ሥራን ፡ ተቀባይ ፡ መሆኑን ፡ የሚያመለክት ፡ ግስ ፡ ነው ።

ተደራራጊ ፦ እርስ ፡ በርስ ፡ መደባደብና ፡ መፋቀር ፡ ወይም ፡ መረዳዳትና ፡ መተዛዘን ፡ ይሆናል ።

ተዳራጊ ፦ አንዱ ፡ ካንዱ ፡ ጋራ ፡ ሲጋጭ ፡ ተዳራጊ ፡ ይሆናል ።

ምሳሌ ፦

1 አሰፋ ፡ ወንድሙን ፡ ሸኘ ።
2 አሰፋ ፡ አሽከሩን ፡ ልኮ ፡ ወንድሙን ፡ አሸኘ ።
3 አሰፋ ፡ ፈለቀንና ፡ በልሁን ፡ አጨፋጨፋቸው ።
4 አሰፋ ፡ ዛሬ ፡ ጤፋችንን ፡ አስተጫጭዶን ።
5 ጤፋችን ፡ በሚገባ ፡ ታጭዶ ፡ ተነቸ ።
6 የሐረር ፡ ሕዝብ ፡ አንድ ፡ ፋብሪካ ፡ ለማቆም ፡ ይመካከራል ።
7 አሰፋ ፡ ማናቸውንም ፡ ነገር ፡ ከባልንጀራው ፡ ጋራ ፡ ይማከራል ።

ማስገንዘቢያ ፤

አደራራጊና ፡ አዳራጊ ፡ በጣም ፡ የተቀራረቡ ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ በሁለቱ ፡ ልዩነት ፡ መካከል ፡ መቸገር ፡ አስፈላጊ ፡ አይመስለኝም ።

እንደዚሁም ፡ በተደራራጊና ፡ በተዳራጊ ፡ መካከል ፡ በጣም ፡ ልዩነት ፡ ያለው ፡ ነገር ፡ ጉልህ ፡ ሆኖ ፡ ስለማይታይ ፡ በነርሱ ፡ መቸገር ፡ አያስፈልግም ።

## ፲፪ ፡ የግስ ፡ አመዳደብ ፡ በርባታ ፡ አካሄድ ፡

ግስ ፡ በሁለት ፡ አካሄድ ፡ ይመደባል ፤ እነርሱም ፡ የሚከተሉት ፡ ናቸው ።

(ሀ) ሕገኛ ፡ ግስ ፡ (ለ) ሕገ ፡ ወጥ ፡ ግስ ፡

(ሀ) ሕገኛ ፡ ግስ ፡ የሚባለው ፡ በቦዝ ፡ አንቀጽና ፡ በአርእስቱ ፡ ሌላ ፡ ፊደልን ፡ ሳይወልድ ፡ በሦስቱም ፡ ጊዜያት ፡ የሚረባ ፡ ግስ ፡ ነው ።

(ለ) ሕገ ፡ ወጥ ፡ በቃሉ ፡ መጀመሪያ ፡ ወይም ፡ መጨረሻ ፡ ባዕድ ፡ ፊደልን ፡ እየወለደ ፡ ወይም ፡ እያጐደለ ፡ የሚረባ ፡ ግስ ፡ ነው ። እንደዚህ ፡ ያለው ፡ ግስ ፡ በየጊዚያቱ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ በየአርእስቱና ፡ በየቦዙ ፡ ያጐድላል ፤ ወይም ፡ ይጨምራል ። ነባር ፡ ግስም ፡ በሦስቱ ፡ ጊዚያት ፡ የማይረባ ፡ በመሆኑ ፡ በዚህ ፡ ክፍል ፡ ይጠቀለላል ።

ምሳሌ ፡-

(ሀ) ሕገኛ ፡ ግስ ፡ መከረ ፡ መከሯል ፡ መክሮ ፡ ነበር ፡ ይመክራል ፡ ይመክር ፡ ነበር ፡ በመከረ ፡ ነበር ፡ ይመክር ፡ ይሆናል ።

መምከር ፡ መክሮ ፡ ይምከር ።

(ለ) ሕገ ፡ ወጥ ፡ ግስ ፡ በላ ፡ በልቷል ፡ በልቶ ፡ ነበር ፡ ይበላል ፡ ይበላ ፡ ነበር ፡ በበላ ፡ ነበር ፡ ይበላ ፡ ይሆናል ።

መብላት ፡- በልቶ ፡- ይብላ ።

አለ ፡ - ብሎ ፡ - ማለት ፡ አየ ፡ አይቶ ፡

ነባር ፡ ግሥን ፡ በሕገ ፡ ወጥ ፡ ግስ ፡ ውስጥ ፡ መጠቅለል ፡ ነው ።

በአዕማድ ፡ ላይ ፡ ቃላቸውን ፡ ይለውጣሉ ፡ የሚባሉ ፡ ግሶች ፡ በራብዕና ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ በግዕዝ ፡ የሚጨርሱ ፡ ግሶች ፡ ናቸው ።

የመምጣት ፡ ግስ ፡ «ናን» ፡ ያስገኛል ።

የመሆን ፡ ግስ ፡- ነው ፡ «ነበርን» ፡ ይወልዳል ።

የመኖር ፡ ግስ ፡ - አለ ፡ - እንደዚሁም ፡ «ኖረን» ፡ ይወልዳል ።

## የማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡ ዝርዝር ፡ አፈታት ።

ማሰሪያ ፡ አንቀጽን ፡ ስንዘረዝር ፡ በሚከተሉት ፡ ዐቅዶች ፡ መሥራት ፡ ይገባል ።

1 ዐይነቱን ፡ 3 ስልቱን ፡ 5 ጊዚያቱን ፡ 7 ጾታውን ፡

2 ጠባዩን ፡ 4 ቍጥሩን ፡ 6 መደቡን ፡ 8 ርባታውን ፡

ምሳሌ ፡- 1 ቀያይ ፡ ላሞች ፡ በመስኩ ፡ ውስጥ ፡ ይግጣሉ ።

ይግጣሉ ፡ የማይሻገር ፡ ግስ ፡ ገቢር ፡ ዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡ የብዙ ፡ ያሁን ፡ ጊዚያት ፡ ፫ኛ ፡ መደብ ፡ ሕገኛ ፡ የወል ፡ ጾታ ፡

2 ልጆች ፡ ማስተማርን ፡ ሥራዬን ፡ እወዳለሁ ።

እወዳለሁ ፡ ተሻጋሪ ፡ ገቢር ፡ ዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡ ነጠላ ፡ ያሁን ፡ ጊዚያት ፡ ፩ኛ ፡ መደብ ፡ ሕገኛ ፡ የወል ፡ ጾታ ፡

## የቦዝ ፡ ዝርዝር ፡ አፈታት ፡

የቦዝን ፡ ዝርዝር ፡ አፈታት ፡ በሚከተሉት ፡ ዐይነት ፡ መዘርዘር ፡ አለብን ።

1 ዐይነቱን ፡ 3 ቍጥሩን ፡ 5 መደቡን ፡
2 ጠባዩን ፡ 4 ጊዚያቱን ፡ 6 አገባቡን ፡

ምሳሌ ፡- ልጁ ፡ ሻይን ፡ አፍልቶ ፡ አጠጣን ።

አፍልቶ ፡ ተሻጋሪ ፡ አድራጊ ፡ ነጠላ ፡ የዋህ ፡ ኀላፊ ፤ ፫ኛ ፡ መደብ ፡ ቅጽል ፡ ቅጽልነቱ ፡ ለልጁ ፡ ነው ።

ልጁ ፡ ምን ፡ እንዳደረገ ፡ ያመለክታል ፡ እንጂ ፡ ሻዩን ፡ እንዴት ፡ አድርጎ ፡ እንዳጠጣን ፡ ወይም ፡ ከምን ፡ ጋራ ፡ ደባልቆ ፡ እንዳጠጣን ፡ ወይም ፡ ለምን ፡ እንዳጠጣን ፡ አይነግረንም ፤ ሙያው ፡ በቅጽል ፡ ውስጥ ፡ የተጠቀለለበት ፡ ስለዚህ ፡ ነው ።

## የአርእስትና ፡ የሳቢ ፡ ዘር ፡ አፈታት ፡

1 ዐይነቱን ፡ 3 ቍጥሩን ፡
2 ጠባዩን ፡ 4 አገባቡን ፡
} መናገር ፡ አለብን ።

## የግሳዊ ፡ ቅጽል ፡ ወይም ፡ የስም ፡ አፈታት ።

1 ዐይነቱን ፡ 3 ቍጥሩን ፡
2 ጠባዩን ፡ 4 አገባቡን ፡
} መናገር ፡ አለብን ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ።

ተውሳከ ፡ ግስ ፡- ቅጽል ፡ ስምን ፡ እያጐላ ፡ እንደሚገልጸው ፡ እንዲሁም ፡ እሱ ፡ ግስን ፡ ይገልጻል ።

አስረጅ ፡-

1 ተክለ ፡ አብ ፡ ትናንት ፡ ወደ ፡ ደደር ፡ ተላከ ።
2 ተክሌ ፡ ዘወትር ፡ ያጠናል ።
3 ወዴት ፡ ትሄዳለህ ?
4 ትምህርቱን ፡ በፍጹም ፡ ጠልቷል ።

እንሆ ፡ በተሰጡት ፡ ማስረጃዎች ፡ ውስጥ ፡ ትናንት ፡ ዘወትር ፡ ወዴትና ፡ በፍጹም ፡ ጊዜን ፡ ቦታንና ፡ ሁኔታን ፡ ( ደረጃን ) ፡ ያመለክታሉ ።

ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ግሥን ፡ ለመግለጽ ፡ የሚጨመር ፡ ቃል ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ግስን ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ ቅጽልን ፡ ተውሳከ፡ ግስን ፡ ንኡስ፡ ሐረግንና ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግን ፡ ይገልጻል ።

አስረጅ ፦

1 አቶ ፡ ወንድሙ ፡ ነገ ፡ ይመጣል ።
2 ፈለቀ ፡ በጣም ፡ ደግ ፡ ልጅ ፡ ነው ።
3 እንግዴህ ፡ በጥንቃቄ ፡ ሥራ ።
4 አቶ፡መንግሥቱ ፡ የያገኙትን፡ዕቃ ፡ በቀስታ፡በጠረጴዛ፡ ላይ ፡ አስቀምጠው።
5 ይህ ፡ ልጅ ፡ ዘወትር ፡ ቢማር ፡ ማንም ፡ አይደርስበትም ።

መስተፃምርና ፡ መስተዋድድ ፡ ከሌላ ፡ ቃላት ፡ ጋራ ፡ አብረው ፡ ካልገቡ ፡ ለየ ብቻቸው ፡ ስሜት ፡ የሚሰጡ ፡ ስላልሆኑ ፡ እነርሱን ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ይገልጻቸዋል ፡ ለማለት ፡ አያስደፍርም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ንኡስ ፡ ሐረግና ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ በአረፍተ ፡ ነገር፡ ውስጥ ፡ ገብተው ፡ የተለየ ፡ አገልግሎት ፡ ስለሚያሳዩ ፡ እነርሱን ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ይገ ልጻቸዋል ፡ ቢባል ፡ በጣም ፡ የተስማማ ፡ ነው ።

## ፩ ፡ የተውሳከ ፡ ግስ ፡ ዐይነቶች ፡

### የዋህና ፡ መጠይቅ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡

ተውሳከ ፡ ግስ ፡ በሚሰጠው ፡ አገላለጽ ፡ ስልት ፡ ( መንገድ) ፡ ይከፈላል ።

የዋህ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡

(ሀ) የጊዜ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ -የጊዜ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ አንድ፡ ሥራ ፡ መቼ ፡ እንደ ፡ ተሠራ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

አስረጅ ፦

1 ይህን ፡ ዓምና ፡ ተምረነው ፡ ነበር ።
2 እግዚአብሔር ፡ በደኅና ፡ ቢያከርመን ፡ ለላመት ፡ እንሠራዋለን ።
3 ነገ ፡ እንመለሳለን ።
4 ዘንድሮ ፡ ጠንክሬ ፡ አርሳለሁ ።
5 ልጁ ፡ በየቀኑ ፡ ያጠፋል ።
6 በቅርቡ ፡ ወደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ መሄዱን ፡ አላውቅም ።

(ለ) የቍጥር ፡ ተውሳከ ፡ ግስ፦ አንድ ፡ ነገር ፡ ሲሠራ ፡ ስንት ፡ ጊዜ ፡ እየተደጋገመ ፡ እንደ፡ተሠራ ፡ ወይም፡ ስንት ፡ ጊዜ ፡ እየተደጋገመ ፡ እንደሚሠራ ፡ የሚያመለክት ፡ ተው ሳከ ፡ ግስ ፡ ነው ።

አስረጅ ፦

1 ስንትዬ ፡ ኀይል ፡ በጥበብ ፡ ላይ ፡ ተመካች !
2 ደጋግሜ ፡ አጠናለሁ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ አይሆንልኝም ።
3 አንደዬ ፡ ከተናገርሁ ፡ በዚያው ፡ ድርቅ ፡ ልበል፡ ማለትን፡ ካንተ፡ አስወግድ።
4 እባክህን ፡ ወንድሜ ፡ ይህንን ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ሥራው ።
5 መጀመሪያ ፡ የደረሰ ፡ ቦታን ፡ ያገኛል ።

(ሐ) የቦታ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡- ቦታን ፡ የሚያመለከት ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡-

1 ብዙ ፡ ሰዎች ፡ እውጭ ፡ ፈሰዋል ።
2 ልጁን ፡ እዚህ ፡ አስቀምጠው ።
3 እባክህ ፡ አንተ ፡ ልጅ ፡ በራስጌዬ ፡ አትቁም ።
4 አየለ ፡ ወዲህ ፡ ና ።
5 ከብቶቹን ፡ ወዲያሃች ፡ አትውሰዳቸው ።
6 ዋጋህን ፡ በሚገባ ፡ ታገኛለህ ፤ ብቻ ፡ ወዲህና ፡ ወዲያ ፡ አትበል ።

(መ) የአኳኋን ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡-አንድ ፡ ግስ ፡ እንዴት ፡ ወይም ፡ በምን ፡ ሀይነት ፡ ወይም ፤ አኳኋን ፡ እንደ ፡ ተደረገና ፡ እንደሚደረግ ፡ የሚያሳይ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡-

1 በቀስታ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ አንሡኝ ።
2 ሁላችንም ፡ አብረን ፡ በዝግታ ፡ እንሂድ ።
3 የዠመሩትን ፡ ሳይፈጽሙት ፡ እንዲያው ፡ ደከሙ ።
4 ወንበዴዎች ፡ ድንገት ፡ እንዳይደርሱብኝ ፡ ከዚህ ፡ ቦታ ፡ ልጥፋ ፡ (ልሂድ) ።
5 ወንጌል ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ ተፋቀሩ ፡ ትላለች ።

ሠ) የመጠንና ፡ የማበላለጥ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡- ተውሳከ ፡ ግሱ ፡ ስንት ፡ እንደ ፡ ሆነና ፡ እስከ ፡ ስንት ፡ እንደሚደርስ ፡ የሚገልጽ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡-

1 አቶ ፡ ፈለቀ ፡ በጕዳዩ ፡ በጣም ፡ ተጨንቀውበታል ።
2 የሥላሴ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ተሠርቶ ፡ ሊያልቅ ፡ ምንም ፡ ያህል ፡ አልቀረ ውም ።
3 የዚያ ፡ ቤት ፡ ጌጥ ፡ በፍጹም ፡ ተወጫምዷል ።
4 ይህን ፡ ነገር ፡ በጭራሽ ፡ አላስታውሰውም ።
5 የአቶ ፡ በልሁ ፡ ተጠሪ ፡ እህሉን ፡ ግማሽ ፡ በግማሽ ፡ ጎርዶ ፡ አስቀረበት ።
6 በዚህ ፡ አገር ፡ ጥጥና ፡ በርበሬ ፡ መሳ ፡ ለመሳ ፡ አይለወጥም ።

(ረ) የአዎንታና ፡ የአሉታ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡- መተማመንንና ፡ መተባባትን ፡ የሚያ መለክት ፡ ነው ።

አስረጅ ፡-

1 ነገሩን ፡ በርግጥ ፡ ዐውቀዋለሁ ።
2 በእውነት ፡ ታሞ ፡ ተኝቷል ።
3 እሺ ፡ እመጣለሁ ።
4 እንቢ ፡ አልሠራም ።

(ሰ) <u>የምክንያት ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡-</u> አንድ፣ ነገር ፡ የሚሠራበትን፣ ምክንያት፣ የሚያመለክት ፡ ነው ።

<u>አስረጅ ፡-</u> ስለዚህ ፡ በፍቅር ፡ ተባብረን ፡ እንሥራ ።

(ሸ) <u>አጠራጣሪ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡-</u>

<u>አስረጅ ፡-</u>

1 ምናልባት ፡ ይህ ፡ ሥራ ፡ በዚህ ፡ ሳምንት ፡ ውስጥ ፡ ያልቃል ።
2 አየለን ፡ አይተኸዋል ? ኧረ ፡ እንጃ ፡ አላየሁትም ።

<u>መጠይቅ ፡ ተዋሳከ ፡ ግሥ ፡</u>

መጠይቅ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ጥያቄን፣ ለማቅረቢያ፣ የሚሆን ፡ ተውሳከ ፡ ግስ፣ ነው።

<u>አስረጅ ፡-</u>

1 ወዴት ፡ ትሄዳለህ ? የቦታ ፡
2 መቼ ፡ ትጽፍለታለህ ? የጊዜ ፡
3 ከእርሱ ፡ ጋራ ፡ ለምን ፡ ትጣላለህ ? የምክንያት ፡
4 አንተ ፡ ልጅ ፡ እንዴት ፡ ሰውን ፡ ትደፍራለህ ? የመጠን ፡
5 በዚህ ፡ አገር ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ይቀመጣል ? የጊዜ ፡
6 ልጁ ፡ ስንትዬ ፡ በደለው ? የቍጥር ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡

## ፱ ፡ የተውሳከ ፡ ግስ ፡ አመዳደብ ፡

<u>ቃላት ፡</u> ከልዩ ፡ ልዩ ፡ መስተዋድዳን ፡ ጋራ ፡ ባንድነት ፡ ገብተው ፡ ሁለቱ ፡ እንዳንዱ ፡ ቃል ፡ ስለሚሠሩ ፡ መስተዋድዶቹ ፡ እንደ ፡ ባዕድ ፡ መነሻዎች ፡ ተቈጥረዋል ፡ እንጂ ፡ በእውነተኛው ፡ ባዕድ ፡ መነሻዎች ፡ አይደሉም ። ነገር ፡ ግን ፡ እንዲሁ ፡ ብንቀበላቸው ፡ ስለማያጎዱ ፡ እንደ ፡ ተለመደው ፡ ጽፌያቸዋለሁ ። አብዛኛውን፣ በስተመነሻ፣ የሚገቡት ፡ የሚከተሉት ፡ ናቸው ።

(ሀ) ለ—ለክርሞው ፡ ብቻ ፡ ማሰብ ፡ በቂ ፡ አይደለም ።
በ—ልጁ ፡ በዝንጋታ ፡ መጥረቢያውን ፡ አስወሰደው ።
ከ—ከዚያ ፡ አንሥተህ ፡ ውሰደው ።
ወደ—ወደዚያ ፡ አትሂድ ።

ወደ ፡ ላይ ፡ ተመልከት ።
ወደ ፡ ፊት ፡ አስተምርሃለሁ ።

(ለ) ከመስተዋድድ ፡ ክፍል ፡ ሳይሆን ፡ ከተወሰነ ፡ አመልካች ፡ ክፍል ፡ የሆኑ ፡ ባዕድ ፡ መድረሻዎች ፡ አሉ ። እነርሱም ፡ ኑ ፡ ን ፡ ናቸው ።

ኑ—ያኔውኑ ፡ ብትመለስ ፡ ኖሮ ፡ ታገኝ ፡ ነበር ።
ን—እደር ፡ ብዬ ፡ ብለምነው ፡ እንቢ ፡ አለና ፡ ማታውን ፡ (ኑ) ተሳፈረ ።

(ሐ) ተደጋጋሚና ፡ ተጫፋሪ ፡ ተውሳከ ፡ ግስንም ፡ በዚሁ ፡ ክፍል ፡ መድቤዋለሁ ።

ዛሬና ፡ ነገ ፡ አባትህ ፡ ሳሉልህ ፡ ማን ፡ ይነካሃል ?
ጧትና ፡ ማታ ፡ ተመላልሼ ፡ አልዘልቀውም ።
ጧት ፡ ጧት ፡ ጅምናስቲክን ፡ እሠራለሁ ።
ፈለቀ ፡ ወዲህና ፡ ወዲያ ፡ ይወላገዳል ።

## ፫ ፡ አወዳዳሪ፡ ተውሳከ፡ ግስ ፡

አወዳዳሪ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡- ማነጻጸርን፡ ማብለጥንና፡ ማበላለጥን ፡ የሚያሳይ ፡ ነው።

አስረጅ ፡-

1 መንግሥቱ ፡ በፍጥነት ፡ ይሠራል ።
2 መንግሥቱ ፡ በጣም ፡ በፍጥነት ፡ ይሠራል ።
3 መንግሥቱ ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ በፍጥነት ፡ ይሠራል ።

## ፬ ፡ የተውሳከ ፡ ግስ ፡ አገባብ ፡

ተውሳከ ፡ ግስ ፡ የሚገልጻቸውን ፡ ቃላት ፡ ተከትሎ ፡ የገባ ፡ እንደሆን ፡ በተከታይነት ፡ ያገለግላል ።

ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ከመሆን ፡ ግስ ፡ ጋራ ፡ የገባ ፡ እንደሆን ፡ መሙሊያ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ነው ። እንግዴህ ፡ እንደ ፡ ቅጽል ፡ በቂና፡ ተከታይ ፡ ሊሆን ፡ ይችላል፡ ማለት፡ ነው።

አስረጅ ፡- 1 በፍጥነት ፡ ሰጠው ። } ተበታይ ፡
2. ልጁ ፡ ዘወትር ፡ ይማግጣል ።
3 ክፉኛ ፡ ይሮጣል ።

4 የልጁ፡ አጥፊነት ፡ አንድና ፡ ሁለት ፡ ሳይባል ፡ ዘወትር ፡ ነው። በቂ ፡ አንዳንድ ቃላት ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ሌላ ፡ ጊዜ ፡ ደግሞ ፡ ሌላ ፡ ነገር ፡ ይሆናሉ ።

አስረጅ ፡-

1 መላ ፡ መጣል ፡ ብቻ ፡ ታውቃለህ ።
2 ዋጋህን ፡ በሚገባ ፡ ታገኛለህ ፤ ብቻ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ አትበል ።
3 ልጁ ፡ ከመጣ ፡ ዝምሮ ፡ እስካሁን ፡ ደኅና ፡ ይሠራል ።
4 በዓለም ፡ ላይ ፡ ብዙ ፡ ደኅና ፡ ደኅና ፡ ሰዎች ፡ ሳይታወቁ ፡ ይኖራሉ ።
5 ልጁ ፡ የቱን ፡ ያህል ፡ አስቸገረ !
6 ዓርባ ፡ ልጆች፡ ያህል ፡ በኳስ ፡ ሜዳ ፡ ይገኛሉ ።
7 ከዚህ ፡ ዛፍ ፡ ሥር ፡ ጥቂት ፡ እንረፍ ።
8 ጥቂት ፡ ሰዎች ፡ ከወደ ፡ ላይ ፡ ሲመጡ ፡ አያለሁ ።

## ፩ ፡ የተውሳከ ፡ ግስ ፡ ዝርዝር ፡ አፈታት ፡

ተውሳከ ፡ ግስን ፡ ለመዘርዘር ፡ ማድረግ ፡ ያለብን ፡

1 ዐይነቱን ፡

(ሀ) ተውሳከ ፡ ግስ ፡ በሚሰጠው ፡ ትርጓሜ ፡ መሠረት ፡ የጊዜ ፡ የቦታ ፡ ያኳኋን ፡ የደረጃ ፡

(ለ) እንደ ፡ አገባቡ ፡ ቀላል ፡ መጠይቅ ፡

2 የማወዳደር ፡ ደረጃውን ፡- ተነጻጻሪ ፡ አብላጭ ፡ አበላላጭ ፡

3 ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ አገባቡ ፡- ግስን ፡ ተውሳከ ፡ ግስን ፡ ቅጽልን ፡ ንኡስ ፡ ሐረግንና ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግን ፡ እንደሚገልጽ ፤

አስረጅ ፡

1 ዛሬ ፡ አሞኛል ።

ዛሬ ፡- የዋህ ፡-የጊዜ ፡-ተነጻጻሪ ፡-ማሰሪያ ፡ አንቀጹን ፡ አሞኛልን ፡ ይገልጻል ።

2 ወንድሙ ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ በተመሥጦ ፡ ይጸልያል ።

እጅግ ፡ በጣም ፡- የደረጃ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ አበላላጭ ፡ የዋህ ፡ በተመሥጦን ፡ ይገልጻል።

በተመስጦ ፡ የዋህ ፡ ያኳኋን ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ተነጻጻሪ ፡ ደረጃ ፡ ይጸልያልን ፡ ይገልጻል ።

## ፳ኛ ፡ መልመጃ ፡

1 (ሀ) ተውሳከ ፡ ግስና ፡ ቅጽል ፡ በምን ፡ በምን ፡ ይመሳሰላሉ ?

(ለ) በምን ፡ በምንስ ፡ ይለያያሉ ?

2 በሚከተሉት ፡ የተውሳከ ፡ ግስ ፡ ዐይነቶች ፡ አንዳንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር፡ ሥራ።

(ሀ) ያኳኋን ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡

(ለ) የምክንያት ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡

(ሐ) ደረጃን ፡ የሚያሳይ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡

3 (ሀ) ተውሳከ ፡ ግስ ፡ የሚገልጻቸው ፡ ቃላት ፡ እነማን ፡ ናቸው ?

(ለ) በያንዳንዳቸው ፡ አንዳንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራና፡ የሠራህባቸውን፡ የተውሳከ ፡ ግስ ፡ ዐይነቶች ፡ አመልክት ።

4 በሚከተሉት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ የሚገኙትን ፡ ተውሳከ ፡ ግሶች ፡ በዝርዝር አፈታት ፡ ደንብ ፡ ዘርዝራቸው ።

(ሀ) ዘወትር ፡ ጧት ፡ ጧት ፡ እየተነሣሁ ፡ አጠናለሁ ።

(ለ) መኰንን ፡ ይህን ፡ ሥራ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ አሳይቶኛል

(ሐ) ጧት ና ፡ ማታ ፡ ራስ ፡ ምታት ፡ ይነሣብኛል ።

5 የማወዳደርን ፡ ደረጃ ፡ የሚያሳይ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ የማሳነስን ፡ ምግባር ፡ እን ዲገልጽ ፡ በሦስቱም ፡ ደረጃዎች ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሠርተህ ፡ አሳይ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ፡ መስተዋድድ ።

መስተዋድድ ፡ አስማሚ ፡ ወይም ፡ አዛማጅ ፡ ማለት ፡ ነው ። ከስምንቱ ፡ የንግ ግር ፡ ክፍሎች ፡ ውስጥ ፡ አምስቱ ፡ በባለቤትና ፡ ባንቀጽ ፡ ሥር ፡ እየተመደቡ ፡ ከሁለት ፡ ላይ ፡ ተከፍለው ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ይገባሉ ፤ መስተዋድድና ፡ መተስፃምር ፡ ግን ፡ በሁለቱም ፡ ክፍሎች ፡ ውስጥ ፡ ሲገቡ ፡ ይገኛሉ ። ቃለ ፡ አጋኖ ፡ በገዛ ፡ ራሱ ፡ የሚጸና ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከማንኛውም ፡ ክፍል ፡ ውስጥ ፡ አይገባም ። እንግዴህ ፡ መስተዋድድ ፡ ባረ ፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ከባለቤት ፡ ጋራ ፡ የሚገቡትን ፡ ስሞችና ፡ ከማስሪያ ፡ አንቀጽ ፡ ጋራ፡ የሚገቡትን ፡ ስሞች ፡ ያስማማል ።

የመስተዋድድ ፡ መግለጫ ፡- መስተዋድድ ፡ በስሞች ፡ በተውላጠ ፡ ስሞችና ፡ በስም ፡ መሰሎች ፡ ላይ ፡ እየተጫነ ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ የቃላትን ፡ ዝምድና ፡ የሚ ያመለክት ፡ ነው ።

### ፩ ፡ የመስተዋድድ ፡ ዐይነት ፡

የመስተዋድድ ፡ ዐይነቶች ፡ ሁለት ፡ ናቸው ።

(ሀ) ነጠላ ፡ አንድ ፡ ቃልን ፡ ወይም ፡ ቃላትን ፡ በመነሻና ፡ በመድረሻ ፡ ላይ ፡ ገብቶ ፡ ሳይከብ ፡ በመነሻ ፡ ላይ ፡ ብቻ ፡ ተጭኖ ፡ የቃላትን ፡ ዝምድና ፡ የሚያሳይ ፡ መስ ተዋድድ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

1 ቍልፉን ፡ በመዶሻ ፡ ሰበረው ።
2 የቅቤ ፡ ናዳ ፡ ይጨፍልቅህ ።
3 እንደ ፡ ጠጣ ፡ ብልኅ ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ደፋር ፡ ያድርግህ ።
4 ስላገራችን ፡ ቅር ፡ ሳይለን ፡ ሕይወታችንን ፡ እንሠዋለን ።

(ለ) ድርብ ፡- አንድ ፡ ቃልን ፡ ወይም ፡ ቃላትን ፡ በመነሻና ፡ በመድረሻ ፡ ላይ ፡ ተጭኖ ፡ (ገብቶ) ፡ የሚገዛ ፡ መስተዋድድ ፡ ነው ።

ቃልን ፡ በመካከል ፡ አድርገው ፡ የሚገዙ ፤

አስረጅ ፡

1 በቡሃ ፡ ላይ ፡ ቆረቆር ፡ ሲጨመርበት ፡ የራስን ፡ መልክ ፡ እንደሚያጠፋው ፡ በእንቅርትም ፡ ላይ ፡ ገሮ ፡ ደግፍ ፡ ሲጨመርበት ፡ በጣም ፡ ከማስከፋቱ ፡ ይልቅ፡ የጥፉ፡ ጥፉ ፡ ያደርጋል ።

2 በምድር ፡ ላይ ፡ መጠቅጠቅ ፡ በሰማይ ፡ መጠየቅን ፡ ያመጣል ።

3 በጌጠኛ ፡ አበባ ፡ ላይ ፡ ብዙ ፡ ንቦች ፡ ይተናነቃሉ ።

4 በመራራ ፡ ነገር ፡ እንጂ ፡ በማር ፡ ነገር ፡ ልቤ ፡ አይጨክንም ።

5 ከዛፉ ፡ ሥር ፡ ወፊቱ ፡ ቱር ፡ ብላ ፡ ተነሣች ።

6 ስለ ፡ ጥበብ ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ዋዘኞች ፡ ዘንድ ፡ ሄደን ፡ ብንጠይቅ ፡ ከስንፍናና ፡ ከግብዝነት ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ ነገርን ፡ አናገኝም ።

ሁለት ፡ መስተዋድዶች ፡ ባንድ ፡ ላይ ፡ ሆነው ፡ አንድ ፡ ቃልን ፡ ሲገዙ ፡

አስረጅ ፡

1 ወደ ፡ ላይ፡ መውጣት ፡ እንጂ ፡ ከወደ ፡ ላይ፡ ወደ፡ ታች፡ መውረድ፡ አያቅትም።

2 ከወደ ፡ ውጋዴን ፡ ሁለት ፡ አሞሮች ፡ እንዳንገጥበቡ ፡ መጡ ።

3 ከወደ ፡ ቆላ ፡ መጣን ።

## 2 የመስተዋድድ ፡ አገባብ ፡

የመስተዋድድ ፡ አገባብ ፡ የያንዳንዳቸውን ፡ ሙያ፡ ወይም፡ አገባብ ፡ የሚያመለክት ፡ ነው።

(ሀ) መገሥገሻ ፡- እነዚህ ፡ መስተዋድዶች ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ካንድ ፡ ቦታ ፡ ተነሥቶ ፡ ወዳንድ ፡ ቦታ ፡ መሄዱን ፡ የሚያመለክቱ ፡ ናቸው ። «እ» ና ፡ «ወደ» ፡ ናቸው ።

አስረጅ ፡

1 ከመንገዱ ፡ ሁሉ ፡ እቤቴ ፡ የሚወስደኝን ፡ እወዳለሁ ።

2 ብዙ ፡ አስተማሪዎች ፡ ለክረምት ፡ ትምህርት ፡ (ለኮርስ) ፡ ወዳዲስ ፡ አበባ ፡ ይሄዳሉ ።

(ለ) መድረሻ ፡- «እስከ—ድረስ» ፡ እነዚህ ፡ መስተዋድዶች ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ካንድ ፡ ቦታ ፡ ተነሥቶ ፡ ወዳንድ ፡ ቦታ ፡ መድረሱን ፡ የሚያመለክቱ ፡ ናቸው ።

አስረጅ ፡

1 እኔና ፡ ፈለቀ ፡ እስከ ፡ ለንደን ፡ ድረስ ፡ አብረን ፡ ሄድን ።

2 አቶ ፡ ፈለቀ ፡ ካዲስ ፡ አበባ ፡ እስከ ፡ ጅቡቲ ፡ ድረስ ፡ በባቡር ፡ ይሄዳሉ ፤ ከዚያ ፡ አንሥተው ፡ እስከ ፡ ፖርት ፡ ሳይድ ፡ ድረስ ፡ ግን ፡ በመርከብ ፡ ይጓዛሉ ።

(ሐ) አጫፋሪ፡- ባንድነት ፡ መሥራትን፡ እያመለከተ ፡ አኳኋንን ፡ የሚያሳይ ፡ መስተዋድድ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

1 በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ብዙ ፡ መኳንንት ፡ ካራዊት ፡ ጋራ ፡ በመጋደል ፡ ሕይወታቸውን ፡ አሳለፉ ።

2 ርኅራኄ ፡ የሌለው ፡ ሰው ፡ ከሕፃናት ፡ ጋራ ፡ ለመዋል ፡ አይችልም ።

(መ) ማንጸሪያ ፡

፩ ፡ ማመሳሰል፡- አንዱ ፡ ነገር ፡ ካንዱ ፡ ነገር ፡ ጋራ ፡ ተመሳስሎ ፡ ስሜቱ ፡ የሚ ገለጽበት ፡ መስተዋድድ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡- እንደ ፡ ፍል ፡ ውኃ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ይዘላል ።

፪ ፡ ማበላለጥ ፡- አንድ ፡ ነገር ፡ ካንድ፡ ነገር፡ ጋራ ፡ ተወዳድሮ፡ በመልካም ፡ ሆነ ፡ በመጥፎ ፡ ነገር ፡ ስሜቱ ፡ የሚገለጽበት ፡ መስተዋድድ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

1 ከሠሩ ፡ አይቀር ፡ እንደ ፡ ደጃዝማች ፡ መኰንን ፡ ደምሰው ፡ ሠርቶ ፡ ሙያን ፡ በታሪክ ፡ ዳኛ ፡ ፊት ፡ አስመስክሮ ፡ ስምን ፡ በዓለም ፡ ሐውልት ፡ ላይ ፡ መቅረጽ ፡ ነው ።

2 ደበበው ፡ እንደ ፡ ተሰማ ፡ በማናቸውም ፡ ነገር ፡ ዘሎ ፡ ጥልቅ፡ ማለትን ፡ እጅግ፡ በጣም ፡ ይጠላል ።

(ሠ) ማድረጊያ ፡

(ሀ) የምንሠራበትን ፡ ዕቃ ፡ ያሳየን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ማድረጊያ ፡ መስተዋድድ፡ ይባላል ።

አስረጅ ፡- ልጆቹ ፡ ድርሰታቸውን ፡ በቀለም ፡ ጻፉ ።

(ለ) ጊዜን ፡ የሚያመለክቱ ፡ ስሞችን ፡ የገዛ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የጊዜ ፡ መስተዋ ድድ ፡ ይሆናል ።

አስረጅ ፡- ቢቻለው ፡ በስድስት ፡ ሰዓት ፡ ይመለሳል ።

(ሐ) ቦታን ፡ በሚያመለክቱ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ የተጫነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የቦታ ፡ መስተዋድድ ፡ ይሆናል ።

አስረጅ ፡- በማይ ፡ ጨው፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ የፈሰሰው ፡ ደም ፡ በኢጣሊያኖች ፡ እብሪት ፡ መሆ ኑን ፡ መላው ፡ ዓለም ፡ ይመሰክራል ።

(መ) በነገር ፡ ስም ፡ ላይ ፡ ሲጫን ፡ የአኳኋን ፡ መስተዋድድ ፡ ይሆናል ።

አስረጅ ፡- በደግነት ፡ ማንም ፡ አይተካከለውም ።

(ረ) የምክንያትና ፡ የአኳኋን ።

(ሀ) ምክንያቱን ፡ የሚያመለክት ፡ መስተዋድድ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡-ስለ ፡ አባቱ ፡ ጉዳይ ፡ ጠበቃ ፡ ለመግዛት ፡ ፈልጓል ።

(ለ) አኳኋንን ፡ ወይም ፡ ግብርን ፡ የሚያሳይ ፡ መስተዋድድ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡-ካንተ ፡ በስተቀር ፡ ሁሉም ፡ ትጉሆች ፡ ናቸው ።

(ሰ) አቀባይ ፡

አንድ ፡ ነገር ፡ ላንድ ፡ ሰው ፡ ወይም ፡ ላንድ ፡ እንስሳ ፡ መሰጠቱን ፡ የሚያመለ ክት ፡ ነው ።

አስረጅ ፡- ግርማዊ ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ባመት ፡ ባመቱ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ሽልማትን ፡ ለተማሪዎች ፡ ይሰጣሉ ።

(ሸ) ዘርፍ ፡ አያያዥ ፡

(ሀ) ባለገንዘብን ፡ የሚያመለክት ፡ መስተዋድድ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡- የሙላቱን ፡ መጽሐፍ ፡ አስጠረዝሁለት ።

(ለ) አንድ ፡ ዕቃ ፡ ከምን ፡ እንደ ፡ ተሠራ ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

አስረጅ ፡-የወርቅ ፡ ሰዓት ፡ ለጊዜው ፡ ቢያብለጨልጭ ፡ ለብዙ ፡ ጊዜ ፡ እንደማይቈይ ፡ ማሰብ ፡ ያስፈልጋል ።

(ሐ) ግብርን ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

አስረጅ ፡-የሹም ፡ ልል ፡ በጥፊ ፡ ያወላውላል ።

(መ) ዝምድናን ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

አስረጅ ፡ የወልደ ፡ ሥሉስ ፡ አባት ፡ ብሉይን ፡ አጠናቀው ፡ ያውቃሉ ።

(ሠ) ወገንነትን ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

አስረጅ ፡-የሕንድ ፡ ጠቅላይ ፡ ሚኒስትር ፡ የአሜሪካንን ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ ጎበኘ ።

ቀ) መነሻ ።

(ሀ) ጊዜን ፡ በሚያመለክቱ ፡ ስሞች ፡ ላይ ፡ በተጫነ ፡ ጊዜ ፡ የጊዜ ፡ መስተዋ ድድ ፡ የሚሆን ፡ ነው ።

አስረጅ ፡ -ከሰዓት ፡ በኋላ ፡ ትምህርትን ፡ አንማርም ።

(ለ) ካንድ ፡ ቦታ ፡ ወዳንድ ፡ ቦታ ፡ መሄድን ፡ የሚያመለክት ፡ የቦታ ፡ መስተ ዋድድ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡- ከሐረር ፡ በስምንት ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ተነሥተን ፡ ባሥር ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ድሬ ዳዋ ፡ ደረስን ።

፫ ፡ የመስተዋድዳን ፡ ንኡስ ፡ ሐረጎች ፡ ሙያ ፡

እንደ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡

አስረጅ ፡-በዛፉ ፡ ሥር ፡ ብዙ ፡ ከብቶች ፡ ተመስገዋል ።

ከቤቱ ፡ ቍንጮ ፡ ላይ ፡ ብዙ ፡ ወፎች ፡ ተነሡ።

አየለ ፡ ከባልንጀሮቹ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ለገሃር ፡ ሄደ ።

እንደ ፡ ቅጽል ፡

አስረጅ ፡- ባይሮፕላን ፡ ጣቢያ ፡ አጠገብ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ተሰበሰቡ ።

የብረት ፡ አልጋ ፡ ትፈልግ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ልሸጥልህ ።

የሰነፍ ፡ እጅ ፡ ከተዘረጋች ፡ በኋላ ፡ መታጠፍ ፡ ያቅታታል ።

፲ኛ ፡ መልመጃ ፡

፩ ፡ የሚከተሉትን ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ጕድለት ፡ በተሰማሚ ፡ መስተዋድዳን ፡ ሙላቸው ።

1 ወርቁ ፡ - - - ሽርሽር ፡ - - - - - አዲስ ፡ አበባ ፡ ሄደ ።
2 እርሱ ፡ - - - አዲስ ፡ አበባ ፡ ከተመለሰ ፡ ከአባቱ ፡ - - - መሥራት ፡ አልፈቀደም ።
3 - - - - - -ቤታችን ፡ - - - ያለውን ፡ መስክ ፡ - - -ሰው ፡ አከራየሁት ።
4 ------እዚህ ፡ ----አባታቸው ፡ ------እጁ ፡ አውጥቶት ፡ አያውቅም ።
5 ስለዚህ ፡ -------ወርቁ ፡ -------ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ተቸግረዋል ።

፪ ፡ መስተዋድዳውያንን ፡ እየለቀምህ ፡ አውጣ ።

1 የእንግሊዝ ፡ ቋንቋ ፡ ባገራችን ፡ የዕውቀት ፡ በር ፡ መክፈቻ ፡ ነው ።
2 በዚህ ፡ አኳኋን ፡ ሰው ፡ እንዴት ፡ አድርጎ ፡ ጤንነቱን ፡ ይጠብቃል ?
3 ቀይ ፡ ፈረስ ፡ ላይን ፡ ያስደስታል ።
4 ሦስት ፡ መቶ ፡ ልጆች ፡ ያህል ፡ ለሁለተኛ ፡ ደረጃ ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ ታጭተዋል ።
5 አያሌ ፡ ተማሪዎች ፡ በሚመጣው ፡ ዓመት ፡ ይመረቃሉ ።
6 እነዚህ ፡ ወጣቶች ፡ በችግኝ ፡ ይመሰላሉ ።

፫ የሚከተሉትን ፡ ንኡስ ፡ ሐረጎች ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ አስገባቸው ።

1 በጠቋሚ ፡ ተይዞ ፡
2 ኩልኩልትን ፡ ካገር ፡ ላይ ፡ ለማጥፋት ፡
3 የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እድሞ ፡

፲፩ኛ ፡ ተጨማሪ ፡ መልመጃ ፡

ግርማዊነታቸው ፡ የብፁዕ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስን ፡ ሐውልት ፡ ሲያቆሙ ፡ የተናገሩት ፡ ቃል ፡

ከዛሬ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ በፊት ፡ ጭንቅና ፡ ሥቃይ ፡ እየታየ ፡ የሰው ፡ ልብ ፡ እንደ ፡ ጦር ፡ በሚወጋ ፡ ኀዘን ፡ በተዋለበት ፡ ቦታ ፡ ለተሰበሰበ ፡ ሕዝባችን ፡ ስንናገር ፡ የደስታና ፡ የኀዘን ፡ አሳብ ፡ ለኛ ፡ እንደሚሰማን ፡ ለሁላችሁም ፡ መሰማቱ ፡ ርግጥ ፡ ነው ።

ሰው ፡ ለደኅንነትም ፡ ለጥፋትም ፡ ምክንያት ፡ ሆኖ ፡ ሕይወቱ ፡ በሚገኝበት ፡ ዘመን ፡ ይነስ ፡ ይደግ ፡ እንጂ ፡ ሲያንስ ፡ በገንዘቡና ፡ በጕልበቱ ፡ ሲበዛ ፡ በሕይወቱ ፡ በመሥዋዕትነት ፡ እስከ ፡ መስጠት ፡ ሲደርስ ፡ የሚታይ ፡ ነው ።

በሁለቱም ፡ ረገድ ፡ የሚሰጠው ፡ መሥዋዕትነት ፡ ለሚገምት ፡ ልብ ፡ አሳዛኝ ፡ ሳይሆን ፡ አያልፍም ። ለደኅንነትም ፡ ለጥፋትም ፡ የሚሰጥ ፡ መሥዋዕትነት ፡ አሳዛኝ ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ ለመዠመሪያው ፡ የሚደረገው ፡ በጎ ፡ ፈቃድን ፡ በመግዛት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከዕለት ፡ ጠቃሚነቱ ፡ በቀር ፡ ለትውልድ ፡ ሥራት ፡ ለታሪክ ፡ ገናናነት ፡ የሚሰጥ ፡ ነውና ፡ ይህን ፡ ለመመልከት ፡ ለበቃ ፡ ኀዘኑ ፡ በደስታ ፡ የሚለወጥ ፡ በመሆኑ ፡ ኀዘንም ፡ ደስታም ፡ ይሰማናል ።

የዛሬ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ በዚሁ ፡ ቀን የኢትዮጵያ ፡ ምሥራቅ ፡ ጳጳስ ፡ የነበሩት ፡ ብፁዕ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ለግፈኛው ፡ ጠላት ፡ አትገዙ ፡ ስለ ፡ ነጻነታችሁ ፡ ተከላከሉ ፤ ነጻነታችሁ ፡ ከሚረክስ ፡ ሙታችሁ ፡ ስማችሁ ፡ ቢቀደስ ፡ ታላቅ ፡ ዋጋ ፡ ያለው ፡ ክብር ፡ ታገኛላችሁ ፡ ብለው ፡ ባርበኞቻችን ፡ መካከል ፡ ሆነው ፡ ስላወገዙ ፡ የፋሺስት ፡ መንግሥት ፡ ወኪል ፡ ጨካኙ ፡ ዤኔራል ፡ ግራዚያኒ ፡ በዚሁ ፡ ቦታ ፡ በመትረየስ ፡ አስደበደባቸው ።

ኢትዮጵያን ፡ ለመውረር ፡ መጥቶ ፡ የነበረው ፡ ፋሺስት ፡ በሙሉ ፡ ዓለም ፡ የሕዝባችንን ፡ ስም ፡ ሲያጠፋ ፡ ጨካኝና ፡ ግፈኛ ፡ እያስመሰለ ፡ ሲሰብክ ፡ ነበር ። ከኢትዮጵያውያንና ፡ ከኢጣሊያኖች ፡ ማንኛቸው ፡ ግፈኛና ፡ ጨካኝ ፡ እንደ፡ሆኑ ፡ ይታወቅ ፡ ዘንድ ፡ በዓለም ፡ ፍርድ ፡ ፊት ፡ ሊመዛዘን ፡ ቻለ ። ሁለቱም ፡ ወገኖች ፡ የተፈተኑባቸው ፡ ዓመታት ፡ በቅርብ ፡ አለፉ ። ይህም ፡ የዛሬ ፡ ቀን ፡ መታሰቢያ ፡ አንደኛው ፡ ዋና ፡ ምስክር ፡ ነው ።

ብፁዕ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ የመጨረሻው ፡ ትንፋሻቸው ፡ «የኢትዮጵያ ፡ መሬት፡ ጠላት ፡ ብትቀበዪ ፡ የተረገምሽ ፡ ሁኚ» ፡ ሲል ፡ ሞታቸውን ፡ ባረከ ። ይህም ፡ የማይሞት ፡ ቃል ፡ እስከ ፡ ምጽአት ፡ መምህር፡ ነው ። ይህንም ፡ ሕያው ፡ የሆነ ፡ ቃል ፡ ተናግረው ፡ ወደ ፡ ተጠሩበት ፡ ሠርግ ፡ ቤት ፡ ለመሄድ ፡ የሰማዕትነት ፡ ጽዋቸውን ፡ ተቀበሉ ።

ኢትዮጵያም ፡ የብፁዕ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስን ፡ የመጨረሻ ፡ ውግዘት ፡ አክብራ ፡ ላደራ ፡ የበቃች ፡ ሁና ፡ ተገኘች ።

በዕረፍት ፡ ከተቀበለቻቸው ፡ ልጆቿ ፡ በቀር ፡ እንሆ ፡ ጠላትን ፡ አስወጥታ ፡ የተበታተኑትን ፡ ልጆቿን ፡ ሰብስባ ፡ በእልልታና ፡ በደስታ ፡ ተቀበለች ።

በዚህ ፡ ቦታ ፡ የፈሰሰው ፡ የብፁዕ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ንጹሕ፡ ደም ፡ ባለማቋረጥ፡ ስለ ፡ ነጻነት ፡ ሲጮህ ፡ ቈይቶ ፡ ዛሬ ፡ መበቀሉን ፡ አየ ።

የብፁዕ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ደም ፡ በብዙ ፡ ወገን ፡ አፍርቷል ። «ነፍሳችሁን ፡ ለመግደል ፡ አይችልምና ፡ ሥጋችሁን ፡ የሚገድለውን ፡ አትፍሩ » ያለውን ፡ የወንጌል ፡ ቃል ፡ ተከትለው ፡ ሞትን ፡ በመናቅና የጨካኞችን ፡ ግርማ ፡ ባለመፍራት ፡ የጻድቅ ፡ ሞታቸውን ፡ ሕይወት ፡ በማድረጋቸው ፤ የተከተሏቸውና ፡ ስለ ፡ ሀገራቸው ፡ የተሠዉ ፡ ጀግኖች ፡ቍጥር ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ነው ፤ የነርሱንም፡መታሰቢያ፡የምንዘነጋው፡አይደለም።

ብፁዕ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ በሰማዕትነት ፡ ባረፉበት ፡ በደማቸው ፡ በከበሩበት ፡ በዚህ ፡ ስፍራ ፡ ለዘለዓለም ፡ ስማቸው ፡ ሲጠራ ፡ እንዲኖር ፡ የሐውልት ፡ መታሰቢያ ፡ ዛሬ ፡ አቁመንላቸዋል ።

የዳግማዊ ፡ ምኒልክ ፡ ሐውልት ፡ ከቆመበት ፡ ስፍራ ፡ ዝምሮ ፡ በሐውልታቸው ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ የሚወርደውን ፡ መንገድ ፡ የጴጥሮስ ፡ጐዳና ፡ ብለን ፡ ሰይመነዋል።

## ጴጥሮስ ፡ ስምህ ፡ የማይሞት ፡ ሕያው ፡ ነው ።

ይህ ፡ ሐውልት ፡ የብፁዕ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስን ፡ ስምና ፡ ታሪክ ፡ ያስተባብራል ። አንተ ፡ መሠረት ፡ ነህ ፡ ባንተ ፡ መሠረትነት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ አንጻለሁ ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ለብፁዕ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ መታሰቢያ ፡ የምናቆመው ፡ ሐውልት ፡ ስለ፡ ሀገራቸው ፡ የተሠዉ ፡ ኢትዮጵያውያን ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ለሚቆምላቸው ፡ መታሰቢያ ፡ እንደ ፡ መዠመሪያ ፡ መሠረት ፡ አድርገን ፡ እንቈጥረዋለን ።

1 ከምንባቡ ፡ ውስጥ ፡ ንኡስ ፡ ሐረጎችን ፡ እየለቀምህ ፡ ጻፍ ።

2 ለቅመህ ፡ ያወጣሃቸውን ፡ ንኡስ ፡ ሐረጎች ፡ አገባብ ፡ ተናገር ።

3 ከምንባቡ ፡ ውስጥ ፡ «ወደ ፡ ተጠሩበት ፡ ሠርግ ፡ ቤት ፡ ለመሄድ ፡ የሰማዕትነት ፡ ጽዋቸውን ፡ ተቀበሉ» ፡ የሚለውን ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ አስፋፍተህ ፡ አስረዳ ።

4 ከምንባቡ ፡ ውስጥ ፡ ሕገኛ ፡ ቅጽሎችን ፡ ልቀምና ፡ ክፍላቸውን ፡ አመልክት።

5 የሚከተሉትን ፡ ተርጕማቸው ። (1) ሰማዕት፡ (2) መሥዋዕት ፡ (3) መታሰቢያ ፡ (4) ውግዘት ፡ (5)ነጻነት ፡ (6)ኩራት ፡ (7) ንጹሕ ፡ ደም ፡ (8) መበቀል፡

6 አርበኛ ፡ የሚለውን ፡ ቃል ፡ በሰፊው ፡ ግለጸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፻ ፡ መስተፃምር ።

መስተፃምር ፡ ቃላት ፡ ልብስን ፡ በየደረጃቸው ፡ እያደረገ ፡ ሊያያዙ ፡ ከሚገባቸው ፡ ቃላት ፡ ልብስ ፡ ጋራ ፡ በየፈርጃቸው ፡ የሚሰፋቸው ፡ መርፌ ፡ ነው ።

መስተፃምር ፡ በሰው ፡ ሠራሽ ፡ ሙጫ ፡ ይመሰላል ። ሰው ፡ ሠራሽ፡ ሙጫ፡ጠንካራ ፡ ከነጭነት ፡ ወደ ፡ ቡና ፡ ዐይነት ፡ የሚያመዝን ፡ በውኃ ፡ ተበጥብጦ ፡ ዝልግልግ ፡ ፈሳሽ ፡ የሚሆን ፡ ከዕንጨት ፡ የሚሠሩ ፡ ነገሮችንና ፡ ከዕንጨት ፡ ዱቄት ፡ ወይም ፡ ገለባ፡ የሚሠሩትን ፡ የሚያያይዝ ፡ ሰው ፡ ሠራሽ ፡ ሣንቃን ፡ አጥብቆ ፡ የሚለስቅ ፡ ሌሎችንም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ነገሮችን ፡ ለማጣመር ፡ የሚችል ፡ ከልዩ ፡ ልዩ ፡ ነገሮች ፡ የሚበጅ ፡ እንደ ፡ ሙጫ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ነው ።

አንድ ፡ ወንበር ፡ መዠመሪያ ፡ ሲገጠም ፡ ያለምስማር ፡ በሰው፡ ሠራሽ ፡ ሙጫ፡ ይጋጠማል ፤ ቀጥሎም ፡ በሚያስፈልግበት ፡ ቦታ ፡ ላይ ፡ እየታየ ፡ በምስማር፡ ይመታል። እንደዚሁም ፡ አንድ ፡ ጠረጴዛ ፡ ሲሠራ ፡ ከእግሮቹ ፡ ጋራ ፡ በምስማር ፡ ከመመታቱ ፡ በፊት ፡ እንደ ፡ ወንበሩ ፡ በሰው ፡ ሠራሽ ፡ ሙጫ ፡ ይጋጠማል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አልፎ ፡ አልፎ ፡ በምስማር ፡ ይመታል ። ወይም ፡ ሙጫ ፡ ብቻ ፡ በቂ፡ ሆኖ፡ያጠነክረዋል። በዚሁ፡ መንገድ ፡ ወረቀቶች ፡ ከወረቀቶች ፡ ጋራ ፡ ይጣበቃሉ ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ወረቀቶች፡ በማስታወቂያ ፡ ሣንቃ ፡ ላይ ፡ ይለጠፋሉ ።

መስተፃምር ፡ በሰው ፡ ሠራሽ ፡ ሙጫ ፡ የተመሰለበት ፡ ምክንያት ፡ ሰው ፡ ሠራሽ ፡ ሙጫ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ነገሮችን ፡ ለማያያዝ ፡ እንደሚችል ፡ መስተፃምርም ፡ በያገባቡ ፡ ልዩ ፡ ነገሮችን ፡ ለማቆራኘት ፡ በመቻሉ ፡ ነው ።

## መስተፃምር ፡ ሁለት ፡ ዋና ፡ ክፍሎች ፡ አሉት ።

ትክክለኛነት ፡ ያላቸውን፡ ነገሮች ፡ በማዕርግ ፡ በማዕርጋቸው ፡ እያደረገ፡ ይሰፋቸዋል ። እንደዚህም ፡ ማለት ፡ ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገርን ፡ ከነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ጋራ ፡ ድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገርን ፡ ከድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ወይም ፡ ከድርብርብ፡ አረፍተ፡ ነገር ፡ ጋራ ፡ ያጫፍራል ፡ ማለት ፡ ነው ። እንዲሁም ፡ ቃላትን ፡ ከቃላት ፡ ጋራ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግን ፡ ከንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ጋራ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግን ፡ ከጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ጋራ ፡ ያያይዛል ። እንግዴህ ፡ ትክክል ፡ የሆኑትን ፡ ነገሮች ፡ ያያይዛል ፡ የተባለበት ፡ ስለዚህ ፡ ነው ።

ሁለተኛው ፡ ዐይነት ፡ በጣም ፡ ሊገለጽ ፡ የሚያስፈልገው ፡ አይደለም ። እርሱም ጥገኛውን ፡ ሐረግ ፡ ከመደበኛው ፡ ሐረግ ፡ ሥር፡ ተጠግቶ ፡ እንዲያድር ፡ የሚያደርገው፡ መስተፃምር ፡ ነው ።

ሰው ፡ ሠራሽ ፡ ሙጫ ፡ ከልዩ ፡ ልዩ ፡ ነገሮች ፡ እንደሚሠራና ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ መንገድ ፡ ሰውን ፡ ባገልግሎቱ ፡ እንደሚጠቅመው ፡ ሁሉ ፡ መስተፃምር ፡ ከልዩ ፡ ልዩ ፡ ቃላት ፡ ተመሥርቶ ፡ ቃላትንና ፡ ሐረጎችን ፡ ለማያያዝ ፡ የሚጠቅም ፡ መሣሪያ ፡ ነው ።

## ፩ኛ ፡ ወደረኛ ፡ መስተፃምር ፡

ወደረኛ ፡ መስተፃምር ፡ እኩልነት ፡ ያላቸውን ፡ ነገሮች ፡ የሚያያይዝ ፡ መስተፃምር ፡ ነው ። አብዛኛውን ፡ጊዜ ፡ ወደረኛ ፡ መስተፃምር ፡ የሚያያይዛቸው ፡ የሚከተሉት፡ ናቸው ።

፩ ፡ ስምን ፡ —ስምንና ፡ ስምን ፡ { ጥሬ ፡ ዘር ፡ / ሳቢ ፡ ዘር ፡ / አርእስት ፡ }

፪ ፡ ተውላጠ ፡ ስምን፡—ተውላጠ ፡ ስምንና ፡ ተውላጠ ፡ ስምን ፡
፫ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግን ፡—ንኡስ ፡ ሐረግንና ፡ ንኡስ ፡ ሐረግን ፡
፬ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግን ፡—ጥገኛ ፡ ሐረግንና ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግን ፡
፭ ፡ አረፍተ ፡ ነገርን፡—አረፍተ ፡ ነገርንና ፡ አረፍተ ፡ ነገርን ፡
፮ ፡ ተውሳከ ፡ ግስን ፡—ተውሳከ ፡ ግስንና ፡ ተውሳከ ፡ ግስን ፡
፯ ፡ ቅጽልን፡—ቅጽልንና ፡ ቅጽልን ፡
፰ ፡ ቦዝን ፡—ቦዝንና ፡ ቦዝን ፡

አስረጅ ፡

፩ ፡ መብላትና ፡ መሥራት ፡ መብልና ፡ መጠጥ ፡ ክፉነትና ፡ ደግነት ፡ መንግሥቱና ፡ በለጠ ፡ በቀለ ፡ መንግሥቱና ፡ ደስታ ፡ በቀለም ፡

፩ ፡ አንቺና ፡ እርሷ ፡ እናንተና ፡ እኛ ፡ አንተና ፡ ተስፋዬ ፡
፫ ፡ በማደያው ፡ ላይና ፡ በመደቡ ፡ ላይ ፡ አፍሰሰው ።
፬ ፡ ሲጽፍና ፡ ሲናገር ፡
፭ ፡ ከእንግዴህ ፡ ወዲህ ፡ ፈለቀ ፡ አይደርስብህም ፤ ጫፍህንም ፡ አይነካውም ።
፮ ፡ ከዚህ ፡ መሬት ፡ ዓምናና ፡ ዘንድሮ ፡ አፈስሁለት ።
፯ ፡ አጭና ፡ ረዥም ፡
፰ ፡ አጥቦና ፡ ተኩሶ ፡

ወደረኛ ፡ መተስተፃምር ፡ ባራት ፡ ይከፈላል ፤ (አራት ፡ ዐይነቶች ፡ አሉት)።
(ሀ) አጫፋሪ፡—በሐሳብ ፡ የሚመሳሰሉ ፡ ነገሮችን ፡ የሚያያይዝ ፡ መስተፃምር ፡ ነው። አዳጋሚ ፡ በፊት ፡ የተነገረው ፡ መስተፃምር ፡ አልበቃ ፡ ሲል ፡ የሚጨመር ፡ ነው። አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ መተስተፃምሩም ፡ ባይደገም ፡ «ም» ፡ ራሱ ፡ አዳጋሚ ፡ መስተፃምር ፡ ነው፡ ይላሉ ። አዳጋሚ ፡ የሚባለው ፡ ቃል ፡ የተገኘው ፡ «አዳገመ» ፡ ከሚለው ፡ ግስ ፡ ነው ። አዳገመ ፡ ማለትም ፡ መዠመሪያ ፡ የተሠራው ፡ ሥራ ፡ አጥጋቢ ፡ ሳይሆን ፡ ቀርቶ ፡ እንደ፡ ገና ፡ እንዲሠራ ፡ ተደረገ ፡ ማለት ፡ ነው ። ለምሳሌ ፡ በቆላ ፡ አገር ፡ በተለይ ፡ ባንዳንድ ፡ ሥፍራዎች ፡ ማሽላ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ይታረማል ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ደግሞ ፡ ዳግሞሽ ፡ ይታረማል ። በዚህ ፡ ጊዜ ፡ መዠመሪያ ፡ የተደረገው ፡ ልፋት ፡ በቂ ፡ ስላልሆነ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ታረመ ፡ ማለት ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ባንድ ፡ ወደረኛ ፡ መስተፃምር ፡ ሲያያዙ ፡ መስተፃምሩ ፡ እንዴት ፡ አዳጋሚ ፡ ይባላል ? በፍጹም ፡ አዳጋሚ ፡ መባል፡ አይገባውም ።

ስለዚህ ፡ አንድ ፡ መስተፃምር ፡ አልበቃ ፡ ብሎ ፡ ሌላ ፡ መስተፃምር፡ በተጨመረ፡ ጊዜ ፡ ያው ፡ ራሱ ፡ አጫፋሪው ፡ መስተፃምር ፡ ተደገመ ፡ እንጂ ፤ በተለይ ፡ አዳጋሚ ፡ መስተፃምር ፡ አልተፈለገለትም ። የዚህ ፡ ክፍል ፡ ዋና ፡ ዋና ፡ መስተፃምሮች ፡-

ደግሞ ፡ ም ፡ በዚያውም ፡ ላይ ፡ ስ ፡ እንግዴህ ፡ ና ፡

<u>አስረጅ ፡</u>

1 አየለና ፡ መኰንን ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርቡላችኋል ፤ ወይዘሮ ፡ ፈለቀችም ፡ ጭምር ።
2 ብሥራትና ፡ አስካለ ፡ ወደ ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ ሄዱ ።
3 ጥላሁን ፡ እየነዘነዘ ፡ አስቸግሮኛል ፤ አንተ ፡ ደግሞ ።
4 ፈለቀን ፡ ድኅነት ፡ ተጫነው ፤ በዚያውም ፡ ላይ ፡ ሕመምተኛ ፡ ሆነ ፤ ኧረ ፡ እንግዴህ ምን ፡ ይበጀዋል ?
5 እባካችሁ ፡ ልጆች ፡ ፈለቀችንም ፡ ደሳለኝንም ፡ ምከሩልኝ ።
6 ዛሬ ፡ ከበደ ፡ ወዴት ፡ ይውላል ? ወደ ፡ ቆላ ፡ ወርዶ ፡ በርበሬ ፡ ሲኮተኩት ፡ ይውላል ፤ አንተስ ?
7 ሌቦች ፡ በሌሊት ፡ መጥተው ፡ ያቶ ፡ ፈለቀን ፡ ቤት ፡ አጥር ፡ ሰብረው ፡ ገቡና፡ በሬዎቹን ፡ ነዱበት ።

ማስረጃ ፡

ና ፡ የሚባለው ፡ መስተፃምር ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ባስረጅነት ፡ የገባ ፡ እንደ ሆነ ፡ ወደረኛ ፡ መተስፃምር ፡ መሆን ፡ አይገባውም ፤ ምክንያቱም ፡ ያንደኛው ፡ ሐረግ ፡ ስሜት ፡ በሁለተኛው ፡ ሐረግ ፡ ስለሚደገፍ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ለሀገራችን ፡ መድከም ፡ ይገባል ፤ ያለድካም ፡ ሀገር ፡ አትጠበቅምና ። እንሆ ፡ የአረፍተ ፡ ነገሩ ፡ ስሜት ፡ «ሀገር ፡ ያለድካም ፡ የማትጠበቅ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ለሀገራችን ፡ መድከም ፡ ይገባናል » ፡ ይላል ፤ ስለ ዚህ ፡ «ስለ» ፡ ን ፡ በሚያመለክትበት ፡ ጊዜ ፡ የግዴታ ፡ ጥገኛ ፡ መሆን ፡ አለበት ።

በ፪ኛው ፡ ቍጥር ፡ የተነገረው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ድርብ ፡ መሆን ፡ አለበት ፤ ምክንያቱም ፡ ሁለቱም ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ራሳቸውን ፡ የቻሉ ፡ በመሆናቸው ፡ ነው ።

ሌቦች ፡ በሌሊት ፡ መጥተው ፡ ያቶ ፡ ፈለቀን ፡ ቤት ፡ አጥር ፡ ሰብረው ፡ ገቡ ።

«ሌቦች ፡ ያቶ ፡ ፈለቀን ፡ በሬዎች ፡ ነዱበት» ፡ ቢል ፡ የአረፍተ ፡ ነገሮቹ ፡ ስሜት ፡ የተሟላ ፡ ነው ።

«ና» ፡ ከዚህ ፡ በላይ፡ እንደ ፡ ተጻፉት ፡ ያሉትን፡ አረፍተ፡ ነገሮች ፡ ያያያዘ፡ እንደ፡ ሆነ ፡ ወደረኛ ፡ መስተፃምር ፡ ይባላል ፡ እንጂ ፤ በጥገኛ ፡ መስተፃምር ፡ የተመሠረተ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ በቦዝ ፡ ክፍል ፡ የሚገባ ፡ ነው ፡ ተብሎ ፡ ሊነገር ፡ አይቻልም ።

(ለ) አማራጭ ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ከሁለት ፡ ወይም ፡ ከሦስት ፡ ከበለጡ ፡ ነገሮች ፡ ተማርጦ ፡ መሠራቱን ፡ ወይም ፡ መወሰዱን ፡ የሚያመለክት ፡ መስተፃምር ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

1 ዛሬ ፡ ብሄድ ፡ ርሱን ፡ ወይም ፡ ዳምጠውን ፡ በቢሮ ፡ አገኛለሁ ።

2 የምትልከው ፡ መቼ ፡ አጣህ ? ፈለቀን ፡ ወይም ፡ እንደሻውን ፡ ላክ ።

አንድ ፡ ሰው ፡ ዛሬ ፡ ወይም ፡ ነገ ፡ እመጣለሁ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ምቹ ፡ ጊዜ ፡ መምረ ጡን ፡ ያስረዳል ፡ እንጂ ፤ መወላወሉን ፡ አያስረዳም ። ስለዚህ ፡ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ መስ ተፃምር ፡ ባማራጭነት ፡ እንጂ ፡ በወላዋይነት ፡ አንጠራውም ።

(ሐ) አፍራሽ ፡ በፊት ፡ (መዠመሪያ)፡ የተነገረውን ፡ አሳብ፡ የሚቀጥለው፡ አሳብ፡ እንዲቃወመው ፡ ሲፈለግ ፡ የሚጨመር ፡ መስተፃምር ፡ ነው ። አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ የሚ ሠራባቸው ፡ መስተፃምሮች ፡-

ግን ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ቢሆንም ፡ ይሁን ፡ እንጂ ፡ ዳሩ ፡ ግን ፡ እንጂ ፡ ሆኖም ፡ ብሎም ፡

አስረጅ ፡

1 ፈለቀ ፡ ዘወትር ፡ መጽሐፍ ፡ ያነባል ፤ ርሱ ፡ ግን ፡ ከመላፋት ፡ በቀር ፡ ሥራ ፡ የለውም ።

2 እኔ ፡ እንኳ፡ ስንት፡ ጊዜ፡ መከርሁት፤ ነገር ፡ ግን ፡ ርሱ ፡ ምክር ፡ አይቀበልም።

3 ፈለቀ ፡ ሊምርህ ፡ ፈልጎ ፡ ነበር ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ የዋልክበትን ፡ ግፍ ፡ ሊረሳው ፡ አልቻለም ።

4 መክሰሩንስ ፡ ከስረሃል ፤ ግና ፡ ቢሆን ፡ ተስፋ ፡ መቍረጥ ፡ አይገባህም ።

5 ልጁ ፡ እንደ ፡ በደለኝ ፡ ሰው ፡ ነግሮኛል ፤ ይሁን፡ እንጂ ፡ ቂም ፡ አሊዝበትም ።

6 አንተ ፡ ሰንፈህ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ጠንክረህ ፡ ብትሠራ ፡ኖሮ ፡ እስካሁን ፡ ትጨ ርስ ፡ ነበር ።

7 አስማው ፡ ያሥቃየዋል ፤ ሆኖም ፡ ለክፉ ፡ አይሰጠውም ።

8 አቶ ፡ ማንደፍሮት ፡ የግዛውን ፡ ያህል ፡ በትምህርት ፡ ቤት ፡ አልቈየም ። የኔን ፡ ያህል ፡ እንጂ ።

9 መንግሥቱ ፡ ላንተ ፡ ቢል ፡ እንጂ ፡ ለኔ ፡ ሲል ፡ አልቈየም ።

10 ሥራ ፡ በመሥራት ፡ ይቃለላል ፡ እንጂ ፡ በወሬ ፡ አይበገርም ።

(መ) አሳብ ፡ ሰጭ ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ አስቀድሞ ፡ ከተነገረ ፡ በኋላ ፡ የሚቀጥ ለው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ማስረጃን ፡ ለመስጫ ፡ ወይም ፡ ተርጕሞ ፡ ለማስረጃ ፡ የሚጨመር፡ መስተፃምር ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ አሳብ ፡ ሰጭ ፡ መስተፃምር ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ እንዲህ ፡ ከሆነ፡ እንዲህ ፡ መሆን ፡ ይገባዋል ፡ ተብሎ ፡ ለመነገር ፡ ሲፈለግ ፡ የሚጨመር ፡ ነው ። አብዛ ኛውን ፡ ጊዜ ፡ የሚሠራባቸው ፡ መስተፃምሮች ፡ የሚከተሉት ፡ ናቸው ።

ስለዚህ ፡ እንዲህ ፡ ከሆነ ፡
ታዲያ ፡ ከዚህም ፡ የተነሣ ፡

<u>አስረጅ ፡</u>

1 አበበ ፡ በመድኀኔ ፡ ዓለም ፡ ፪ኛ ፡ ደረጃ ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ ባሥረኛው ፡ ክፍል ፡ በፈተና ፡ አንደኛ ፡ ሆነ ፤ ስለዚህ ፡ መንግሥት ፡ የሚያስፈልገውን ፡ ያህል ፡ ገን ዘብ ፡ ከፍሎ ፡ ወደ ፡ ኢንግላንድ ፡ ሊልከው ፡ ነው ።

2 በፈተና ፡ አንደኛ ፡ የሆነ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ወጭ ፡ አገር ፡ ይላካል ፤ እንዲህ ፡ ከሆነ ፡ (እንዲህ ፡ ከሆነማ) ፡ ሁላችንም ፡ ጠንክረን ፡ ማጥናት ፡ አለብን ።

3 ልጁ ፡ እንቅልፉን ፡ አጥቶ ፡ ሌት ፡ ከቀን ፡ (ሌሊት ፡ ከቀን)፡ ይሠራል ፤ ከዚ ህም ፡ የተነሣ ፡ በፈተና ፡ አንደኛ ፡ ሳይሆን ፡ አይቀርም ።

4 ወደ አዲስ ፡ አበባ ፡ የሚሄደው ፡ ባቡር ፡ ዛሬ ፡ በ፷ ፡ ሰዓት ፡ ይነሣል ፤ ታዲያ ፡ ዕቃህን ፡ ለማዘጋጀት ፡ ለምን ፡ ቸል ፡ ትላለህ ?

## <u>፪ኛ ፡ ጥገኛ ፡ መስተፃምር ፡</u>

ጥገኛ ፡ መስተፃምር ፡ ባንቀጽ ፡ ላይ ፡ እየተጫነ ፡ መደበኛውን ፡ ሐረግ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ እያደረገ ፡ ከሌላው ፡ መደበኛ ፡ ሐረግ ፡ ጋራ ፡ የሚያያይዝ ፡ መስተፃምር ፡ ነው ።

የጥገኛ ፡ መስተፃምር ፡ ዐይነቶች ፡ ብዙ ፡ ናቸው ፤ በጣም ፡ የተለመዱት ፡ ግን ፡ የሚከተሉት ፡ ናቸው ።

| | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|
| እንደ ፡ | የ | ከ | ምንም ፡ እንኳ፡—ቢ ፡ ወይም ፡ ቢ፡ስ፡ | | |
| እንዲ ፡ | የሚ | ና | እኮ ፡ | ቢ | ባ በ—ጊዜ ፡ |
| እንዳ ፡ | የማ | ቢ | ሲ | | ከ—በኋላ ፡ |
| የ-እንደ ፡ ሆነ ፡ | የም | ብ | ሳ | | ከ—ይልቅ፡ |
| እየ ፡ እ.የ ፡ | ስለ | ከ | ክ | እስከ፡—ድረስ፡ | |

<u>አስረጅ ፡</u>

1 ማናቸውም ፡ ተማሪ ፡ ተግቶ ፡ እንዲያጠና ፡ የጠበቀ ፡ አደራ ፡ ተጥሎበታል ።

2 ከራቀ ፡ ዘመድ ፡ ባዕዳዊ ፡ ጎረቤት ፡ ለችግር ፡ ጊዜ ፡ እንደሚደርስ፡ ርግጥ፡ነው።

3 በሠራኸው ፡ መጠን ፡ እከፍልሃለሁ ። ጥገኛው ፡ መስተፃምር ፡ ውስጠ ፡ ታዋቂው ፡ «የ» ነው ።

4 የሰው ፡ አጥር ፡ የሰረሰረ ፡ እንደ ፡ ሰረቀ ፡ ወይም ፡ እንደ ፡ ገደለ ፡ ያህል ፡ ይቈጠራል ።

5 ፈለቀ ፡ ሥራውን ፡ ከጨረሰ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ይሄዳል ።

6 ትናንትና ፡ ምሳ ፡ ሲበላ ፡ ተኝተህ ፡ ነበር ።

7 ይህ ፡ ነገር ፡ ጠበቃው ፡ እንዳመለከተው ፡ መፈጸሙ ፡ ነው ።

8 አገሪቱ ፡ በሀብት ፡ እንደምትበልጥ ፡ የተረጋገጠ ፡ ነው ።

ከብላቴን ፡ ጌታ ፡ ኅሩይ ፡ ወልደ ፡ ሥላሴ ፡ መጽሐፍ ፡ ከጥሩ ፡ ምንጭ ፡

## <u>የተጠቀሱ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡</u>

1 ካፊር ፡ ባሕርይ ፡ አልፎ ፡ የጠነከረው ፡ ሁሉ ፡ ነጭም ፡ ጥቍርም ፡ ወይም ፡ ሌላም ፡ ዐይነት ፡ በጠቅላላው ፡ ደንጊያ ፡ ይባላል ።

2 በጭራሽ ፡ ስማቸውን ፡ እንኳ ፡ የሚያውቅ ፡ አልነበረም ።

3. አልጫ ፡ የሆነውን ፡ ልብ ፡ በሃይማኖትና ፡ ባምልኮተ ፡ እግዚአብሔር ፡ አጣፈጡት ።

4 በክርስቶስ ፡ መሠረትነት ፡ የተሠራችው ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እንዳትወድቅ ፡ ደግፈው ፡ የያዙ ፡ ጠንካሮች ፡ አዕማድ ፡ እነዚህ ፡ ሐዋርያት ፡ ናቸው ።

5 በኃጢአት ፡ ጨለማ ፡ ውስጥ ፡ የነበረውን ፡ ያሕዛብን ፡ ልብ ፡ በንጽሕናና ፡ በቅድስና ፡ ብርሃን ፡ አበሩት ።

6 ያሕዛብን ምድር ፡ (ልብ) ፡ በዕርፈ ፡ መስቀል ፡ እያረሱ ፡ ከሰፊው ፡ ጎተራ ፡ ከወንጌል ፤ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ እያወጡ ፡ የዘሩ ፡ እነዚህ ፡ ሐዋርያት ፡ ናቸው ።

7 በጠነከረው ፡ መሬት ፡ ባሕዛብ ፡ ልብ ፡ ፍቅርንና ፡ ርኅራኄን ፡ እያፈሰሱ፡ የመረዳዳትንና ፡ የመተሳሰብን ፡ ተክል ፡ እንዲያበቅል ፡ አደረጉ ።

8 ከወደቁም ፡ በኋላ ፡ ዐይናቸውን ፡ አቅንተው ፡ ቢመለከቱ ፡ ከጌታችን ፡ በስተቀር ፡ ማንንም ፡ አላዩም ።

እንሆ ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ በስምንተኛው ፡ ቍጥር ፡ የተጻፈውን፡ ድብልቅ፡ አረፍተ፡ ነገር ፡ ነጣጥለን ፡ ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ እናደርጋቸዋለን ።

1 እነርሱ ፡ ወደቁ ።
2 ዐይናቸውን ፡ አቅንተው ፡ ተመለከቱ ።
3 ከጌታችን ፡ በቀር ፡ ማንንም ፡ አላዩም ።
ጥገኛ ፡ መስተፃምሮች ፡ —ከ—በኋላ ፡ ቢ ፡ ናቸው ።

እንሆ ፡ ሦስቱ ፡ ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ጥገኛና ፡ መደበኛ ፡ ሆነው ፡ በጥገኛ ፡ መስተፃምራን ፡ ይያያዛሉ ።

ከወደቁም ፡ በኋላ ፡ ዐይናቸውን ፡ አቅንተው ፡ ቢመለከቱ ፡ ከጌታችን ፡ በቀር ፡ ማንንም ፡ አላዩም ።

| ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ | መደበኛ ፡ ሐረግ ። |
|---|---|
| 1 ከወደቁም ፡ በኋላ ፡ | ከጌታችን ፡ በቀር ፡ ማንንም ፡ አላዩም ። |
| 2 ዐይናቸውን ፡ አቅንተው ፡ ቢመለከቱ ። | |

ስለ ፡ ጥገኛ ፡ መስተፃምር ፡ በጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ክፍል ፡ ተመልከት ።

## ፲፪ኛ ፡ መልመጃ ፡

(ሀ) የሚከተሉትን ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ጉድለት ፡ በወደረኛ ፡ መስተፃምር ፡ ብቻ ፡ ሙላ ።

1 ጌታሁን ፡ ----ተሾመ ፡ ውብሸት ፡ ----የሚሠሩት ፡ ያስደስታል ።
2 አሰፋ ፡ ---ወንድሙ ፡ ---- በሥራ ፡ ላይ ፡ ናቸው ።
3 ወርቅነህ ፡ ድክር ፡ እንግሊዝኛን ፡ ያውቃል ፤ ---አጥርቶ ፡ አይናገርም ።
4 ---ሂድ ፡---- ተቀመጥ ።
5 ዛሬ ፡ ---ነገ ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ይመጣልኛል ።
6 አንዳንድ ፡ ነጋዴዎች ፡ በዋጋ ፡ መውጣትና ፡ መውረድ ፡ ምክንያት ፡ ይከስራሉ ፤ ----ተስፋ ፡ ቈርጠው ፡ ሥራቸውን ፡ አይተውም ።
7 ግርማ ፡ ቀይ ፡ ነው ፤ ጉግሳ ፡ ----የቀይ ፡ ዳማ ፡ ነው ።
8 ሣህለ ፡ ማርያም ፡ ትምህርትን ፡ ለመቀበል ፡ ችሎታ ፡ አለው ፤ ----አእምሮውን ፡ ለማሠራት ፡ አይሞክርም ።
9 አባተ ፡ ፈጣን ፡ ልጅ ፡ ነው ፤ ----መልእክት ፡ አያስተካክልም ።

10 ሠላሳ ፡ ብር ፡ ስጠኝ ፡----እኔ ፡ ጉዳይህን ፡ እጨርስልሃለሁ ።

11 መኪናውን ፡ ለማሳደስ ፡ እንረዳሃለን፤----ተነሥቶ ፡ ጉዳይ ፡ ይሞላ ፡ አይመስለኝም ።

12 ደመቀ ፡ ---አበበ ፡ ተነፋፍቀዋል ፤ --------ሳይጠያየቁ ፡ አይቀሩም ።

13 አዲስ ፡ ---ቢሰውር ፡ ለመምጣት ፡ አስበው ፡ ነበር ፤ ----ምን ፡ ሆነው ፡ ቀሩ?

14 ከኛ ፡ በኩል ፡ አንድ ፡ ልጅ ፡ ጉድሏል ፤ ----- አንሄድም ።

(ለ) የሚከተሉትን ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች፡ ጉድለት ፡ በጥገኛ ፡ መስተፃምራን ፡ ብቻ ፡ ሙላ ።

1 አየለንና ፡ ፈለቀን ፡ ----መጡ ፡ ጠርቻቸዋለሁ ።

2 ጣሊያኖች ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ ያላገባብ ፡ ---አፈሡ፤----ፈጁት ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ወዳርበኞች ፡ ዘንድ ፡ ሄደው ፡ ተቀላቀሉ ።

3 ከዚህ ፡ ፈተና ፡ ---አላመልጥ ፡ ---ዐውቀው ፡ ለምን ፡ በከንቱ፡ ታታልለኛለህ?

4 ጉዳዬን ፡ ----ትፈጽምልኝ ፡ ውለታህን ፡ እከፍልሃለሁ ።

5 አቶ ፡ ፈለቀ ፡ በጠና ፡ ----ታመመ ፤ መናዘዝ ፡ አቅቶታል ።

6 አምስት ፡ ሺ ፡ ብር ፡ አግኝቼ ፡ --- ሆን --- አንድ ፡ ትልቅ ፡ ሱቅ ፡ እስካሁን ፡ ድረስ፡ ---ሠራሁ ፡ ነበር ።

7 መኰንን ፡ ይሠራ ፡ ----እንቅጠረው ።

8 -----ሠራ--- ----ይሠራ ፡ ----ይምጣና ፡ ይቀመጥ ።

9 ከሦስት ፡ ሰዓት ፡ አንሥቼ ፡ -----ሄድ ፡ ---አጠናለሁ ።

10 እባህክ ፡ ልጄ ፡ ሆይ፡ ----ትናገር ፡ አትቸኵል ።

11 ነገሩ ፡ እኔ ፡ -----አሰብሁት ፡ አልተፈጸመም ።

12 --------ቸግረኝ ፡ በቅሎዬን ፡ አልሸጣትም ።

13 እኔ ፡ -----ታመም ፡ እርሳቸው ፡ ቢታመሙ ፡ ይፈቅዳሉ ።

14 ------ትሄድ ፡ አሳሰበኝ ።

## ፲፫ኛ ፡ ተጨማሪ ፡ መልመጃ ፡

## አትክልትና ፡ አረም ፡

አንድ ፡ ሰው ፡ ከቤቱ ፡ አጠገብ ፡ አንድ ፡ ሰፊ ፡ ያትክልት ፡ ቦታ ፡ አሰናድቶ ፡ መሬቱን ፡ ቆፍሮ ፡ ዐፈሩን ፡ ካለሰለሰ ፡ በኋላ ፡ የሚያምር ፡ መልክና ፡ የሚጣፍጥ ፡ መዐዛ ፡ ያለው ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ዘርን ፡ ፈልጎ ፡ አበባ ፡ ዘራበት ። ጧት ፡ ተነሥቶ ፡ ማታም፡ ፀሐይ ፡ ሳትጠልቅ ፡ ቀደም ፡ ብሎ ፡ ውኃ ፡ እየቀዳ ፡ አትክልቱን ፡ ያጠጣል ። አበባው ፡ አብቦ ፡ የሚባላውም ፡ ለምልሞ፡ ለመንፈሱ፡ ደስታ፡ ለሥጋውም፡ ጥቅም፡ የሚያገኝበት፡ ጊዜ፡ ደርሶ፡ ድካሙን፡ ለመርሳት ፡ ሰውዬው፡ በጣም፡ ይጓጓ፡ ነበር። ነገር፡ ግን፡ የዘራው፡

መልካም ፡ ዘር ፡ ገና ፡ ብቅ ፡ ብቅ ፡ ሲል ፡ ብዙ ፡ ሀይነት ፡ ሣርና ፡ ቅጠል ፡ በመካከሉ ፡ ችፍ ፡ ብሎ ፡ እየበቀለ ፡ አትክልቱን ፡ በመልካም ፡ አበቃቀል ፡ እንዳይወጣ ፡ ከለከለው ።

ሰውዬው ፡ ግን ፡ ካትክልቱ ፡ ጋራ ፡ ተቀላቅሎ ፡ የወጣውን ፡ መጥፎ ፡ አረም ፡ ለማጥፋት ፡ ሲል ፡ ከጧት ፡ ዠምሮ ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ ይሠራል ። በቀን ፡ ብዛት ፡ አረሙ ፡ መጥፋቱ ፡ ቀርቶ ፡ እያደር ፡ እየበረከተ ፡ ይሄድ ፡ ዠመር ። አሁንም ፡ ተስፋ ፡ ሳይቆርጥ ፡ በብዙ ፡ ሲታገል ፡ ቆየ ፤ በመጨረሻው ፡ ያትክልቱን፡ ቦታ ፡ አረሙ ፡ በሙሉ፡ አለበሰው ። ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ሰውዬው ፡ እንደ ፡ ተሸነፈ ፡ ስተለ ፡ ረዳው ፡ « ለካ ! የደከምሁት ፡ በከንቱ ፡ ኖሯል ። እግዚአብሔር ፡ ሥራውን ፡ ካልባረከለት ፡ ሰው ፡ ምንም ፡ ቢለፋ ፡ ፍሬ ፡ አያገኝበትም ። ሐዘኔና ፡ ጸጸቴ ፡ እጅግ ፡ የበረታ ፡ ሆኖ ፡ ለልቤ ፡ በጣም ፡ ተሰማው ። ደስታዬ ፡ ከእኔ ፡ አልፎ ፡ ለወዳጆቼ ፡ ይተርፋል ፡ ብዬ ፡ ለተስፋዬ ፡ ወሰን ፡ አልነበረውም ። አሁን ፡ ግን ፡ የድካሜ ፡ ዋጋ ፡ ላይን ፡ ደስ ፡ የማያሰኝና ፡ ለምንም ፡ የማይጠቅም ፡ መጥፎ ፡ አረም ፡ ብቻ ፡ ሆኖ ፡ አገኘሁት» ፡ ብሎ ፡ እንባውን ፡ አፍስሶ ፡ ቀረ ።

ከበደ ፡ ሚካኤል ።

## ከምንባቡ ፡ ውስጥ ፡ የወጡ ፡ ጥያቄዎች ፡

1 ወደረኛ ፡ መስተፃምሮችን ፡ ልቀምና ፡ ጻፍ ፤ ክፍላቸውንም ፡ አመልክት ።
2 ባትክልት ፡ የተመሰሉት ፡ እነማን ፡ ናቸው ?
3 አረም ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በሰፊው ፡ አስረዳ ።
4 ንኡስ፡ ሐረጎቹንና ፡ ጥገኛ፡ ሐረጎቹን፡ እየለቀምህ፡ በያይነታቸው፡ አመልክት።
5 እግዚአብሔር ፡ ሥራውን ፡ ካልባረከለት ፡ ሰው ፡ ምንም ፡ ቢለፋ ፡ ፍሬ ፡ አያገኝበትም ፡ የሚለውን ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ በተቻለህ ፡ መጠን ፡ ግለጸው ።
6 የሚከተሉትን ፡ መስተፃምራን ፡ ባረፍተ ፡ ነገሮች ፡ አስገባቸው ።
ይሁን፡ እንጂ፡ ነገር፡ ግን ፡ ከዚህም፡ የተነሣ ፡ ና፡ ወይም፡ ምንም፡ እንኳ ፡—ቢ፡ እንደ ፡ -የ-እንደ ፡ ሆነ ፡ እስከ ፡ ስለ ፡
7 አትክልታችን ፡ እንዲፋፋልን ፡ ምን ፡ ማድረግ ፡ ይገባናል -?
8 በወደረኛና ፡ በጥገኛ ፡ መስተፃምራን ፡ መካከል ፡ ምን ፡ ልዩነት ፡ አለ ?

## ምዕራፍ ፡ ፳ ፡ ቃለ ፡ አጋኖ ።

አንዳች ፡ ነገር ፡ ስሜት፡ እንዲሰጥ ፡ የፈለግን፡ እንደ፡ሆነ፡ ነገሩን፡ በተለየ፡ ድምፅ ፡ ከበድ ፡ አድርገን ፡ እንገልጸዋለን ። ቃለ ፡ አጋኖ ፡ ከሌሎቹ ፡ የንግግር ፡ ክፍሎች ፡ ጋራ፡ የታወቀ ፡ ዝምድና ፡ የለውም ።

እንግዴህ ፡ ቃለ ፡ አጋኖ ፡ በገዛ ፡ ራሱ ፡ የሚጸና ፡ የሌሎቹን ፡ ዝምድና ፡ የማይፈልግ ፡ ቃል ፡ ነው ።

ቃለ ፡ አጋኖ ፡ በሚከተሉት ፡ ዐይነቶች ፡ ይነገራል ።

1 ድንጋጤ፡—ውይ!ዘራፍ! የጠቅል ፡ አሽከር ! ወድቀህ ፡ ተነሣ ! ዋይ ! ወይኛ

2 መገረም፡—ግሩም! ጉድ ፡ ፈልቶ ! ጉድ! አዬ ፡ ጉድ !

3 ደስታ፡—የምሥራች ! እንኳን ፡ ደስ ፡ አለህ ! ቤት፡ ለምቦሳ ! ሹመት ፡ ያዳብር!

4 ትካዜ፡—አሌሔ ! እህህ ! አዬ ፡ ጉድ ! ወዮ ! ወዮልኝ !

5 ዛቻ፡—ቆይ ፡ ብቻ ! ወዮልህ ! ወዶት ፡ ትገባ ፡ ይሆን !

6 ማኅላመስ፡—ኀሽ ! አበጀህ ! ያሳድግህ ! ወሰው !

ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥም ፡ ይነገራል ።

1 ግሩም ፡ ነው ፡ እኮ ፡ በል ! ማን ፡ እንዲህ ፡ አድርጎ ፡ አሳየህ !

2 አይዞህ ! እንደ ፡ ሥራህ ፡ መጠን ፡ ዋጋህን ፡ እከፍልሃለሁ ።

3 ይህ ፡ ልጅ ፡ ምንዬ ፡ ተምሮ ፡ እዚህ ፡ ደረሰ !

4 እንደ ፡ ምን ፡ አድርጌ ፡ ይህን ፡ ቀንበር ፡ ከትከሻዬ ፡ ላይ ፡ አወርደዋለሁ !

5 ልጄ ፡ ሆይ ! እውነተኛውን ፡ ነገር ፡ ተከተል ።

6 እንጃ ፡ እርሱን ፡ አላየሁትም ።

7 ኧረ ፡ በል ! በቀለን ፡ ያየኸው ፡ የት ፡ ነው ?

8 ይኸውልሃ ! ትቶት ፡ ሄዷል ።

ቃለ ፡ አጋኖ ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ለሰው ፡ የተፈጥሮ ፡ ስሜቱን ፡ መግለጫ፡ ስለ፡ ሆነ ፡ ከልብ ፡ ውስጥ ፡ መንጭቶ ፡ መምጣት ፡ አለበት ፡ እንጂ ፤ እንደ፡ ሌሎቹ ፡ የንግግር ፡ ክፍሎች ፡ አጥንተን ፡ የምንማረው ፡ አይደለም ። የሆነ ፡ ሆኖ ፡ በጥቂቱ ፡ ዘዴውን ፡ መመልከት ፡ አስፈላጊ ፡ ነው ።

# ፪ኛ ፡ ክፍል ፡ አገባብ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ፡ ሐረግ ፡

ቃላት ፡ እንደ ፡ ሰንሰለት ፡ ተያይዘው ፡ ወይም ፡ እንደ ፡ ሐረግ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው፡ ተያይዘው ፡ የመገናኘታቸው ፡ አሰካክ ፡ ሐረግ ፡ ያሰኛቸዋል ፤ ስለዚህ ፡ ሐረግ ፡ ማለት ፡ ተሳሳቢ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ሐረግ ፡ እንደሚከተለው ፡ በ፫ ፡ ይከፈላል ።

1 ንኡስ ፡ ሐረግ ፥

2 ጥገኛ ፡ ሐረግ ፥

3 መደበኛ ፡ ሐረግ ፥

ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ባለቤትና ፡ አንቀጽ ፡ የሌለው ፡ ቃላትን ፡ በዘኀብረት ፡ የያዘ ፡ ባረ ፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ እንዳንድ ፡ ክፍል ፡ ሆኖ ፡ የሚገባ ፡ ነው ። ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ባራት ፡ ንኡሳን ፡ ክፍሎች ፡ ይከፈላል ።

## የንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ዐይነቶች ፡

1 መስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡
2 አርእስታዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡
3 ሳቢ ፡ ዘር ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡
4 የቦዝ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡

## የንኡስ ፡ ሐረግ ፡ አመዳደብ ፡

መስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ፡- መስተዋድድ ፡ ማናቸውንም ፡ የስም ፡ ዐይነቶች ፡ እንደሚገዛ ፡ አርእስትንና ፡ ሳቢ ፡ ዘርንም ፡ ይገዛቸዋል ፤ ስለዚህ ፡ በመስተዋድድ ፡ የሚመደበው ፡ ሐረግ ፡ መስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ነው ።

ምሳሌ ፡

| | | |
|---|---|---|
| ከሰዓት ፡ በኋላ ፡ | እንደ ፡ ሰነፍ ፡ ልጅ ፡ | በሰይፍ ፡ |
| በዛፉ ፡ ላይ ፡ | እንደ ፡ ትጉህ ፡ ልጅ ፡ | በመንገድ ፡ |
| ከዛፉ ፡ ላይ ፡ | ከፈለቀ ፡ በስተቀር ፡ | በንፍገት ፡ |
| እንደ ፡ ሥራህ ፡ | ስለ ፡ ፈለቀ ፡ ጉዳይ ፡ | ወደ ፡ እርሻው ፡ |
| በመፎከር ፡ | ስለ ፡ ፈለቀ ፡ ነገር ፡ | ወደ ፡ ደጋ ፡ |
| እንዳባትህ ፡ | በመደንፋት ፡ | በማላገጥ ፡ |
| ባስተያየት ፡ | ባነጋገር ፡ | ባለባበስ ፡ |

አርእስት ፡ ማናቸውንም ፡ የስም ፡ ዐይነቶች ፡ ወይም ፡ ሳቢ ፡ ዘርን ፡ የገዛ ፡ እንደ ፡ ሆነና ፡ በሕገኛ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ የተገለጸ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አርእስታዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ተብሎ ፡ ይጠራል ።

ምሳሌ ፡

| | | |
|---|---|---|
| ሥራን ፡ ማጠናቀቅ ፡ | ልጆችን ፡ ማስተማር ፡ | ተግቶ ፡ መሥርት ፡ |
| ልብስን ፡ ማጠብ ፡ | መጽሐፍን ፡ ማንበብ ፡ | አስቦ፡ ማደር ፡ |
| ሁል ፡ ጊዜ ፡ መንቀባረር ፡ | የደብዳቤ፡ አጻጻፍን፡መማር፡ | |

ቦዝ ፡ ስሞችን ፡ የሳበ ፡ እንደሆን ፡ ወይም ፡ በተውሳከ ፡ ግስ ፡ የተገለጸ ፡ እንደሆን ፡ ቦዛዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ይሆናል ።

ምሳሌ ፡

| | | |
|---|---|---|
| ወንድሙን ፡ ሸኝቶ ፡ | ዱሩን ፡ መንጥሮ ፡ | ሌትና ፡ ቀን ፡ ሠርቶ ፡ |
| ወንዙን ፡ ተሻግሮ ፡ | አነባበቡን አጥፍቶ፡ ጢት፡ ማታ፡ | (ጢትና፡ ማታ)፡ ተገላምጦ፡ |
| ፍየሏን ፡ ሰብሮ ፡ | ዘወትር ፡ ተክዞ ፡ | አስተያየቱን ፡ ለውጦ ፡ |
| ማሳውን ፡ አለስልሶ ፡ | ድምፁን ፡ አጥፍቶ ፡ | አገሩን፡ ከድቶ፡ ጨለማ፡ ለብሶ፡ |

ሳቢ ፡ ዘር ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡- በሳቢ ፡ ዘር፡ የሚመሠረተው ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ነው ። ሳቢ ፡ ዘርና ፡ አርእስት ፡ የነገር ፡ ስሞች ፡ ናቸው ። ልዩነታቸው ፡ አርእስት ፡ በ ፡ «መ» ፡ ስለሚ

ዝምርና ፡ በስም ፡ ደንብ ፡ ስለማይበዛ ፡ ነው ። እንደዚሁም ፡ ሳቢ ፡ ዘር ፡ በ ፡ «አ» ፡ ስለ ሚዝምርና ፡ ስለሚበዛ ፡ ነው ። ከዚህ ፡ በስተቀር ፡ በሌላው ፡ ግብራቸው ፡ አይለያዩም ። ባማርኛችን ሳቢ ፡ ዘርን ፡ እንደ ፡ አርእስት ፡ በብዙ ፡ እንሠራበትም ።

ምሳሌ ፡

ቃልን ፡ አሰባበር ፡ ዕርፍን ፡ አጨባበጥ ፡
ንግግርን ፡ አሰጣጥ ፡ እንዝርትን ፡ አያያዝ ፡

## የንኡስ ፡ ሐረግ ፡ አገባብ ፡

ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ሦስት ፡ አገባቦች ፡ አሉት ፤ እነርሱም ፡ የሚከተሉት ፡ ናቸው ።

1 ቅጽላዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡
2 ስማዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡
3 ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡

ቅጽላዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ እንዳንድ ፡ ቅጽል ፡ ሆኖ ፡ ስሞችን ፡ የሚገልጽ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ፡ ነው ።

## መስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ እንደ ፡ ቅጽል ፡

አስረጅ ፡- 1 ባገር ፡ ቤት ፡ ሰዎች ፡ ለጤናቸው ፡ አይጠነቀቁም ።

ባገር ፡ ቤት ፡ የሚለው ፡ ቃል ፡ ሰዎችን ፡ ይገልጻል ፤ ምክንያቱም ፡ ሰዎች ፡ ያሉበ ትን ፡ ስፍራ ፡ ስለሚያመለክትም፡ ነው ። ባማርኛችን ፡ እንደዚህ ፡ ያለው ፡ ቃል ፡ ከዚህ ፡ በፊት ፡ ተለይቶ ፡ አይታወቅም ፡ ነበር ፤ አሁን ፡ ግን ፡ ይኸው ፡ ተገልጾአል ፡ በዚሁ ፡ ዘዴ፡ ማጥናት ፡ ነው ።

ይህ ፡ ዐይነት ፡ ቅጽላዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ በመሆኑና ፡ ባለመሆኑ ፡ የተጠራጠርን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ወደ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ለመለወጥ ፡ መሞከር ፡ ነው ። ርግጥ ፡ የተለወጠ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ቅጽላዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ነው ፤ ያልተለወጠ ፡ እንደሆነ ፡ ግን ፡ ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ «ባገር ፡ ቤት ፡ ያሉ ፡ (የሚኖሩ) ፡ ሰዎች ፡ ለጤ ናቸው ፡ አይጠነቀቁም» ፡ ማለት ፡ ነው ።

2 ወርቅነህ ፡ ለመነገጃ ፡ ገንዘብ ፡ አለው ።
«ወርቅነህ ፡ ለመነገጃ ፡ የሚሆን ፡ ገንዘብ ፡ አለው» ማለት ፡ ነው ።
3 የፈረስህ ፡ ልጓም ፡ ጠባብ ፡ ነው ።
4 የጭቃ ፡ ቤት ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ አይኖርም ፡ ማለትን ፡ አልሰማህም ፡ እንዴ ?
5 የጠረጴዛውን ፡ እግር ፡ ቀለም ፡ አትፋቀው ።
6 የኤርትራ ፡ ሕዝብ ፡ ስለ ፡ ነፃነቱ ፡ ቀናተኛ ፡ በመሆኑ ፡ ተጋድሎውን ፡ እንደ ፡ ቀጠለ ፡ ነው ።
7 የሰው ፡ ጤፉ ፡ ልጅ ፡ አሳብ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ነው ።

በዘርፍ ፡ በዘርፍ ፡ አስተኔ ፡ በዘርፍ ፡ አስተኔ ፡ የወገን ፡ ቅጽልና ፡ በግብር ፡ አመልካች ፡ ዘርፍ ፡ አስተኔ ፡ ቅጽል ፡ ደንብ ፡ የሚነገሩት ፡ ቅጥያዎች ፡ ሁሉ ፡ በቅጽላዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ክፍል ፡ መጠቅለል ፡ አለባቸው ።

## ቦዛዊ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ እንደ ፡ ቅጽል ፡

### አስረጅ ፡

1 ፈለቀ ፡ ወንድሙን ፡ ሸኝቶ ፡ በቶሎ፡ ይመለሳል ።

2 ወንድሙን ፡ ሸኝቶ ፡ ብቻውን ፡ አይበላም ።

3 ወንዙን ፡ ተሻግሮ ፡ ነፍጡን ፡ ደገነና ፡ የድኵላውን ፡ ራስ ፡ በጥርቆ ፡ ጣለው ።

4 በዛፉ ፡ ሥር ፡ የተጋደመው ፡ አንበሳ ፡ ፍየሏን ፡ ሰብሮ ፡ ደሟን ፡ ስለ ፡ ጠጣ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ ማለት ፡ አቅቶታል ።

5 ትናንትና ፡ ማታ ፡ አንድ ፡ ሌባ ፡ ድምጡን ፡ አጥፍቶ ፡ መጣና ፡ ልብሳችንን ፡ ሁሉ ፡ ሙልጭ ፡ አድርጎ ፡ ወሰደ ።

6 አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ በትጋት ፡ ሠርተው ፡ መበልጸግን ፡ ይጠሉና ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተቀጽላ ፡ ተጣብቀው ፡ ይኖራሉ ።

7 ከዝንጀሮ ፡ ጋራ ፡ ጪት ፡ ማታ ፡ ተገላምጩ ፡ አላርስም ፡ ማለት ፡ ወይዘሮ ፡ ድኅነትን ፡ ያለድካም ፡ ለማግባት ፡ ያስችላል ።

ስማዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ስማዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ እንዳንድ ፡ ስም ፡ ሆኖ ፡ በስም፡ ፋንታ ፡ የሚገባ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ እንደ ፡ ባለቤት ፡ እንደ ፡ ተሳቢና ፡ እንደ ፡ መሙሊያ ፡ ይሆናል ።

## አርእስታዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ እንደ ፡ ስም ፡

1 ትምህርትን ፡ ማጥናት ፡ ትልቅ ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ ነው ።

2 አካሄድን ፡ ማሳመር ፡ ያስከብራል ።

3 የሰውን ፡ ገንዘብ ፡ መፈለግ ፡ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ አደኅይቷል ።

4 ቤትንና ፡ ልብስን ፡ ማጽዳት ፡ ከብዙ ፡ በሽታዎች ፡ ይጠብቃል ።

### በተሳቢነት ፡

5 በሽተኞችን ፡ መጎብኘት ፡ ታፈቅራለች ።

6 ልጅቱ ፡ አበባ ፡ ማበጃጀትን ፡ ትወዳለች ።

7 ንቦች ፡ አውራቸውን ፡ መከተልንና ፡ ማገልገልን ፡ በተፈጥሮ ፡ ጠባያቸው ፡ ያውቃሉ ።

8 የግብር ፡ ቤትን ፡ ማስጌጥ ፡ አትፈቅድም ።

## በመሙሊያነት ፡

9 እግዚአብሔር ፡ የማይወደው ፡ ሰውን ፡ ማታለል ፡ ነው ።
10 በሥራ ፡ ላይ ፡ ማፌዝ ፡ የተሰጠንን ፡ አደራ ፡ መሻር ፡ ነው ።
11 አገርን ፡ መውድድ ፡ እውነትን ፡ ማስፋፋት ፡ ነው ።
12 እኔ ፡ እምወደው ፡ ኳስ ፡ መጫወትን ፡ ነው ።

## ሳቢ ፡ ዘር ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ እንደ ፡ ስም ፡

አስረጅ ፡

1 ዕርፍ ፡ አያያዝ ፡ በአሰፋ ፡ ያምራል ።
2 አገር ፡ አገዛዝ ፡ በእርሱ ፡ ጊዜ ፡ ቀረ ። } በባለቤትነት ፡

3 መንግሥቱ ፡ ቃል ፡ አሰባበርን ፡ ያሳምራል ።
4 ፈለቀ ፡ ምክር ፡ አሰጣጥን ፡ በደንብ ፡ ያውቃል ። } በተሳቢነት

ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡- ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ባንድ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ፋንታ ፡ ገብቶ ፡ የሚሠራ ፡ ነው ።

መስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ እንደ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡

አስረጅ ፡

1 በሰው ፡ ላይ ፡ መፎክር ፡ የእብሪት ፡ ሥራ ፡ ሰውን ፡ ያስወቅሳል ።
2 አባቴ ፡ ከሰዓት ፡ በኋላ ፡ ይመጣሉ ።
3 ከዛፉ ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ ወፍ ፡ ተነሥታ ፡ በረረች ።
4 አንድ ፡ ላም ፡ ከቤታቸው ፡ አጠገብ ፡ ትግጣለች ።
5 ባንድ ፡ ሳምንት ፡ ውስጥ ፡ ሁለት ፡ መጻሕፍት ፡ ያነባል ።
6 ከእርሱ ፡ በስተቀር ፡ ማንንም ፡ አያፍርም ።
※ ቦዝ፡ ንኡስ፡ ሐረግ፡ እንደ፡ ተውሳከ፡ ግስ፡ ሲሆን፡ በቦዝ፡ ክፍል፡ ተመልከት።

## ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡

ባለቤትና ፡ አንቀጽ ፡ ያለው ፡ ቃላትን ፡ በዘኀብረት ፡ የያዘ ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ፡ ከመደበኛው፡ ተጠግቶ፡ የሚገባ፡ ነው። ጥገኛ፡ ሐረግ፡ በጥገኛ፡ መስተፃምር ፡ ይመሠረታል ። መስተዋድድ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ጥገኛውን ፡ መስተፃምር ፡ ውጦ ፡ ባንቀጽ ፡ ላይ ፡ የሚያርፍበት ፡ ጊዜ ፡ አለ ። በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ደኅና ፡ አድርጎ ፡ ማስተዋል ፡ አስፈላጊ ፡ ነው ። አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ መስተዋድዶች ፡ ባንቀጾች ፡ ላይ ፡ በተጫኑ ፡ ጊዜ ፡ ጥገኛ ፡ መስተፃምሮች ፡ ይሆናሉ ፤ አንዳንዱ ፡ ግን ፡ በውስጠ ፡ ታዋቂነት ፡ ጥገኛውን ፡ መስተፃምር ፡ ያስገኛሉ ።

አስረጅ ፡

መስተዋድድ ፡ ጥገኛ ፡ መስተፃምር ፡ ሲሆን ፡

መፀዛ ፡ ስለ ፡ ታመመ ፡ ዘመዶቹ ፡ በፍጥነት ፡ ወደ ፡ ሐኪም ፡ ቤት ፡ ወሰዱት ። እኔ ፡ በመጣሁ ፡ ቊጥር ፡ እናንተ ፡ መጨነቅ ፡ የለባችሁም ።

## የጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ዐይነቶች ፡

የጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ዐይነትና ፡ አገባብ ፡ አንድ ፡ ናቸው ።

ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ እንደ ፡ ስም ፡ እንደ ፡ ቅጽል ፡ እንደ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ሆኖ ፡ ባረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ይገባል ፤ ለብቻው ፡ ሆኖ ፡ በተነገረ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ሙሉ ፡ ስሜትን ፡ አይሰጥም ።

ስም ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡- በስም ፡ ፋንታ ፡ ገብቶ ፡ የሚሠራ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ነው ።

### እንደ ፡ ባለቤት ፡

አስረጅ ፡

1 ትናንትና ፡ መንገደኛውን ፡ የገፈፉት ፡ በብዙ ፡ ምርመራ ፡ አመኑ ።
2 በዛፉ ፡ አጠገብ ፡ የቆመው ፡ ያክሥቴ ፡ ልጅ ፡ ነው ።
3 ይህን ፡ መጽሐፍ ፡ የጻፈው ፡ አልታወቀም ።

### እንደ ፡ ተሳቢ ፡

1 አንተና ፡ ፈለቀ ፡ እንደ ፡ ተጣላችሁ ፡ ሰምቻለሁ ።
«አንተና ፡ ፈለቀ ፡ መጣላችሁን ፡ ሰምቻለሁ » ፡ ማለት ፡ ነው ።
2 ይህ ፡ ልጅ ፡ ጠንክሮ ፡ ካጠና ፡ እንደሚሸለም ፡ አምናለሁ ።
3 ካንድ ፡ ሰዓት ፡ በኋላ ፡ የሚመጣውን ፡ አታስገባ ።
4 ኧረ ፡ በምን ፡ ምክንያት ፡ የተነጋገርነውን ፡ ረሳሽው ?

### እንደ ፡ መስተዋድድ ፡ ተገዥ

1 በሠራኸው ፡ መጠን ፡ እከፍልሃለሁ ። «በሠራኸው ፡ ሥራ ፡ ልክ ፡ እከፍልሃለሁ» ፡ ማለት ፡ ነው ።

2 የሰው ፡ አጥር ፡ የሰበረ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ሰረቀ ፡ ወይም ፡ እንደ ፡ ገደለ ፡ ያህል ፡ ይቈጠራል ።

3 የዋሸ ፡ ሰው ፡ ወንጀል ፡ ከሠራ ፡ ቊጥር ፡ ነው ።
4 ተወው ፡ ይቀመጥ ፡ ሥራውን ፡ እንደሆን ፡ ባለበት ፡ ያከናውናል ።

### እንደ ፡ ተጣማሪ ፡

1 ወሬው ፡ አንዳርጌ ፡ እንደ ፡ ረታ ፡ በከተማ ፡ ውስጥ ፡ ይነፍሳል ።
2 ጠብ ፡ ያነሣውን ፡ እንቢተኛ ፡ የነበረውን ፡ ሁላችንም ፡ እናውቀዋለን ።

## እንደ ፡ ቃል ፡ መግለጫ ፡ ተጨማሪ ፡

3 ምስሎው ፡ ቤቱን ፡ የተሸከመው ፡ ከማይነቅዝ ፡ ዕንጨት ፡ የተበጀ ፡ ነው ።

4 ማንደፍሮትን ፡ በሁለተኛው ፡ ክፍል ፡ አንደኛ ፡ የሆነውን ፡ ጥራልኝ ።

5 ታታሪው ፡ ገበሬ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ካምሳ ፡ ዳውላ ፡ ያመረተው ፡ በራስ ፡ ስሞሽ ፡ እህሉን ፡ አስጫነው ።

## እንደ ፡ አንቀጽ ፡ መሙሊያ ፡

1 ልጁ ፡ አቶ ፡ ፈለቀ ፡ የመረጡት ፡ ነው ።

2 አስተማሪው ፡ ከ፪ኛ ፡ ደረጃ ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ ተመርጦ ፡ የወጣ ፡ ነው ።

3 ይህ ፡ ሰው ፡ ትናንትና ፡ የሰበከው ፡ ነው ።

<u>ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ</u> ፡- ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ እንዳንድ ፡ ቅጽል ፡ ሆኖ ፡ ስምን ፡ የሚገልጽ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ነው ።

<u>አስረጅ</u> ፡

1 ታላቁ ፡ ነጋዴ ፡ አቶ ፡ ማንደፍሮት ፡ በስንት ፡ትግል ፡ ያስመጡትን ፡ ቦንዳ ፡ ላቶ ፡ በፈቃዱ ፡ በርካሽ ፡ ዋጋ ፡ ሸጡት ።

2 አቶ ፡ አየለ ፡ አናጢው ፡ የሠራቸው ፡ ቁም ፡ ሣጥኖችና ፡ ወንበሮች ፡ በጣም፡ ያማሩና ፡ የተዋቡ ፡ ስለ ፡ ነበሩ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ለመግዛት ፡ በዋጋ ፡ ተሜረቱባቸው ።

3 ልጁ ፡ ሰነፍ ፡ ብጤ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የበቃ ፡ ዕውቀትን ፡ አያገኝም ።

4 ካምስት ፡ ሺ ፡ የሚበልጡ ፡ ሰዎች ፡ በሐረር ፡ ከተማ ፡ ይኖራሉ ።

<u>ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ</u> ፡- ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ በተውሳከ ፡ ግስ ፡ ፋንታ ፡ እየገባ ፡ እንዳንድ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ የሚያገለግል ፡ ነው ።

የተውሳከ ፡ ግሳውያን ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ዐይነቶች ፡ የሚከተሉት ፡ ናቸው ።

፩ ፡ ምክንያታዊ ፡
፪ ፡ አፍራሽ ፡
፫ ፡ ውለተኛ ፡
፬ ፡ ውጤትን ፡ አመልካች ፡
፭ ፡ ዐላማን ፡ አመልካች ፡
፮ ፡ አማራጭ ፡
፯ ፡ አኳኋን ፡
፰ ፡ ጊዜን፡ አመልካች ፡

<u>፩ ፡ ምክንያታዊ</u> ፡- አንድ ፡ ነገር ፡ ለምን ፡ እንደ ፡ ተደረገ ፡ ወይም፡ለምን ፡ ወደ ፊት ፡ እንደሚደረግ ፡ ያስረዳናል ።

ስለ ፡— መልአኩ ፡ ወንድሙን፡ ስለሚወደው ፡ በትምህርት ፡ ቤት፡ያግዘዋል።
ና ፡— ውብሸት ፡ እናቱን ፡ ናፍቋልና ፡ መሄዱ ፡ አይቀርም ።
ከ-ዘንድ፡- ውብሸት ፡ ይህን ፡ ከተናገረ ፡ ዘንድ ፡ ይፈረድበታል ።

፪ ፡ አፍራሽ ፡-መከራ ፡ ወይም ፡ ደስታ ፡ ሲበዛ ፡ ቢውል ፡ የቍርጠኛ ፡ ሰውን ፡ አሳብ ፡ አይለውጠውም ፡ የማለትን ፡ ስሜት ፡ የሚገልጽ ፡ መስተፃምር ፡ ነው ።

አስረጅ ፡-

ምንም ፡ እንኳ ፡ ቢ—ምንም ፡ እንኳ ፡ ኢጣያልኖች ፡ ባንዳንድ ፡ ቦታ ፡ ላይ ፡ ሕዝቡን ፡ በማታለያ ፡ ስብከት ፡ ቢያዋኽሩቁት ፡ ነፃነቱን ፡ አልረሳም ።

ቢ-እንኳ ፡-　　ቢናገርህ ፡ እንኳ ፡ አትመልስለት ።
ምንም ፡ ቢ-　　ምንም ፡ ቢቸግረኝ ፡ በሰንበት ፡ አልሠራም ።
ቢ-እኮ ፡ -　　ቢሠራም ፡ እኮ ፡ የሚያሳፍር ፡ አይደለም ።

፫ ፡ ውለተኛ ፡ በሁለት ፡ ወይም ፡ ከሁለት ፡ በበለጡ ፡ ሰዎች ፡ መካከል ፡ የሚ ደረገውን ፡ ውል ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

የ-እንደሆን፡—　　እህል ፡ የጫነለት ፡ እንደሆን ፡ መቶ ፡ ብር ፡ ይከፍለዋል ።
ብ-　　በዚህ ፡ ሳምንት ፡ ውስጥ ፡ ብትመልስ ፡ እንቀበልሃለን ።
ብ-ም　　ብቀመጥም ፡ ባልቀመጥም ፡ የቤቱን ፡ ኪራይ ፡ እከፍላለሁ ።

፬ ፡ ውጤትን ፡ አመልካች ፡

ውጤትን ፡ አመልካች፡- የተደረገ ፡ ነገርን ፡ ውጤት ፡ የሚያሳይ ፡ መስተፃምር ፡ ነው ።

አስረጅ፡- እስኪ፡- (ሀ) ዐይኖቹ ፡ እስኪፈሱ ፡ ድረስ ፡ ሌት ፡ ከቀን ፡ አለቀሰ ።
(ለ) የባሕር ፡ ማሽላን ፡ እስኪያር ፡ ድረስ ፡ ካልጠበሱት ፡ ለጤንነት ፡ አይስማማም ።

፭ ፡ ዐላማን ፡ አመልካች ፡- ሰውዬው ፡ የሚያደርገውን ፡ ቍርጥ ፡ አሳብ ፡ የሚ ያሳይ ፡ ጥገኛ ፡ መስተፃምር ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

እንዲ-　　ወደ ፡ ሐረር ፡ እንዲሄድ ፡ አንድ ፡ አውቶሞቢል ፡ ተከራየ ።
ሊ-　　ወንድሙን ፡ ሊጠይቅ ፡ ወደ ፡ ሆስፒታል ፡ ሄደ ።
ዘንድ-　　ወንድሙን ፡ ያሳፍር ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ባቡር ፡ ጣቢያ ፡ ሄደ ።

ማስገንዘቢያ ፡

ከሊቃውንት ፡ ወገን ፡- ዘንድና ፡ ሊ ፡ እንደ ፡ ጥንታቸው ፡ ከግእዙ ፡ ሲያያዝ ፡ በመጣው ፡ ዐዋጅ ፡ በዘንድ ፡ አንቀጽነት ፡ ይጠሩ ፡ ይላሉ ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ ዘንድና ፡ ሊ ፡ በትንቢት ፡ ጊዜያት ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡ የሚሆኑ ን ፡ ግሶች ፡ በመነሻ ፡ ወይም ፡ በመድረሻ ፡ ገብተው ፡ ከማሰር ፡ ስለሚያግዷቸው ፡ ባሁኑ ፡ ያማርኛ ፡ ሰዋስው ፡ አካ ሄድ ፡ በመስተፃምር ፡ ክፍል ፡ እንዲሆኑ ፡ ተመድበዋል ።

፮ ፡ አማራጭ ፡- አንዱን ፡ ካንዱ ፡ አብልጦ ፡ ማፍቀርን ፡ ወይም ፡ መጥላትን ፡ ወይም ፡ መሻልንና ፡ አለመሻልን ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

<u>አስረጅ ፡</u>

ከ-ይልቅ፡- ከተቀረጸው ፡ እርሳስ ፡ ይልቅ ፡ ያልተቀረጸውን ፡ እመርጣለሁ ። ማለት ፡ የተቀረጸውን ፡ እርሳስ ፡ ከመምረጥ ፡ ይልቅ ፡ ያልተቀረጸውን ፡ እርሳስ ፡ እመ ርጣለሁ ፡ ማለት ፡ ነው ።

እንዲ-የትምህርትን ፡ ጣዕም ፡ ያላወቀ ፡ ሕፃን ፡ እንዲማግጥ ፡ ሰነፍ ፡ ሰውም ፡ ጊዜውን ፡ በመንገላወድ ፡ ያሳልፋል ።

እንደ ፡- አንዳርጌን ፡ እንደ ፡ ሸለምከው ፡ እኔንም ፡ ሸልመኝ ።
አንዳርጌ ፡ እንደ ፡ ጎበዝ ፡ ያህል ፡ አልበረታህም ።

<u>፲ ፡ ሁኔታን ፡ አመልካች ፡-</u> አንድ ፡ ሰው ፡ በሠራው ፡ መጠን ፡ ዋጋውን ፡ እንደ ሚያገኝና ፡ አንድ ፡ ነገርን ፡ ሲሠራ ፡ አኳኋኑን ፡ እንደሚያሳይ ፡ ይገልጻል ።

<u>አስረጅ ፡</u>

እንደ ፡ — እንደ ፡ ተመኘነው ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ በማየታችን ፡ ታላቅ ፡ ደስታ ፡ ተሰምቶናል ።
እንድ ፡ — እንደ ፡ ደከምን ፡ እንድንቀር ፡ የቸሩ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ አይደለም ።

ፕሮግራማችንን ፡ እንደ ፡ ፈለግነው ፡ ለመለወጥ ፡ አንችልም ።
እየ- አማረ ፡ እየሮጠ ፡ መጣ ።
አማረ ፡ እየጸፈ ፡ ያጠናናል ።

<u>፲፩ ፡ ጊዜን ፡ አመልካች ፡-</u> አንድ ፡ ነገር ፡ የተደረገበትን ፡ ወይም ፡ የሚደረግ በትን ፡ ሰዓት ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

<u>አስረጅ ፡-</u> እንደ፡- ወንድሙ ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ ተመለሰ ፡ እንጂ ፡ አልቆየም ።

ሲ- አቶ ፡ ፈለቀን ፡ ሲመለሱ ፡ ጥራቸው ።
ሳ- ወደ ፡ ሥራህ ፡ ሳትሄድ ፡ ጉዳዬን ፡ ጨርስልኝ ።
እስኪ- አበበ ፡ እስኪ ፡ መለስ ፡ ጥቂት ፡ እንሥራ ።
በ-ጊዜ፡- በመጣህ ፡ ጊዜ ፡ ጠይቀው ።
ስ ፡ - ወንድም ፡ ጋሻ ፡ ሳለ ፡ ምንም ፡ አይቸግረኝ ።

<u>ማስገንዘቢያ</u> ፡- ተውሳከ፡ ግሳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ በዝን ፡ አርእስትን ፡ ቅጽላዊ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግንና ፡ ተውሳከ ፡ ግስን ፡ ስለሚገልጽ ፡ ጥገኛውን ፡ ሐረግ ፡ አውጣ ፡ በተ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ገላጮቹ ፡ ሁሉ ፡ አብረውት ፡ ይወጣሉ ። ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ እንዳለ ፡ አውጣ ፡ የተባለም ፡ እንደሆን ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ለብቻው ፡ ይወጣል ። እንግዴህ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ከሚገልጸው ፡ ጋራ ፡ አብሮ ፡ መውጣቱንና ፡ እንደ ፡ ገና፡ ለብቻው ፡ መውጣቱን ፡ አስተውል ።

## የንኡስና ፡ የጥገኛ ፡ ሐረጎችን ፡ አፈታት ፡

፩ ፡ ዐይነቱ ፡

፪ ፡ አገባቡ ፡

ምሳሌ ፡- 1 ባፋፍ ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ ወንድሙን ፡ ይጣራል ።

ባፋፍ ፡ ላይ ፡ መስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ የቦታ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ሆኖን ፡ ቦዙን ፡ ይገልጻል ።

2 ደምሴ ፡ ከቤት ፡ መውጣት ፡ አይወድም ።

ከቤት ፡ መስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ የቦታ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ መውጣትን ፡ አርእስቱን ፡ ይገልጻል ።

3 እኛን ፡ በኀጢአት ፡ የተለወስነውን ፡ ባሮቹን ፡ ሊያድን ፡ መጣ ።

በኀጢአት ፡ የተለወስነውን ፡ ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ባሮቹን ፡ ይገልጻል ።

በኀጢአት ፡ መስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ የተለወስነውን ፡ ይገልጻል ።

ሊያድን ፡ ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ «መጣን» ፡ ይገልጻል ።

## መደበኛ ፡ ሐረግ ።

መደበኛ ፡ ሐረግ ፡ የሚባለው ፡ ባለቤትና ፡ አንቀጽ ፡ ያለው ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግን ፡ የማይጨምር ፡ በገዛ ፡ ራሱ ፡ ሙሉ ፡ ስሜትን ፡ ለመስጠት ፡ የሚችል ፡ አረፍተ፡ ነገር፡ ነው። በዚህ ፡ ክፍል ፡ መደበኛ ፡ ሐረግን ፡ «ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር» ፡ ብለን ፡ እንጠራዋለን ።

አስረጅ ፡

1 አንዳርጌ ፡ ከፎቅ ፡ ላይ ፡ ወደቀ ።
2 ዘወትር ፡ እሠራለሁ ።
3 እባክህ ፡ መጽሐፌን ፡ በጠረጴዛው ፡ ላይ ፡ አስቀምጥልኝ ።
4 እንዲያው ፡ በከንቱ ፡ ደክሜ ፡ ተመለስሁ ።
5 ይህች ፡ ሴት ፡ በርበሬውን ፡ መሳ ፡ ለመሳ ፡ ለወጠችው ።
6 ወዲያ ፡ ወዲህ ፡ ብለህ ፡ ሥራ ፡ መፈለግ ፡ አለብህ ።
7 በፊት ፡ ምሳችንን ፡ እንብላ ።
8 ትናንትናና ፡ ዛሬ ፡ ደስ ፡ አይለኝም ።
9 መቼ ፡ መጣህ ፡ አቶ ፡ ፈለቀ ?
10 በየቀኑ ፡ ሥራህን ፡ በማከናወንህ ፡ ትመሰገናለህ ።

## ፲፩ኛ ፡ መልመጃ ።

1 (ሀ) ከሚከተሉት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ ጥገኛውን ፡ ሐረግ ፡ እየለየህ ፡ አመልክት ።

አየለ ፡ በፈተና ፡ አንደኛ ፡ የሆነው ፡ ትናንትና ፡ ከጥምቀተ ፡ ባሕር ፡ ሲመጣ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ብር ፡ በወረቀት ፡ እንደ ፡ ተጠቀለለ ፡ በመንገድ ፡ ዳር ፡ ወድቆ ፡ አገኘ ።

2 ልጁ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ ስላለው ፡ እየሮጠ ፡ ሄደ ።

3 ለእናቱም ፡ ገንዘብ ፡ ማግኘቱንና ፡ እንዴት ፡ እንዳገኘው ፡ ነገራት ።

(ለ) ከሚከተሉት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ ንኡስ ፡ ሐረጎችንና ፡ ጥገኛ ፡ ሐረጎችን ፡ አውጣ ፤ አገባባቸውንም ፡ በየዐይነታቸው ፡ አመልክት ።

1 በጥጋብ ፡ ወራት ፡ እህልን ፡ መሸመትና ፡ በችግር ፡ ጊዜ ፡ እህልን ፡ ማሸመት ፡ ከጥበበኛ ፡ ያስቈጥራል ።

2 እየተወሳህ፡ ለመኖር፡ ብትፈልግ፡ በተቻለህ፡ መጠን ፡ ቀዋሚ ፡ ነገርን ፡ ሥራ።

3 ዘወትር ፡ አሸናፊ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ በቀን ፡ ብዛት ፡ መሸነፉ ፡ አይቀርም ።

4 አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ ያምላክን ፡ ክብር ፡ ለመቀደስ ፡ የተፈጠሩ ፡ መሆናቸውን፡ አያስቡም ።

5 በተደሰትን ፡ ጊዜ ፡ የበለጠ ፡ ሥራ ፡ እንደምንሠራ ፡ አምናለሁ ።

6 ደበበው ፡ በፈቃዱ ፡ እንደ ፡ ቀረ ፡ አስታውቋል ።

7 መንክር ፡ በፈቃዱ ፡ የተናገረውን ፡ አይቀበልም ።

8 ወሬው ፡ አየለ ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ ነው ።

9 ማመልከቻህን ፡ ትናንትና ፡ ያቀረብክልንን ፡ ተመልክተነዋል ።

10 ደበበው ፡ እንዲጽፈው ፡ አስቀድመን ፡ አስበንበታል ።

11 ሰው ፡ በጠና ፡ ስለ ፡ ታመመ ፡ አይሞትም ።

12 ነፋሱ ፡ መጥፎ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ በቤት ፡ ዋልን ።

13 በኔ ፡ በኩል ፡ ብትመጣ ፡ አብረን ፡ እንሄዳለን ።

14 ሥራችንን ፡ ከጨረስን ፡ በኋላ ፡ ለሽርሽር ፡ እንሄዳለን ።

15 ያንን ፡ መንገደኛ ፡ የገፈፉት ፡ ሽፍቶች ፡ ተያዙ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ።

አረፍተ ፡ ነገር ፡ ማለት ፡ ሙሉ ፡ ስሜትን ፡ የሚሰጥ ፡ የቃላት ፡ መተባበር ፡ ነው ። እንደዚህም ፡ ለማለት ፡ ይቻላል ፤ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ቃላት ፡ በዘኅብረት ፡ ተቀነባብረው ፡ አንድ ፡ ስሜትን ፡ የሚሰጡበት ፡ ክፍል ፡ ነው ። አረፍተ ፡ ነገር ፡ ባምስት ፡ ይከፈላል ።

### ያረፍተ ፡ ነገር ፡ ዐይነቶች ፡

ያረፍተ ፡ ነገር ፡ ዐይነቶች አምስት ፡ ናቸው ።

፩ ፡ ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡
፪ ፡ ድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡
፫ ፡ ድርብ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡
፬ ፡ ድርብ ፡ ድብልቅ ፡ አረፍተ፡ ነገር ፡
፭ ፡ ድርብርብ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡

ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር፡- አንድ፡ መደበኛ፡ ሐረግ፡ ነው ። በነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር፡ ውስጥ ፡ ለመገኘት ፡ የሚችሉት፡ ሕገኛ ፡ ቅጽል ፡ ሕገኛ ፡ ተሸሳከ ፡ ግስና ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ፡ ናቸው ። እንደ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ያለው ፡ ግን ፡ በነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ለመገኘት ፡ አይችልም ።

እንግዲህ ፡ በነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ባንድ ፡ ባለቤትና ፡ ባንድ ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡ ብቻ ፡ ወይም ፡ ከነገላጮቹ ፡ ጭምር ፡ የሚነገር ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

1 የመንግሥቱን ፡ ያህል ፡ አልከፈልህም ።
2 የመንግሥቱን ፡ ያህል ፡ አልሠራህም ።
3 ልጁ ፡ ምንም ፡ ያህል ፡ አላስቸገረኝም ።
4 በምቾት ፡ ልጅ ፡ ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ (ያድጋል) ፡ ይፋፋል ።
5 ሰው ፡ በጥጋቡ ፡ ብዙ ፡ ነገርን ፡ ያደርጋል ።
6 በቆላ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ልብሳቸውን ፡ በእንዶድ ፡ ያጥባሉ ።
7 አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ በመታገሥ ፡ ዋጋቸውን ፡ ያገኛሉ ።
8 ፍሥሐ ፡ ከወርቁ ፡ በኋላ ፡ ይጠራል ።
9 አስተዳደርን ፡ ማወቅ ፡ ለትልቅ ፡ ደረጃ ፡ ያደርሳል ።
10 ልጆች ፡ ሆይ ! ሰው ፡ ማክበርን ፡ መልካሙን ፡ ሥራ ፡ ተማሩ ።
11 አቶ ፡ አየለ ፡ መልካሙን ፡ ሥራውን ፡ በስንፍና ፡ አስወሰደው ።
12 ከብቶቹ፡ ካጥር ፡ ግቢ ፡ ናቸው ።
13 ያላንዳች ፡ ምክንያት ፡ ከሥራህ ፡ አትፈናቀል ።
14 መንግሥቱ ፡ በትምህርት ፡ ጊዜ ፡ ይማግጣል ።
15 አቶ ፡ ወልደ ፡ አምላክ ፡ በሥራ ፡ ላይ ፡ ናቸው ።

ድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገር፡- ካንድ ፡ መደበኛ ፡ ሐረግና ፡ ካንድ ፡ ወይም ፡ ከሁለት ፡ ወይም ፡ ከሦስት ፡ ከሚበልጡ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረጎች ፡ የሚመደብ ፡ አረፍተ፡ ነገር ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

1 መጻሕፍትን ፡ አብዝቶ ፡ ስለማያነብ ፡ ብዙ ፡ ጥቅምን ፡ አያገኝም ።
2 ልጁ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ገላውን ፡ ስለሚታጠብ ፡ ጤናማ ፡ ነው ።
3 እግዚአብሔር ፡ በቸርነቱ ፡ አዝርዕትንና ፡ ዕፀዋትን ፡ ለሕይወታችን ፡ መደገፊያ ፡ አድርጎ ፡ ስለ ፡ ፈጠረልን ፡ ልናመሰግነው ፡ ይገባናል ።
4 ዛሬ ፡ ደመና ፡ ጥሎ ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ ፀሐይዋ ፡ እንዲህ ፡ አድርጋ ፡ ባላቃጠለችም ፡ ነበር ።
5 አያሌ ፡ ተማሪዎች ፡ በሚመጣው ፡ ዓመት ፡ ይመረቃሉ ።
6 መርፌ ፡ የራሷን ፡ ቀዳዳ ፡ ሳታይ ፡ ለብዙ ፡ ስው ፡ ትጠቅማለች ። (ያማርኛ ፡ ተረት) ፡

7 እንጀራው ፡ ከመሣሣቱ ፡ የተነሣ ፡ እፍ ፡ ቢሉት ፡ ይበራል ።
8 ልቤ ፡ ስለ ፡ ሣሣ ፡ መጠጥ ፡ እንኳ ፡ ቢሆን ፡ ለመጠጣት ፡ አልፈቅድም ።
9 ልብሴ ፡ ሥሥ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከብርድ ፡ አያስጥለኝም ።
10 መሬትን ፡ አልፎ ፡ አልፎ ፡ ካላከሩት ፡ ፍሬ ፡ ያለውን ፡ እህል ፡ አይሰጥም ።
11 ካጋም ፡ የተጠጋ ፡ ቀልቋል ፡ ዘለዓለም ፡ ሲያለቅስ ፡ ይኖራል ። (ያማርኛ፡ ተረት) ፡

12 አይቡን ፡ ሳያዩት ፡ እንቱን ፡ ጠገቡት ። (ያማርኛ ፡ ተረት) ፡

ድርብ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡- ድርብ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ከሁለት ፡ ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ በወደረኛ ፡ መተስፃምር ፡ የሚመደብ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

1 ሳይንስ ፡ አይገባኝም ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ ከማጥናት ፡ አላቋርጥም ።
2 የነፋስ ፡ ሥራው ፡ እንጂ ፥ ራሱ ፡ ጎልቶ ፡ ለኛ ፡ አይታይም ።
3 ማናቸውም ፡ ነገር ፡ ይዘገያል ፡ እንጂ ፥ መድረሱ ፡ አይቀርም ።
4 ነገራችንን ፡ አሁን ፡ እንጨርስ ፤ አለበለዚያም ፡ እንቃጠር ።
5 ወይ ፡ አልሄድህ ፡ ወይ ፡ አልተቀመጥህ ፡ ለምን ፡ ጊዜህን ፡ በከንቱ ፡ ታሳልፋለህ ?

6 አየለ ፡ ሳይንስን ፡ ያጠናል ፤ አንተስ ፡ ምን ፡ ትመለከታለህ ።
7 ፈለቀች ፡ የኩታን ፡ ድር ፡ ትፈትላለች ፤ ይሁንና ፡ አታቀጥነውም ።
8 ለተማሪ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ መሄድ ፡ በየቀኑ ፡ አይፈቀድም ፤ እንዲህ ፡ ከሆነ ፡ መታገሥ ፡ አለብን ።

9 ሥራውን ፡ ቆንዦ ፡ አድርገን ፡ እንሠራልሃለን ፤ ብቻ ፡ እነበቀለ ፡ ይምጡ ።
10 በከተማ ፡ ውስጥ ፡ በሽታ ፡ ገብቷል ፤ እንግዲያውስ ፡ ውጭ፡ ውጭ ፡ ማለት ፡ ይቅርብን ።

11 መብራት ፡ ፈጣን ፡ ልጅ ፡ ነው ፤ ሆኖም ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ችላ ፡ ማለትን ፡ ያበዛል ።

12 ሆዴን ፡ እኮ ፡ አሞኛል ፥ በቀለ ! ታዲያ ፡ ለምን ፡ ወደ ፡ ሆስፒታል ፡ አንወስድህም ።

13 ለሰዎች ፡ አንተ ፡ አስብላቸው ፡ እንጂ ፤ እነርሱ ፡ ያስቡልኛል ፡ ብለህ ፡ አሳብህን ፡ አትጣልባቸው ።

ድርብ ፡ ድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡-

ድርብ ፡ ድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ከድርብና፡ ካንድ ፡ ወይም ፡ ካንድ ፡ ከበለጡ፡ ጥገኛ ፡ ሐረጎች ፡ የሚመደብ ፡ ነው ።

1 በዚህ ፡ ዓለም ፡ ከማር ፡ የሚጣፍጥ ፡ ነገር ፡ የለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ማርን ፡ ለማይ ወዱ ፡ ሰዎች ፡ ኮሶ ፡ መስሎ ፡ ይታያቸዋል ።

2 ሰው ፡ ከጠሉት ፡ በኋላ ፡ ነገሩ ፡ ሁሉ ፡ ይመራል ፡ እንጂ ፤ ጣዕምን ፡ አያገኝም ።

3 ነፋስ ፡ ሲነፍስ ፡ ረቂቅ ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ ዕፀዋትንና ፡ ደመናትን ፡ ሲያንቀሳቅሳ ቸው ፡ ይታያል ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ጨስንና ፡ ዐቧራን ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ ሲያክለበል ባቸው ፡ ይታያል ።

4 ፈለቀና ፡ መኰንን ፡ ደኅና ፡ አድርገው ፡ ስላጠኑ ፡ ፈተናውን ፡ አለፉት ፤ የሥ ራቸውንም ፡ ዋጋ ፡ ከምስጋና ፡ ጋራ ፡ ተቀበሉ ።

5 ባ፲፱፻፵፪ ፡ ዓ ፡ ም ፡ በሁለተኛው ፡ ተርም ፡ ትምህርት ፡ ቤቶች ፡ ለዕረፍት ፡ ተዘግተው ፡ ሳሉ ፡ ዘመዶቼን ፡ ለመጎብኘት ፡ ወደ ፡ አሰላ ፡ ሄጄ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በሥራ ፡ ምክንያት ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ አገር ፡ ተዛውረው ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ሄደው ፡ ቈዩኝ ።

<u>ከብላቴን ፡ ጌታ ፡ ኅሩይ ፡ ወልደ ፡ ሥላሴ ፡ መጽሐፍ ፡ ከጥሩ ፡ ምንጭ ፡ የተጠቀሱ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡</u>

6 ስምዖን ፡ ሆይ ! የምድር ፡ ነገሥታት ፡ ግብር ፡ የሚቀበሉት ፡ ከልጆቻቸው ፡ ነውን ፡ ወይስ ፡ ከሌሎች ፡ ነው ? ብሎ ፡ ቢጠይቀው ፡ ከሌሎች ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ።

7 እንግዲያውማ ፡ ልጆቻቸው ፡ ከግብር ፡ ነፃ ፡ ናቸው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እንዳናሰና ክላቸው ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ሂደህ ፡ መቃጥንህን ፡ ጣልና ፡ መዠመሪያ ፡ የምትይዘውን ፡ ዓሣ ፡ አፉን ፡ ስትከፍተው ፡ አፉት ፡ ድሪም ፡ ታገኛለህ ፤ ከዚያም ፡ አውጥተህ ፡ ሁለቱን ፡ ስለኔ ፡ ሁለቱን ፡ ስላንተ ፡ ስጣቸው ።

8 ቅዱስ ፡ ጴጥሮስ ፡ ሥጋውና ፡ ነፍሱ ፡ በጽኑ ፡ መንፈርስ ፡ መጋደልን ፡ ተጋድ ለው ፡ ስለ ፡ ፍርሀት ፡ ሥጋው ፡ ድል ፡ በመሆኑ ፡ ጌታውን ፡ አላውቀውም ፡ ብሎ ፡ ባፉ ፡ ብቻ ፡ ተናገረ ፡ እንጂ ፡ ጌታው ፡ መሆኑንና ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ መሆኑን ፡ በልቡ ፡ አልካደም ፤ ስለዚህ ፡ ፈራ ፤ ተርበደበደ ፡ ዘላበደ ።

9 በባሕር ፡ ላይ ፡ ተወረወረና ፡ እየዋኘ ፡ ወጣ ።

10 እኔ ፡ ግን ፡ ተከሳሹ ፡ ከከሳሾቹ ፡ ጋራ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ተቋቁሞ ፡ ወንጀለኛ ፡ ነው ፡ ለተባለበት ፡ ነገር ፡ ምላሽ ፡ የሚሰጥበት ፡ ጊዜ ፡ ሳያገኝና ፡ ሳይናገር ፡ በሌለበት ፡ ይፈረድበት ፡ ዘንድ ፡ የሮማውያን ፡ ወግ ፡ አይደለምና ፡ ብትፈቅዱ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ቂሳርያ ፡ ወርዳችሁ ፡ ከዚያ ፡ ተፋረዱት ፡ አልኋቸው ።

<u>ድርብርብ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡-</u> ድርብርብ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ከሁለት ፡ ከሚበልጡ ፡ ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ የማመደብ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ነው ።

<u>አስረጅ ፡-</u> 1 ጀንበሯ ፡ ጠለቀች ፤ ዝናሙ ፡ መጣ ፤ እንግዴህ ፡ ወዴት ፡ ሄጄ ፡ አድራለሁ ?

2 ፈለቀና ፡ እየለ ፡ ከፉኛ ፡ ተጣልተዋል ፡ ስለዚህ ፡ እነርሱን ፡ ለማስታረቅ ፡ አስቢያለሁ ፤ አንተንም ፡ ለሽምግልና ፡ እፈልግሃለሁ ።

፫ ፡ ይህ ፡ ቦታ ፡ ለዶሮች ፡ በጣም ፡ ተስማሚ ፡ ነው ፡ ዕንቍላልም ፡ እንደ ፡ ልባቸው ፡ ለመጣል ፡ ይችላሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በዚሁ ፡ ቀበሌ ፡ ዕንቍላል ፡ ርካሽ ፡ ነው ።

፬ ፡ ወይፈኑ ፡ ወገሽ ፤ ያኛውም ፡ በሬ ፡ አንካሰ ፡ በዚህኛው ፡ ብቻ ፡ ለማረስ ፡ አይቻልም ፤ ስለዚህ ፡ በዶማ ፡ መቆፈር ፡ ይሻልሃል ።

ማስገንዘቢያ ፡- ምንም ፡ እንኳ ፡ ስልትና ፡ ዐይነት ፡ በትርጓሜ ፡ ቢመሳሰሉ ፡ ያረፍተ ፡ ነገር ፡ ዐይነት ፡ የምንለው ፡

፩ ፡ ነጠላን ፡
፪ ፡ ድርብን ፡
፫ ፡ ድብልቅን ፡
፬ ፡ ድርብ ፡ ድብልቅንና ፡
፭ ፡ ድርብርብን ፡ ጠቅልሎ ፡ የሚይዘውን፡ ክፍል፡ ነው።

ያረፍተ ፡ ነገር ፡ ስልት ፡ የምንለው ፡ ግን ፡

፩ ፡ ሐተታዊ፡ አረፍተ፡ ነገርን፡
፪ ፡ ጥያቄያዊ፡አረፍተ፡ ነገርንና፡
፫ ፡ ትእዛዛዊ፡አረፍተ፡ ነገርን፡
፬ ፡ አጋናኝ ፡ » »
ነውና ፤

ልዩነታቸውን ፡ ደኅና ፡ አድርጎ ፡ መመልከት ፡ ያስፈልጋል ።

## ፲፭ኛ ፡ መልመጃ ፡

(ሀ) የሚከተሉትን ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ በያይነታቸውና ፡ በየስልታቸው ፡ አመልክት ።

1 ላቶ ፡ መንግሥቱ ፡ የሚያስፈልገውን ፡ ያህል ፡ መጻሕፍት ፡ ገዝቼ ፡ እልክለታለሁ ።

2 ልጁ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ በአእምሮው ፡ እየጎለመሰ ፡ ይሄዳል ።

3 ብዙ ፡ ልጆች ፡ እየተሰለፉ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ይሄዳሉ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ ከተማ ፡ ለከተማ ፡ ይንገላወዳል ።

4 አቶ ፡ ምናልኩለት ፡ ዘንድሮ ፡ ከዚህ ፡ መሬት ፡ ሠላሳ ፡ ዳውላ ፡ ስንዴ ፡ አፈሱለት ።

5 ሽፍቶቹ ፡ ባንድ ፡ ትልቅ ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ ሦስት ፡ መንገደኞች ፡ ገፈፉና ፡ ወደ ፡ ሰፈራቸው ፡ እየፈነደቁ ፡ ተመለሱ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እረኞች ፡ ተሰውረው ፡ አይተዋቸው ፡ ኖሮ ፡ ወደ ፡ ጣቢያ ፡ ሄደው ፡ ለፖሊሶች ፡ ነገሩ ፤ ወዲያውም ፡ የፖሊሶቹ ፡ አዛዥ ፡ በረኞቹ ፡ ጠቋሚነት ፡ እየተመራ ፡ ሄዶ ፡ እንዳሉ ፡ አፍሶ ፡ አመጣቸው ።

6 ስለ ፡ በሽታዬ ፡ ብዙ ፡ መድኀኒቶችን ፡ ገዝቼ ፡ ነበር ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ እስካሁን ፡ ድረስ ፡ የሚያቀልልኝ ፡ አጣሁ ።

7 መበደሉን ፡ ልጁ ፡ በድሎሃል ፤ ቢሆንም ፡ ይቅርታ ፡ እንድታደርግለት ፡ እለምንሃለሁ ።

8 ስላንተ ፡ ይቅርታ ፡ አደርግለታለሁ ፤ ቢሆንም ፡ ነገሩን ፡ እረሳው ፡ አይመስለኝም ።

7*

9 ደምሴ ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ይደክማል ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ድካሙ ፡ አልታወቀለትም፤ የሆነ ፡ ሆኖ ፡ እስከ ፡ መጨረሻው ፡ መታገሥ ፡ አለበት ።

(ለ) በሚከተሉት ፡ ያረፍት ፡ ነገር ፡ ዐይነቶች ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ሥራ ።

ከነዚህ ፡ ግሶች ፡ በስተቀር ፡ በሌላ ፡ እንዳትሠራ ።

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| ፈጀ ፡ | ቀባ ፡ | ተቆጨ ፡ | ጫረ ፡ | ገረፈ፡ ተናደደ፡ |
| ፉረ ፡ | ቆጋ ፡ | ጨረሰ ፡ | ተረተረ ፡ | ደነበቀ ፡ |
| ፈካ ፡ | ቀዳ ፡ | አቃጠለ ፡ | ለፋ ፡ | ሞላ ፡ |
| ጣረ ፡ | ቀጨ ፡ | ቆፈረ ፡ | ለቀለቀ ፡ | ሰበረ ፡ |

፩ ፡ ድርብ ፡ ድብልቅ ፡
፪ ፡ ድብልቅ ፡
፫ ፡ ድርብ ፡
፬ ፡ ነጠላ ፡

(ሐ) ባራቱም ፡ የግስ ፡ ስልቶች ፡ በነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ አንዳንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራ ።

(መ) ሁለት ፡ ድብልቅና ፡ ሁለት ፡ ድርብ ፡ ድብልቅ ፡ ዐረፍተ ፡ ነገሮችን ፡ ሥራና ፡ በየሐረግ ፡ ዐይነታቸው ፡ ለይተህ ፡ አሳይ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ፡ መተንተን ።

## የነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ አተናተን ፡

መተንተን ፡ ማለት ፡ ባንድነት ፡ ተገጣጥመው ፡ የሚነገሩትን ፡ ቃላት ፡ ብትን ትን ፡ ወይም ፡ ልይትይት ፡ አድርጎ ፡ ክፍል ፡ ክፍላቸውን ፡ ማመልከት ፡ ነው ።

አሁን ፡ በመዠመሪያ ፡ የምንማረው ፡ ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገርን ፡ ከሁለት ፡ ላይ ፡ መክፈልን ፡ ነው ።

**አስረጅ ፡**

1 ንብ ፡ ማርን ፡ ትሠራለች ።
2 ጠረጴዛው ፡ አልተወለወለም ።
3 ሽልምልሙን ፡ ሳሕን ፡ ከጠረጴዛው ፡ ላይ ፡ አንሺው ።
4 ቀይ ፡ ዳማ ፡ ፈረስ ፡ እገዛልሃለሁ ።
5 እውነተኛ ፡ ዕውቀት ፡ በቀላል ፡ አይገኝም ።
6 ሰውን ፡ ማመስገን ፡ በፊት ፡ መርምሮ ፡ ነው ።

## ሰንጠረዥ ፡ 1 ፡

ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገርን ፡ ከሁለት ፡ ከፍሎ ፡ የሚያሳይ ፡

| ተ ፡ ቍጥር ፡ | ባለቤት ፡ ከነንዙ ፡ | አንቀጽ ፡ ከነንዙ ፡ |
|---|---|---|
| 1 | ንብ ፡ | ማርን ፡ ትሠራለች ፡ |
| 2 | ጠረጴዛው ፡ | አልተወለወለም ፡ |
| 3 | አንች ፡ | ሽልምልሙን ፡ ሳሕን ፡<br>ከጠረጴዛው ፡ ላይ ፡ አንሺው ፡ |
| 4 | እኔ ፡ | ተይ ፡ ዳግ ፡ ፈረስን ፡<br>እገዛልሃለሁ ፡ |
| 5 | እውነተኛ ፡ ዕውቀት ፡ | በቀላል ፡ አይገኝም ፡ |
| 6 | ሰውን ፡ ማመስገን ፡ | በረት ፡ መርምር ፡ ነው ፡ |

ከዚህ ፡ በላይ ፡ በተሰጠው ፡ ሰንጠረዥ ፡ ባለቤት ፡ ከነንዙ ፡ ወይም ፡ ከነገላጮቹና ፡ አንቀጽ ፡ ከነንዙ ፡ ወይም ፡ ከነገላጮቹ ፡ እየሆኑ ፡ ከሁለት ፡ ላይ ፡ ተከፍለው ፡ ነበር፤ አሁን ፡ ግን ፡ አራቱንም ፡ ለየብቻቸው ፡ አድርገን ፡ በሚከተለው ፡ ሰንጠረዥ ፡ እናሳያለን ።

አስረጅ ፡

1 ማናቸውም ፡ መሬት ፡ ዕፀዋትንና ፡ አዝርዕትን ፡ ለማብቀል ፡ ምግብን ፡ ይፈልጋል ።
2 ዕፀዋት ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ እንስሳት ፡ ያድጋሉ ።
3 የሳይንስ አስተማሪአችን ፡ በየቀኑ ፡ ጅምናስቲክን ፡ ይሠራል ።
4 አዳኙ ፡ ካንድ ፡ ሰዓት ፡ በፊት ፡ በዚህ ፡ አለፈ ።
5 ትንሹቱ ፡ ልጅ ፡ በፍጥነት ፡ ወደ ፡ ጨዋታዋ ፡ ሄደች ።
6 ብዙ ፡ ጥቋቍር ፡ ላሞች ፡ በጥጋቱ ፡ ላይ ፡ ይግጣሉ ።
7 ሽረኛ ፡ እረኛ ፡ የከብቶቹን ፡ መውጣትና ፡ መግባት ፡ ብቻ ፡ ይመለከታል ።
8 በዚህ ፡ ገደማ ፡ ድንግል ፡ መሬት ፡ አይገኝም ።

## ሰንጠረዥ ፡ 2 ፡

ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገርን ፡ ከሁለት ፡ ላይ ፡ ከፍሎ ፡ የሚያሳይ ፡

| ተራ ፡ ቍጥር ፡ | ባለቤት ፡ ከነንዙ ፡ | | አንቀጽ ፡ ከነንዙ ፡ | |
|---|---|---|---|---|
| | ባለቤት ፡ | የባለቤት ፡ ገላጭ ፡ | ማመሪያ ፡ አንቀጽ ፡ | ያንቀጽ ፡ ገላጭና ፡ ተሳባቢ ፡ |
| 1 | መሬት ፡ | ማናቸውም ፡ | ይፈልጋል ፡ | 1 ቤቱ ፡ ምግብን ፡<br>2 ዕፀዋትንናአዝርዕትንለማብቀል |
| 2 | ዕፀዋት | ሁሉ ፡ | ያድጋሉ ፡ | እንደ ፡ እንስሳት ፡ |
| 3 | አስተማሪ ፡ | 1 የሳይንስ ፡<br>2 አችን ፡ | ይሠራል ፡ | 1 በየቀን ፡ በቀኑ ፡<br>2 ጅምናስቲክን ፡ |
| 4 | አዳኝ ፡ | ካዕብ ፡ ፊደል ፡ | አለፈ ፡ | 1 ካንድ ፡ ሰዓት ፡ በፊት ፡<br>2 በዚህ ፡ |
| 5 | ልጅ ፡ | ትንሹቱ ፡ | ሄደች ፡ | በፍጥነት ፡ ወደ ፡ ጨዋታዋ ፡ |
| 6 | ላሞች ፡ | ብዙ ፡ ጥቋቍር ፡ | ይግጣሉ ፡ | በጥጋቱ ፡ ላይ ፡ |
| 7 | እረኛ ፡ | ሽረኛ ፡ | ይመለከታል ፡ | የከብቶቹን፡መውጣትና፡መግባት፡ብቻ፡ |
| 8 | መሬት ፡ | ድንግል ፡ | አይገኝም ፡ | በዚህ ፡ ገደማ ፡ |

ከማይሻገር ፡ ግስ ፡ ክፍል ፡ የመሆን ፡ ግስ ፡ ራሱን ፡ ያልቻለ ፡ ስለ ፡ ሆነ፡መሙሊያ ፡ያስፈልገዋል፤ ስለዚህ፡ አገባቡና፡አተናተኑን፡በሚከተለው፡በንጠረዥ፡ ተመልከት።

አስረጅ ፡

1 ዘለቀ ፡ ቅን ፡ ልጅ ፡ ነው ።
2 ትዳሩን ፡ ለማሸነፍ ፡ ጥረቱ ፡ ትልቅ ፡ ነው ።
3 ልጆችን ፡ ማስተማር ፡ ታላቅ ፡ ሥራ ፡ ነው ።
4 የዚህ ፡ ከተማ ፡ መሐንዲስ ፡ እርሱ ፡ ነው ።
5 አየለ ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ገር ፡ ነው ።
6 አሰፋ ፡ አጭር ፡ ነው ።
7 ቀይ ፡ ዶሮ ፡ ውድ ፡ ነው ።
8 የዛሬ ፡ ምሳችን ፡ እንኩቶ ፡ ነው ።
9 እነዚያ ልጆች ፡ ግብረ ፡ ገቦች ፡ ናቸው ።
10 እኔ ፡ በሩጫ ፡ ረገድ ፡ (በኩል ) ፡ ደካማ ፡ ነኝ ።

ሰ ን ጠ ረ ዥ ፡ 3 ፡

በመሆን ፡ ግስ ፡ የተሠራውን ፡ ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ አተናተን ፡ የሚያመለክት ፡

| ተራ ፡ ቍጥር፡ | ባለቤት ፡ | | አንቀጽ ፡ | |
|---|---|---|---|---|
| | ባለቤት ፡ | የባለቤት ፡ ገላጭ፡ | ማሰሪያ ፡አንቀጽ፡ | የአንቀጽ ፡ መሙሊያ ፡ |
| 1 | ዘለቀ ፡ | | ነው ፡ | ቅን ፡ ልጅ ፡ |
| 2 | ጥረቱ፡ | ትዳሩን ፡ በማሸነፍ ፡ | » | ትልቅ፡ |
| 3 | ልጆችንማስተማር | | » | ታላቅ ፡ ሥራ ፡ |
| 4 | መሐንዲስ ፡ | የዚህ ፡ ከተማ ፡ | » | እርሱ ፡ |
| 5 | አየለ ፡ | | ነው ፡ | እጅግ ፡ በጣም ፡ ገር ፡ |
| 6 | አሰፋ ፡ | | » | አጭር ፡ |
| 7 | ዶሮ ፡ | ቀይ ፡ | » | ውድ ፡ |
| 8 | ምሳ ፡ | የዛሬ ፡ አችን ፡ | » | እንኩቶ ፡ |
| 9 | ልጆች ፡ | እነዚያ ፡ | ናቸው | ግብረ ፡ ገቦች ፡ |
| 10 | እኔ፡ | | ነኝ ፡ | በሩጫ ፡ ረገድ ፡ ደካማ፡ |

ከዚህ ፡ በፊት ፡ በሁለተኛው ፡ ሰንጠረዥ ፡ ውስጥ ፡ ተሻጋሪ ፡ ግሶች ፡ ስለ፡ ነበሩ፡ ቀጥተኛም ፡ ተሳቢዎች ፡ ነበሩ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በዚያ ፡ ክፍል ፡ ባለቤቱንና ፡ የባለቤቱን ፡ ገላጭ ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጹንና ፡ የማሰሪያ ፡ አንቀጹን ፡ ገላጭ፡ እየከፋፈልን ፡ ለማሳየት፡ ብቻ ፡ ስለ ፡ ነበር ፡ ተሳቢዎቹን ፡ ለብቻቸው ፡ ሳናወጣቸው ፡ ቀርተው ፡ ነበር ፤ አሁን ፡ ግን ፡ አውጥተናቸዋልና ፤ በሚከተለው ፡ ተመልከት ።

<u>አስረጅ ፡</u>

1 ወዴላው ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ በመንሸራተቱ ፡ በቅሎዪቱን ፡ ገጠባት ።

2 ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ዓለምን ፡ መነኑ ፡ ( ናቁ) ።

3 መንግሥቱ ፡ በጦር ፡ ሯጩን ፡ ድኾላ ፡ ከመሬት ፡ ጋራ ፡ ሰፋው ።

4 ፈለቀ ፡ ቀይ ፡ ቀዩን ፡ ሥጋ ፡ ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ ቆነቆነው ።

## <u>ሰንጠረዥ ፡ 4፡</u>

### ቀጥተኛ ፡ ተሳቢን ፡ ለብቻው ፡ የሚያሳይ ፡

| ተራ ፡ ቍጥር፡ | ባለቤት፡ | | አንቀጽ ፡ | | |
|---|---|---|---|---|---|
| | ባለቤት ፡ | የባለቤት፡ ገላጭ ፡ | ማሠሪያ፡ አንቀጽ፡ | ቀጥተኛ ፡ ተሳቢ ፡ | ያንቀጽ ፡ ገላጭ ፡ |
| 1 | ወዴላው ፡ | | ገጠባት ፡ | በቅሎዪቱ'ን ፡ | ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ በመንሸራተቱ ፡ |
| 2 | ሰዎች ፡ | ብዙ ፡ | መነኑ ፡ | ዓለምን ፡ | |
| 3 | መንግሥቱ ፡ | | ሰፋው ፡ | ሯጩን ፡ ድኾላ ፡ | በጦር ፡ ከመሬት ፡ ጋራ ፡ |
| 4 | ፈለቀ ፡ | | ቆነቆነው ፡ | ቀይ ፡ ቀዩን ፡ ሥጋ፡ | ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ |

ቀጥተኛ ፡ ተሳቢ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ገላጩን ፡ አስከትሎ ፡ ይገባል ።

<u>አስረጅ ፡</u>

1 አቢላሙ ፡ ማጋዋን ፡ ላም ፡ ጋዳት ፡ አቢላሙ ፡ ዐመለኛዋን ፡ ላም ፡ ወደራት ።

2 አስተማሪው ፡ በትርፍ ፡ ጊዜው ፡ አትክልቱን ፡ ይኮተኩታል ።

## <u>ሰንጠረዥ ፡ 5 ፡</u>

### የቀጥተኛን ፡ ተሳቢ ፡ ገላጭ ፡ የሚያሳይ ፡

| ተራ ፡ ቍጥር፡ | ባለቤት ፡ | | አንቀጽ ፡ | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|
| | ባለቤት ፡ | የባለቤት ፡ ገላጭ፡ | ማሰሪያ አንቀጽ | ተሳቢ ፡ | የተሳቢ፡ ገላጭ፡ | ያንቀጽ ፡ ገላጭ ፡ |
| 1 | አቢላም ፡ | ካዕብ፡ ፈደል ፡ | ጋዳት ፡ | ላም ፡ | ማጋዋን ፡ | |
| 2 | አስተማሪ ፡ | ው | ይኮተኩታል ፡ | አትክልትን ፡ | ካዕብ ፡ ፈደል ፡ | በትርፍ፡ ጊዜው፡ |

ተሻጋሪ ፡ ግስ ፡ የመስጠትን ፡ ምግባር ፡ እየገለጸ ፡ የሚሰጠውን ፡ ዕቃ ፡ በቀጥታ ፡ ያመለክታል ። በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ተቀባዩ ፡ መስተዋድድ ፡ ጉድሎት ፡ የተገኘ ፡ እንደሆን ፡ ኢርቱዕ ፡ ተሳቢ ፡ ይሆናል ።

<u>አስረጅ</u> ፡

1 ዛሬ ፡ አስተማሪዎቻችን ፡ አንዳንድ ፡ ደብተር ፡ አደሉን ።
2 ለሠርግህ ፡ ሁለት ፡ ሰንጎችን ፡ ያስመጣልሃል ።
3 አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ ለይስሙላ ፡ ገንዘባቸውን ፡ ይናኙላቸዋል ።
4 ወንድሜ ፡ አንድ ፡ የኪስ ፡ ብርዕን ፡ (ወንዩ) ፡ ላከልኝ ።

## <u>ሰንጠረዥ ፡ 6 ፡</u>

### ኢርቱዕ ፡ ተሳቢን ፡ የሚያመለክት ።

| ተራ ፡ | ባለቤት ፡ | | አንቀጽ ፡ | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|
| ተቁጥር፡ | ባለቤት ፡ | የባለቤትገላጭ | ግስራያ አንቀጽ | ኢርቱዕ፡ ተሳቢ | ቀጥተኛ፡ተሳቢ | ያንቀጽ ፡ ገላጭ ፡ |
| 1 | አስተማሪዎች፡ | አችን ፡ | አደሉ ፡ | ን ፡ | አንዳንድ፡ደብተር፡ | ዛሬ ፡ |
| 2 | እርሱ ፡ | | ያስመጣል ፡ | ልህ ፡ | ሁለት፡ሰንጎች፡ | ለሠርግህ ፡ |
| 3 | ሰዎች ፡ | አንዳንድ ፡ | ይናኙአል ፡ | ልአቸው ፡ | ገንዘባቸውን ፡ | ለይስሙላ ፡ |
| 4 | ወንድም ፡ | ዬ ፡ | ላከ ፡ | ልኝ ፡ | አንድ፡የኪስ፡ብርዕ፡ | |

ተሻጋሪ ፡ ገቢር ፡ ግስ ፡ ያለባዕድ ፡ መነሻ ፡ ወይም ፡ መድረሻ ፡ ረዳትነት ፡ እየተ ነገረ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ያንቀጽን ፡ መሙሊያ ፡ (አረጋጋጭ ) ፡ ሲፈልግ ፡ ይታያል ።

<u>አስረጅ</u> ፡

1 አቶ ፡ መንግሥቱ ፡ ልጃቸውን ፡ ገብሬ ፡ አደረጉት ።
2 ተክለ ፡ አብ ፡ ብርዑን ፡ ጎባጣ ፡ አደረገው ።
3 አፄ ፡ ምኒልክ ፡ በዐድዋ ፡ ጦርነት ፡ ላይ ፡ ጣሊያንን ፡ ድል ፡ አደረጉት ።
4 ዳኛው ፡ ተከሳሹን ፡ በድሉ ፡ አገኘው ።

<u>ማስገንዘቢያ</u> ፡

አንዳንድ ፡ ያማርኛ፡ ተሻጋሪ፡ ግሶች ፡ ራሳቸውን ፡ መቻል ፡ እያቃታቸው ፡ መሙ ሊያን ፡ ይፈልጋሉ ። ስለዚህ ፡ የነዚህን ፡ ግሶች ፡ ስሜት ፡ ለመሙላት ፡ የሚዉመ ሩት ፡ ቃላት ፡ መሙሊያ ፡ ይባላሉ ። ነገር ፡ ግን፡ ሊቃውንት ፡ ግዕዙን ፡ እየጠቀሱ ፡ መሙ ሊያ ፡ መባላቸው ፡ ቀርቶ ፡ ቀጥተኛ ፡ ተሳቢ ፡ ይባሉ ፡ ይላሉ። እንደዚህም ፡ ማለታቸው፡ አንቀጾቹ ፡ ድርብ ፡ ተሳቢዎችን ፡ የሚፈልጉ ፡ ናቸው ፡ በማለት ፡ ነው ። ይሁን ፡ እንጂ ፡ የተደረበውን ፡ ተሳቢ ፡ ነጥሉ ፡ ከርፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ሲያወጡት ፡ ያንቀጹ ፡ ግብር ፡ የተጓደለ ፡ ስለሚሆን ፡ መሙሊያነቱን ፡ አይለቅምና ፤ ድርብ ፡ ተሳቢ ፡ እንዳልሆነ ፡ አስተውል ።

## ሰንጠረዥ፡ 7፡

### ልዩ ፡ ያንቀጽ ፡ መሙሊያን ፡ የሚያሳይ ፡

| ተራ ቍጥር | ባለቤት ፡ | | አንቀጽ ፡ | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|
| | ባለቤት ፡ | የባለቤት ገላጭ | ማሰሪያአንቀጽ | ቀጥተኛ፡ተሳቢ | መሙሊያ ፡ | ያንቀጽ ፡ ተጨማሪ ፡ |
| 1 | አቶ፡ መንግሥቱ ፡ | | አደረጉ ፡ | ልጃቸውን<br>ት | ገበሬ ፡ | |
| 2 | ተክለ ፡ አብ ፡ | | አደረገ ፡ | ብርዑን<br>ው | ጎባጣ ፡ | |
| 3 | አፄ ፡ ምኒልክ ፡ | | አደረጉ ፡ | ጣሊያንን<br>ት | ድል ፡ | በዐድዋ፡ጦርነት፡ላይ |
| 4 | ዳኛው ፡ | ው | አገኘው ፡ | ተከሳሹን ፡ | በድሎ ፡ | |

በተሻጋሪና፡በማይሻገሩ፡ግሶች፡የሚሠሩት፡አረፍተ፡ነገሮች፡ባንድነት፡ይተነተናሉ ።

**አስረጅ ፡**

1 ካንዳርጌ ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ አምስት ፡ ብር ፡ መነተፈ ።
2 እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ማለት ፡ ከኃጢአት ፡ መራቅ ፡ ማለት ፡ ነው ።
3 ረዥሙ ፡ ልጅ ፡ ዘወትር ፡ ለትምህርቱ ፡ ይፍጨረጨራል ።
4 ይህ ፡ ቦዳ ፡ መሬት ፡ ባምስት ፡ ዓመት ፡ በመቅለዙ ፡ እገረማለሁ ።
5 እሳት ፡ ፋልማውን ፡ አንቀረቀበው ።
6 ብልኍ ፡ ገበሬ ፡ የጤፉን ፡ ድከን ፡ በሰዓቱ ፡ ይጎቻል ።

## ሰንጠረዥ ፡ 8 ፡

| ተራ ፡ ቍጥር ፡ | ባለቤት ፡ | የባለቤት ፡ ገላጭ ፡ | አንቀጽ ፡ | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|
| | | | ማሰሪያአንቀጽ | ተሳቢ፡ከነጓዙ፡ | መሙሊያ ፡ | ያንቀጽ፡ገላጭ ፡ |
| 1 | እርሱ ፡ | | መነተፈ ፡ | አንድ ፡ አም ስት ፡ ብር ፡ | | ካንዳርጌ፡ ላይ ፡ |
| 2 | እግዚአብሔርን፡መፍራት፡ ማለት ፡ | | ነው ፡ | | ከኃጢአት፡ መ ራቅ ፡ ማለት ፡ | |
| 3 | ልጅ ፡ | ረዥሙ ፡ | ይፍጨረ ጨራል ፡ | | | ዘወትር፡ ለትም ህርቱ ፡ |
| 4 | እኔ ፡ | | እገረማለሁ፡ | | | ይህ ፡ በመቅ ለዙ ፡ - - - - |
| 5 | እሳት ፡ | | አንቀረቀበው ፡ | ፋልማውን፡ | | |
| 6 | ገበሬ ፡ | ብልኍ ፡ | ይጎቻል ፡ | የጤፉን፡ድከን፡ | | በሰዓቱ ፡ |

## የድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ አተናተን ።

ድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገርን ፡ ከመተንተናችን ፡ በፊት ፡ መደበኛውንና ፡ ጥገኛውን ፡ ሐረግ ፡ እየለየን ፡ ጽፈን ፡ የጥገኛውን ፡ ሐረግ፡ ሙያ ፡ እንዘረዝራለን ፤ መደበኛው፡

ሐረግ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ሙሉ ፡ የለውም ፡ ይሁን ፡ እንጂ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ የማለት ፡ ግስ ፡ ይሰበዋል ። የሆነ ፡ ሆኖ ፡ በጠቅላላው ፡ አስተያየት ፡ ስንገምት ፡ ጥገኛው ፡ ሐረግ ፡ ሙሉ ፡ ሲኖረው ፡ መደበኛው ፡ ሐረግ ፡ ሙሉ ፡ የለውም ፡ ብለን ፡ እንገምታለን ።

የሚከተሉትን ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ በመደበኛና ፡ በጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ሥር ፡ እየለየን ፡ ጽፈን ፡ የጥገኛውን ፡ ሐረግ ፡ ሙሉ ፡ እናሳያለን ።

1 የዛሬ ፡ አሥራ ፡ አምስት ፡ ቀን ፡ የተከልኸው ፡ ባሕር ፡ ዛፍ ፡ ጠደቀ ።

2 ሰውዬውን ፡ ወደ ፡ አፋፉ ፡ ሳይደርስ ፡ በሩጫ ፡ ለጥቀህ ፡ ጥራው ።

3 መብራት ፡ ማናቸውንም ፡ ሰው ፡ እየመራ ፡ ወደሚፈልግበት ፡ ሥፍራ ፡ ይወስደዋል ።

4 የማትጠገበው ፡ ምክሩ ፡ አንገቶት ፡ ራስ ፡ ስለምታደርግ ፡ የተጠሙ ፡ ሰዎች ፡ ይረኩባታል ።

5 በማናቸውም ፡ ጊዜ ፡ ለሚቀርብለት ፡ ጥያቄ ፡ መልስ ፡ አያጣም ።

6 በዚያ ፡ ጥቅጥቅ ፡ ደን ፡ ውስጥ ፡ ብታቋርጥ ፡ ካንበሳ ፡ በስተቀር ፡ ሌላ ፡ አስጊ ፡ አውሬ ፡ አይገጥምህም ።

7 አንድ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ እስከሚሞትበት ፡ ጊዜ ፡ ድረስ ፡ እውነተኛ ፡ የልብ ፡ ዕረፍትን ፡ አያገኝም ።

8 ከፋልማው ፡ መሬት ፡ አራት ፡ ጥንድ ፡ ብቆርጥልህ ፡ ይበቃሃል ።

9 አስፋው ፡ የፈለቀን ፡ ጥጥ ፡ እንዳስበላ ፡ ጓደኞቹ ፡ ተናግረውበታል ።

10 ደጃዝማች ፡ በየነን ፡ በማይ ፡ ጨው ፡ሜዳ ፡ ላይ ፡ የጀብዱ ፡ ሥራ ፡ የሠሩትን ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ ያውቃቸዋል ።

11 ልጁ ፡ በሥራው ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ።

12 ፈለቀች ፡ ትናንትና ፡ ራሷ ፡ እስኪዞር ፡ ድረስ ፡ አጠናች ።

13 አባቶቻችን ፡ በዚህ ፡ ወርካ ፡ ሥር ፡ የነበረውን ፡ ምንጭ ፡ በሙቀጫ ፡ እንደ ፡ ደፈኑት ፡ ሰማን ።

14 በኩሬ ፡ አጠገብ ፡ የተሠራ ፡ ቤት ፡ በክረምት ፡ ወራት ፡ ይወረዛል ።

15 ከመኪና ፡ ይልቅ ፡ የጋሪ ፡ ወጪ ፡ ይበልጣል ።

16 በቤታችን ፡ አጠገብ ፡ ያለችው ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ባልታሰበ ፡ ሰዓት ፡ አበበች ።

17 ወርቅነህ ፡ በሄደበት ፡ ያለችግር ፡ ይለምዳል ።

| መደበኛ ፡ ሐረግ ፡ | ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ |
| --- | --- |
| 1 ባሕር ፡ ዛፍ ፡ ጠደቀ | የዛሬ ፡ አሥራ ፡ አምስት ፡ ቀን ፡ የተከልኸው ፡ ሙሉው ፡ ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ባሕር ፡ ዛፍ ፡ የሚለውን ፡ ስም ፡ ይገልጻል ። |

| | |
|---|---|
| 2 ሰውዬውን፡ በሩጫ፡ ለጥቀህ ፡ ጥራው ፡ | ወደ ፡ አፋፉ ፡ ሳይደርስ ፡<br>ሙያው፡- ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡<br>ጥራው ፡ የሚለውን ፡ አንቀጽ ፡ ይገልጻል ። |
| 3 መብራት ፡ ወደ ፡ ሥፍራ ፡ ይወስዳል ። | የሚፈልግበት ፡<br>ሙያው፡- ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡<br>ሥፍራ ፡ የሚለውን ፡ ስም ፡ ይገልጻል ። |
| መደበኛ ፡ ሐረግ ፡ | ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡<br>ማናቸውንም ፡ ሰው ፡ እየመራ ፡<br>ሙያው ፡ ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡<br>ይወስዳል ፡ የሚለውን፡ አንቀጽ ፡ ይገልጻል። |
| 4 ሰዎች ፡ ይረኩበታል ። | የማትጠገበው ፡<br>ሙያው ፡ ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ምክሩ ፡<br>የሚለውን ፡ ስም ፡ ይገልጻል ።<br>ምክሩ ፡ አንዠትን ፡ ራስ ፡ ስለምታደርግ ፡<br>ሙያው ፡ ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡<br>ይረኩባታል ፡ የሚለውን ፡ አንቀጽ ፡ ይገል<br>ጻል ።<br>የተጠሙ ፡<br>ሙያው ፡ ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ሰዎች ፡<br>የሚለውን ፡ ስም ፡ ይገልጻል ። |
| 5 በማናቸውም፡ ጊዜ፡ ለጥያቄ፡ መልስ ፡ አያጣም ። | የሚቀርብለት ፡<br>ሙያው ፡ ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡<br>ጥያቄ ፡ የሚለውን ፡ ስም፡ ይገልጻል ። |
| 6 ካንበሳ፡በስተቀር፡ሌላ፡ አስጊ፡ አውሬ ፡ አይገጥምህም ። | በዚያ ፡ ጥቅጥቅ ፡ ደን ፡ ውስጥ ፡ ብታቋርጥ ፡<br>ሙያው ፡ ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡<br>አይገጥምህም፡ የሚለውን፡ ግስ ፡ ይገልጻል ። |
| 7 አንድ፡ ነፍስ፡ገዳይ፡እስከ፡ጊዜ፡ድረስ፡ እውነተኛ፡የልብ፡ዕረፍትን፡ አያገኝም። | የሚሞትበት ፡<br>ሙያው ፡ ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ጊዜ ፡<br>የሚለውን ፡ ስም ፡ ይገልጻል ። |
| 8 ይበቃሃል ። | ከፋልማው፡ መሬቱ ፡ አራት ፡ ጥንድ ፡ ብቆ<br>ርጥልህ ፡<br>ሙያው ፡ ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡<br>ይበቃሃል፡ የሚለውን፡ አንቀጽ ፡ ይገልጻል ። |
| 9 ጓደኞቹ ፡ ተናግረውበታል ። | አስፋው ፡ የፈለቀን ፡ ጥጥ ፡ እንዳስበላ ፡ |

| | |
|---|---|
| | ሙያው ፡ ስማዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ የተናገረውበታል፡ አንቀጽ፡ ተሳቢ፡ ነው። |
| 10 ደጃዝማች፡ በየነን፡ ማንም፡ሰው፡ያውቃቸዋል። | በማይ፡ ጨው፡ ሜዳ፡ላይ፡ የጀብዱ፡ ሥራ፡ የሠሩትን ፡ ሙያው ፡ ተጣማሪ ፡ ጥገኛ፡ ሐረግ ፡ ተጣ ማሪነቱም፡ ለመደበኛው፡ሐረግ፡ ባለቤት ፡ ለደጃዝማች ፡ በየነ ፡ ነው ። |
| 11 ልጁ፡ በሥራው፡ (ምስጉን) ነው ። | የተመሰገነ ፡ ሙያው ፡ ስማዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ የነው ፡ የማሰሪያ ፡ አንቀጹ ፡ መሙሊያ ፡ ነው ። |
| 12 ፈለቀች፡ ትናንትና፡ አጠናች። | ራሷ ፡ እስኪዞር ፡ ድረስ ፡ ሙያው፡ ተውሳከ፡ ግሳዊ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ የመደበኛውን ፡ ሐረግ፡ አንቀጽ ፡ አጠናችን ፡ ይገልጻል ። |
| 13 ሰማን ። | 1 አባቶቻችን ፡ ምንጩን ፡ በሙቀጫ ፡ እንደ ፡ ደፈኑት ፡ ሙያው፡ ስማዊ፡ ጥገኛ፡ ሐረግ ፡ የመደበኛ ው፡ሐረግ፡አንቀጽ፡የሰማን፡ተሳቢው፡ነው፤<br>2 በዚህ ፡ ወርካ ፡ ሥር ፡ የነበረውን ፡ ሙያው፡ ቅጽላዊ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ምንጭ፡ የሚለውን ፡ ስም ፡ ይገልጻል ። |
| 14 ቤት፡በክረምት፡ወራት፡ይወረዛል። | በኩሬ ፡ አጠገብ ፡ የተሠራ ፡ ሙያው ፡ ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ቤት ፡ የሚለውን ፡ ስም ፡ ይገልጻል ። |
| 15 የጋሪ ፡ ወጪ ፡ ይበልጣል ። | የመኪና ፡ ወጪ ፡ ከሚበልጥ ፡ ይልቅ ፡ ሙያው ፡ ተውሳከ፡ ግሳዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ፡ ይበልጣል ፡ የሚለውን ፡ የመደበኛውን ፡ ሐረግ ፡ አንቀጽ ፡ ይገልጻል ። |
| ፲፮ ጽጌ ፡ በ(የአልታሰበው) ሰዓት ፡ አበበች ። | 1 ያልታሰበው ፡ ሙያው ፡ ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ፡ ሐረግ፡ ሰዓት ፡ የሚለውን ፡ የመስተዋድዱን ፡ ተገዥ ፡ ይገልጻል ። |

17 ወርቅነህ፡ ያለችግር፡ (በ---) ይለምዳል ።

2 በቤታችን ፡ አጠገብ ፡ ያለችው ፡ ሙያው፡ ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ጽጌ ፡ የሚለውን ፡ ስም ፡ ይገልጻል ።

የሄደበት ፡ ሙያው ፡ ስማዊ፡ ጥገኛ፡ሐረግ ፡ የመስተ ዋድድ ፡ ተገኝ ፡ ነው ።

ማስገንዘቢያ፡- የ ፡ የሚ ፡ የማ ፡ የም ፡ የሚባሉትን ፡ ጥገኛ ፡ መስተፃምሮች ፡ እያንዳንዳቸ ውን ፡ መስተዋድድ ፡ ሲጫናቸው ፡ በውስጠ ፡ ታዋቂነት ፡ ቀርተው ፡ በጽሑፍ ፡ ይታ ጣሉ ፤ በምንተነትንበት ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ከጥገኛ ፡ ሐረጎች ፡ ጋራ ፡ አብረው ፡ ይጻፉሉ ፤ ምሳ ሌያቸውን ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ በተጻፉት ፡ በሦስተኛው ፡ ባምስተኛው ፡ በሰባተኛው ፡ ባሥራ ስድስተኛውና ፡ ባሥራ ፡ ሰባተኛው ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ ተመልከት ።

## የድርብ ፡ ድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ አተናተን ፡

አየለ ፡ በፈተና ፡ አንደኛ ፡ የሆነው ፤ ትናንትና ፡ ከቅንነት ፡ አገር ፡ ሲመጣ ፡አም ስት ፡ መቶ ፡ ብር ፡ በወረቀት ፡ ተጠቅሎ ፡ በመንገድ ፡ ዳር ፡ ወድቆ ፡ አገኘና ፡ ለቀበሌው፡ ፍርድ ፡ ቤት ፡ ወስዶ ፡ ሰጠ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የገንዘቡ ፡ ጌታ ፡ በማስታወቂያም ፡ በም ርምርም ፡ ስላልተገኘ ፤ የፍርድ ፡ ቤቱ ፡ ከሁለት ፡ ወር ፡ በኋላ ፡ መልሶ ፡ ሰጠው ።

መደበኛ ፡ ሐረግ ፡

1 አየለ፡ ለቀበሌው፡ ፍርድ፡ ቤት፡ ወስዶ ፡ ሰጠ ።

2 አምስት፡ መቶ፡ ብር፡በወረቀት፡ ተጠቅሎ፡በመንገድ፡ ዳር፡ ወድቆ፡ አገኘ።

3 የፍርድ ፡ ቤቱ ፡ ከሁለት ፡ ወር ፡ በኋላ ፡ መልሶ ፡ ሰጠው ።

ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡

1 በፈተና ፡ አንደኛ ፡ የሆነው ፡ አገባቡ ፡ ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ሆኖ ፡ አየለ ፡ የሚለውን ፡ የመደበኛውን ፡ ሐረግ ፡ ባለ ቤት ፡ ይገልጻል ።

2 ትናንትና፡ ከቅንነት ፡ አገር ፡ ሲመጣ፡ ተውሳከ፡ ግሳዊ፡ ጥገኛ፡ ሐረግ፡ ያንደኛውን፡ መደበኛ፡ሐረግ፡ማሰሪያ፡አንቀጽ፡ይገልጻል።

3 የገንዘቡ ፡ ጌታ ፡ በምርምርም ፡ በማስታወ ቂያም ፡ ስላለተገኘ ፡ ተ ፡ ግ ፡ ጥ፡ ሐተ፡ የሁለ ተኛውን ፡ መደበኛ ፡ ሐ ፡ ማ ፡ አ፡ ይገልጻል።

ማስገንዘቢያ ፡-

ላንደኛው፡መደበኛ፡ሐረግ፡ ባለቤት፡ በፈተና፡አንደኛ፡የሆነው፡የሚለው፡ ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ፡ ሐረግ፡ ቅጽሉ፡ነው፡ የተባለበት፡ ወደ፡ኋላ፡ተመልሶ፡ ባለቤቱን፡ ይገልጻል፡ በማለት፡ ነው፡እንጂ፤በእውነተኛው፡ አገባቡ፡እንደ፡ ተጣማሪ፡ባለቤት፡ ሳይሆን ፡ ቀርቶ ፡ አይደለም ።

ተጣማሪ ፡ ቃል ፡ ወይም ፡ ሐረግ ፡ ለሚጣመርለት ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ገላጭ ፡ ሆኖ ፡ የሚገባ፡ ነው ፤ ስለዚህ ፡ ተጣማሪ፡ ለሚጣመርለት፡ ቃል፡ ወይም፡ ሐረግ፡ ገላጭ ፡ ከሆነ ፡ በሚተነተንበት ፡ ጊዜ ፡ ክፍሉን ፡ በገላጭነት ፡ በቅጽል ፡ ውስጥ ፡ መጠቅለል ፡ ነው ።

፭ኛ ፡ ሰንጠረዥ ፡ ከፍተኛ ፡ የድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ መተንተኛ ፡

| | ሐረግ ፡ | የሐረግ፡ ዐይነት ፡ | የጥ፡ ሐረግ ሙያ | መስተፃም | ባለቤት ፡ | የባ ገላጭ ፡ | ግ ፡ አንቀጽ ፡ | ተሳቢ ፡ | የተሳቢ ገላጭ ፡ | መሙሊያ ፡ | ተውሳከ፡ግሳዊ፡ ተጨማሪ፡ |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| 1 | ሀ) ባሕር ፡ ዛፍ ፡ ጠደቀ ፡ | መደበኛ ፡ | | | ባሕር፡ ዛፍ፡ | | ጠደቀ ፡ | | | | |
| | ለ) የዛሬዐሥራአምስት፡ ቀን፡የተከልኸው | ጥገኛ፡ ሐ ፡ | ቅጽል፡ | የ(ጥ፡መፃ)፡ | አንተ ፡ | | ተከልኸው ፡ | | | | የዛሬ፡ዐሥራ፡ አምስት፡ቀን |
| 2 | ሀ) ሰውዬውን፡ በሩጫ፡ ለጥቀህ ፡ ጥራው፡ | መደበኛ ፡ | | | አንተ ፡ | በሩጫ፡ ለጥቀህ | ጥራው ፡ | ሰውዬ ውን ፡ | | | |
| | ለ) ወደ ፡ አፋፉ ፡ ሳይደርስ ፡ | ጥገኛ ፡ | ተ ፡ ግስ ፡ | ሳ (ጥ፡መፃ) | እርሱ ፡ | | ይደርሳል ፡ | | | | ወደ ፡ አፋፉ ፡ |
| 3 | ሀ) ሙብራት ፡ ወደ ፡ ሠፈር ፡ ይወስዳል ፡ | መደበኛ ፡ | | | ሙብራት ፡ | | ይወስዳል ፡ | እርሱን | | | ወደ ፡ ሠፈር ፡ |
| | ለ) ማንኛውንም ፡ ሰው ፡ እየመራ ፡ | ጥገኛ ፡ | ተ ፡ ግስ ፡ | እየ(ጥ መፃ) | እርሱ ፡ | | መራ ፡ | ሰው ፡ | ማንኛ ፡ | | |
| | ሐ) የሚፈለግበት ፡ | ጥገኛ ፡ | ቅጽል፡ | የሚ(ጥ መ) | እርሱ ፡ | | ይፈለግበታል ፡ | | | | |
| 4 | ሀ ) ሰዎች ፡ ይረኩበታል ፡ | መደበኛ ፡ | | | ሰዎች ፡ | | ይረካሉ ፡ | | | | በእርስዋ ፡ |
| | ለ) የማትጠገበው ፡ | ጥገኛ ፡ | ቅጽል ፡ | የም(ጥ፡መ) | እርሷ ፡ | | አትጠገብም ፡ | | | | |
| | ሐ) ምክሩ፡ አንዠት፡ ራስ፡ ስለምታደርግ፡ | » | ተ ፡ ግስ ፡ | ስለ ፡ » | ምክር ፡ | ካዕብ፡ | ራስታደርጋለች | አንጀት | | ራስ ፡ | |
| | መ) የተጠሙ ፡ | » | ቅጽል ፡ | የ » | እነርሱ ፡ | | ተጠሙ ፡ | | | | |
| 5 | ሀ) በማንኛውም ፡ ጊዜ፡ ለጥያቄ፡መልስ ፡ አያጣም ፡ | መደበኛ ፡ | | | እርሱ ፡ | | አያጣም ፡ | መልስ፡ | | | በማንኛውም፡ ጊዜ፡ለጥያቄ |
| | ለ) የሚቀርብለት ፡ | ጥገኛ ፡ | ቅጽል ፡ | የሚ(ጥ መ) | እርሱ ፡ | | ይቀርባል ፡ | | | | ለርሱ ፡ |
| 6 | ሀ) ካንበሳ ፡ በስተቀር ፡ ሌላ ፡ አውሬ ፡ አይገጥምህም ፡ | መደበኛ. | | | አውሬ ፡ | ሌላ ፡ | አይገጥምህም፡ | አንተን | | | ካንበሳ ፡ በስተቀር ፡ |
| | ለ) በዚህ፡ጥቅጥቅ፡ደን፡ውስጥ፡ብታቋርጥ፡ | ጥገኛ ፡ | ተ ፡ ግስ ፡ | ብ(ጥ መፃ) | አንተ ፡ | | ታቋርጣለህ ፡ | | | | በዚህ፡ጥቅጥቅ፡ደን፡ውስጥ |
| 7 | ሀ) አንድ፡ ነፍሰ፡ገዳይ፡ እስከ፡ጊዜ፡ ድረስ፡ እውነተኛ፡ የልብ፡ዕረፍትን፡ አያገኝም፡ | መደበኛ ፡ | | | ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ | አንድ ፡ | አያገኝም ፡ | ዕረፍ ትን ፡ | እውነተ ኛየልብ | | እስከ ፡ ጊዜ ፡ ድረስ ፡ |
| | ለ) (የ) ሚሞትበት ፡ | | ቅጽል ፡ | የሚ(ጥ መ) | እርሱ ፡ | | ይሞትበታል ፡ | | | | |
| 8 | ሀ) ይበቃሃል ፡ | መደበኛ ፡ | | | አንተ ፡ | | ይበቃሃል ፡ | | | | |
| | ለ) ከፋልማው ፡ መሬት ፡ አራት ፡ ጥንድ ፡ ብቆርጥልህ ፡ | ጥገኛ ፡ | ተ ፡ ግስ ፡ | ብ(ጥ፡ መፃ) | እኔ ፡ | | እቆርጣለሁ ፡ | ጥንድ ፡ | አራት ፡ | | ከፋልማው፡ መሬት፡ላንተ፡ |

## ፪ኛ ፡ ሰንጠረዥ ፡ ከፍተኛ ፡ የደብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ መተንተኛ ፡

| 1 ሐረግ ፡ | የሐረግ ፡ ዐይነት ፡ | የጥ፡ ሐረግ፡ ሙያ ፡ | መስተፃምር | ባለቤት ፡ | የባ ፡ ገላጭ ፡ | ማ፡ አንቀጽ | ተሳቢ ፡ | የተሳቢ ፡ ገላጭ ፡ | መሙሊያ ፡ | ተው ግስ፡ተጨ |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| (ሀ) አየለ፡ ለቀበሌው፡ ፍርድ፡ቤት ፡ ወስዶ ፡ ሰጠ ። | መደበኛ ፡ | | | አየለ ፡ | ለቀበሌው፡ ፍርድ፡ቤት፡ ወስዶ | ሰጠ ፡ | | | | |
| (ለ) በፈተና ፡ አንደኛ ፡ የሆነው ፡ | ጥገኛ ፡ | ተጣማሪ ፡ | የ (ጥ፡መፃ) | እርሱ ፡ | | ሆነ ፡ | | | አንደኛ ፡ | |
| (ሐ) ትናንትና ፡ ከቅንነት ፡ አገር ፡ ሲመጣ ፡ | » | ተውሳከ ፡ ግስ ፡ | ሲ(ጥ፡መፃ) | እርሱ ፡ | | መጣ ፡ | | | | ትናንትና ፡ ከቅንነት ፡ አገር ፡ |
| (መ) አምስት ፡ ሙቶ ፡ ብር ፡ በወረቀት ፡ ተጠቅልሎ ፡ በመንገድ ፡ ዳር ፡ ወድቆ ፡ አገኘ ። | መደበኛ ፡ | | ና(ወደረኛ) መፃ ፡ | እርሱ ፡ | | አገኘ ፡ | ብር ፡ | (ሀ) አምስት፡ ሙቶ (ለ)በወረቀት፡ተጠቅልሎ፡ በመንገድ፡ ዳር ፡ ወድቆ ፡ | | |
| (ሠ) ፡ የገንዘቡ ፡ ጌታ በማስታወቂያም ፡ በምርምርም፡ ስላልተገኘ ፡ | ጥገኛ ፡ | ተውሳከ ፡ ግስ ፡ | ስለ( ጥ ፡ መፃ) ፡ | ጌታ ፡ | የገንዘቡ ፡ | አልተገኘም | | | | በማስታወቂያም በምርምርም ፡ |
| (ረ) የፍርድ ፡ ቤቱ ፡ ከሁለት ፡ ወር፡ በኋላ ፡ መልሶ ፡ ሰጠው ፡፡ | መደበኛ ፡ | | ነገር ፡ ግን፡ (ወ) | ቤቱ ፡ | የፍርድ ከሁለት ወርበኋላ መልሶ | ሰጠው ፡ | | | | |

## ፫ኛ ፡ ሰንረጠዥ ፡ የድርብ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ መተንተኛ ፡

| | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| 1(ሀ) ሰው ፡ ባለማስተዋልና ፡ ባለመገንዘብ ፡ ያንዳንድ ፡ ነገሮችን ፡ እውነተኛ ፡ አገልግሎታቸውን ፡ በዝቅተኛነት ፡ ይገምተዋል ። | መደበኛ ፡ | | | ሰው ፡ | | ይገምተዋል ፡ | አገልግሎት ፡ | (ሀ) አቸውን ፡ (ለ) ያንዳንድ፡ ነገሮችን እውነተኛ ፡ | | ባለማስተዋልና ባለ መገንዘብ ፡ በዝቅተኛነት ፡ |
| (ለ) ይሁን ፡ እንጂ ፡ በነርሱ ፡ መጠቀሙን ፡ አይተውም ። | መደበኛ ፡ | | (ወደረኛ) ፡ ይሁን ፡ እንጂ ፡ | ሰው ፡ | | አይተውም | መጠቀሙን ፡ | | | በእነርሱ ፡ |

ባነስተኛ ፡ ሰንጠረዥ ፡ የሚተነተኑ ፡ ድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡

1 አስፋው ፡ የፈለቀን ፡ ጥጥ ፡ እንዳስበላ ፡ ጓደኞቹ ፡ ተናግረውበታል ።

2 ደጃዝማች ፡ በየነን ፡ በማይ ፡ ጨው ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ጀብዱ ፡ የሠሩትን ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ ያውቃቸዋል ።

3 ልጁ ፡ በሥራው ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ።

4 ፈለቀች ፡ ትናንትና ፡ ራሷ ፡ እስኪዞር ፡ ድረስ ፡ አጠናች ።

5 አባቶቻችን ፡ በዚህ ፡ ወርካ ፡ ሥር ፡ የነበረውን ፡ ምንጭ ፡ በሙቀጫ ፡ እንደ ፡ ደፈኑት ፡ ሰማን ።

6 በኩሬ ፡ አጠገብ ፡ የተሠራ ፡ ቤት ፡ በክረምት ፡ ወራት ፡ ይወረዛል ።

7 ከመኪና ፡ ወጪ ፡ ይልቅ ፡ የጋሪ ፡ ወጪ ፡ ይበልጣል ።

8 በቤታችን ፡ አጠገብ ፡ ያለችው ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ባልታሰበ ፡ ጊዜ ፡ አበበች ።

፩ኛ ፡ ሰንጠረዥ ፡ አነስተኛ ፡ የድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ መተንተኛ ፡

| ቍ | ባለቤት ፡ | የባለቤት ገ ፡ | ማሰሪያ ፡ አ ፡ | የማ ፡ አን ፡ ገ ፡ | ተሳቢ ፡ | የተሳቢ ፡ ገ ፡ | መሙሊያ ፡ |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| 1 | ጓደኞች ፡ | ካዕብ ፈደል | ተናግረ ዋል ፡ | በእርሱ ፡ | አስፋ፡የፈለቀን ጥጥ፡ እንዳስበላ | | |
| 2 | ሰው ፡ | ማንም ፡ | ያውቃቸ ዋል ፡ | | ደጃዝማች ፡ በየነን ፡ | በማይ ፡ ጨው፡ ሜዳ፡ ላይ፡ ጀብ ዱ፡ የሠሩትን ፡ | |
| 3 | ልጁ ፡ | | ነው ፡ | | | | በሥራው ፡ የተመሰገነ ፡ |
| 4 | ፈለቀች ፡ | | አጠናች ፡ | ትናንት፡ራሷ፡እ ስኪዞር፡ ድረስ፡ | | | |
| 5 | እኛ ፡ | | ሰማን ፡ | | አባቶቻችን ፡ ምንጩን፡ በሙ ቀጫ ፡ እንደ ፡ ደፈኑት ፡ | በዚህ ፡ ወርካ ፡ ስር፡ የነበረውን | |
| 6 | ቤት ፡ | በኩሬ፡ አጠ ገብ የተሠራ | ይወረዛል ፡ | በክረምት ፡ ወራት ፡ | | | |
| 7 | ወጪ ፡ | የጋሪ ፡ | ይበልጣል ፡ | የመኪና፡ ወጪ ከሚበልጥ ፡ ይልቅ ፡ | | | |
| 8 | ጽጌ ፡ | በቤታችን፡አጠ ገብ ፡ ያለችው ፡ | አበበች ፡ | ባልታሰበ ፡ ሰዓት ፡ | | | |

## ፲፮ኛ ፡ መልመጃ ፡

፩ኛ ፡ የሚከተሉትን ፡ ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ተንትናቸው ፡ (በሰንጠረዥ ፡ ዐቅድ) ፡

1 ዛሬ ፡ ሕፃኑ ፡ በጣም ፡ ተቅበጥብጧል ።

2 የቡሔ ፡ ዳቦ ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ እልክልሃለሁ ።

3 ወይዘሮ ፡ አይንኩኝ ፡ ልጅዋን ፡ በጉልበቱ ፡ አዳሪ ፡ አደረገችው ።

4 መንግሥቱ ፡ የቅን ፡ ቅን ፡ (እጅግ ፡ በጣም ፡ ቅን) ፡ ነው ።

5 መኰንን ፡ በብስኪሌት ፡ እንደ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ይበራል ።

6 የኔ ፡ ወንድም ፡ እንደ ፡ እንዝርት ፡ ሹር ፡ ነው ።

፪ኛ ፡ የሚከተሉትን ፡ ድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ተንትናቸው ። (በሰንጠረዥ፡ ዐቅድ)፡

1 የሚዋደዱት ፡ በቀለና ፡ እንደሻው ፡ እስከ ፡ ደብረ ፡ ማርቆስ ፡ ድረስ ፡ አብረው ፡ ሄዱ ።

2 መንግሥቱን ፡ ትናንትና ፡ በዚህ ፡ በኩል ፡ ሲያልፍ ፡ አየሁት ።

3 በቀለ ፡ እስኪመለስ ፡ ድረስ ፡ ትምህርቴን ፡ በትጋት ፡ አጠናለሁ ።

4 ከዚህ ፡ በፊት ፡ ያላየኸውን ፡ ነገር ፡ ባየህ ፡ ጊዜ ፡ የመዠመሪያ ፡ አሳብህ፡«ይህ፡ ምንድርነው ? » ይሁን ።

5 በአሥመራ ፡ በኩል ፡ የመጣውን ፡ የግብጽን ፡ ጦር ፡ አጼ ፡ ዮሐንስ፡ ድል ፡ካደረጉት ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ አንሰራርቶ ፡ መጣና ፡ ቢገጥማቸው ፡ ግንባሩን ፡ አጠፉት ።

6 የሐረር ፡ አየር ፡ ንብረት ፡ ለጤንነት ፡ የተስማማ ፡ መሆኑ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ አገሮች ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ታወቀ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ሐረርን ፡ ለመጎብኘት ፡ በዕረፍት ፡ ጊዜያቸው ፡ ይመጣሉ ።

7 ከኦሊ ፡ ኢሪክሰን ፡ መጽሐፍ ፡ የተጠቀሱ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡

(ሀ) ልጆች ፡ መታዘዝን ፡ ያልተማሩበት ፡ ቤት ፡ የባለጌ ፡ ዋሻ ፡ ነው ።

(ለ) ዋልጌዎች ፡ (የማይሠሩ ፡ ወስላቶች ፡ ሰነፎች) ፡ ቅጠልን ፡ የሚበተብቱ ፡ ትሎችን ፡ ይመስላሉ ።

(ሐ) ስድ ፡ ሆነው ፡ የሚፋንኑትን ፡ አሳቦቻችንን ፡ በቅን ፡ መንገድ ፡ ልንመራ ፡ ይገባናል ።

(መ) እስካሁን ፡ ድረስ ፡ እንከን ፡ ወይም ፡ ሰሐ ፡ የሌለው ፡ አላየሁም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ፡ የዝርዝር ፡ አፈታት ።

የዝርዝር ፡ አፈታት ፡ የያንዳንዱን ፡ ቃል ፡ ግብር ፡ እየለየን ፡ የምናውቅበት ፡ ክፍል፡ ነው።

አስረጅ ፡

፩ ብዙ ፡ ወጣቶች ፡ ትምህርታቸውን ፡ በትጋት ፡ ይማራሉ ።

ብዙ ፡ የመጠን ፡ ቅጽል ፡ ተከታይ ፡ ወጣትን ፡ ይገልጻል ።

ወጣቶች ፡ የወል ፡ ስም ፥ የወል ፡ ጾታ ፥ የብዙ፡ ቍጥር፥ ሙያው ፡ ባለቤት፥ ባለቤትነቱም፡ ለአንቀጹ ፡ ለይማራሉ ፡ ነው ።

ትምህርት ፡ የነገር ፡ ስም ፥ ግዑዝ ፡ ጾታ ፥ ነጠላ፡ ቍጥር ፡ ሙያው ፡ ተሳቢ ፡ ተሳቢነቱም፡ ለማሰሪያ ፡ አንቀጹ ፡ ለይማራሉ ፡ ነው ።

አቸው ፥ አገናዛቢ ፡ ዐጸፋ ፡ ፫ኛ ፡ መደብ ፡ የወል ፡ ጾታ ፡ የብዙ፡ ቍጥር ፡ ሙያው ፡ አገናዛቢ ፡ (ዝርዝር ) ፡ ቅጽል ፡ ነው ። የእነርሱ ፡ ትምህርት ፡ ያሰኝ ፡ የነበረውን ፡ ትምህርታቸው ፡ አሰኝቷል ።

ን - ተጠቃሽ ፡ ተሳቢን ፡ የሚያመለክት ፡ ቅጽል ፡ ነው ።
በትጋት ፡ የግብር ፡ ተውሳከ ፡ ከግስ ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጹን ፡ ይማራሉን ፡ ይገልጻል ።
ካዕቡ ፡ ፊደል ፡ «ሉ» ፡ ዐጸፋዊ ፡ ዝርዝር ፡ ፫ኛ ፡ መደብ ፡ የብዙ ፡ ቍጥር ፡ ሙያው ፡ ለወ ጣቶች ፡ የባለቤት ፡ ዝርዝር ፡ ነው ።
ይማራሉ ፡ ተሻጋሪ ፡ ገቢር ፡ ዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡ የብዙ ፡ ቍጥር ፡ የአሁንና ፡ የትንቢት ፡ ፫ኛ ፡ መደብ ፡ የወል ፡ ጾታ ፡ ሕገኛ ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡

2 መንግሥቱ ፡ በዘቢጥ ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ በሠጋር ፡ በቅሎ ፡ ሲፈስ ፡ አንድ ፡ ያለመ ጠን ፡ እብሪት ፡ የነፋው ፡ ጎረምሳ ፡ ከወደ ፡ ኋላው ፡ መጥቶ ፡ በጎመዳም ፡ ዱላ ፡ ቢያቦነው ፡ እንደ ፡ ከረረች ፡ ኳስ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ጓንና ፡ አራት ፡ ክንድ ፡ ያህል ፡ ርቆ ፡ ነጠረ ።
መንግሥቱ ፡ የተጸውዖ ፡ ወንዴ ፡ ነጠላ ፡ ሙያው ፡ ባለቤት ፡ ባለቤትነቱም ፡ ለጥገኛ ፡ ሐረጉ ፡ ለሲፈስና ፡ ለማሰሪያ ፡ አንቀጾቹ ፡ ለነጠረና ፡ ለጓን ፡ ነው ።
በ-ላይ ፡ ድርብ ፡ የቦታ ፡ መስተዋድዳን ፡ ዘቢጥ ፡ ሜዳን ፡ ይገዛል ።
ዘቢጥ ፡ የቦታ ፡ ስም ፡ የተጸውዖ ፡ ግዑዝ ፡ ሙያው ፡ የመስተዋድዱ ፡ የ«የ» ፡ ተገዥ ።
(ዘርፍ ፡ ዘርፍነቱም ፡ ለሜዳ ፡ ነው) ።
የ-ባለገንዘብን ፡ የሚያመለክት ፡ ነጠላ ፡ መስተዋድድ ፡ «በ» ፡ስለ ፡ ተጫነው ፡ ውስጠ ፡ ታዋቂ ፡ ሆኖ ፡ ቀርቷል ፤ አገባቡ ፡ ዘቢጥን ፡ ዘርፋዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ለማድረግ ፡ ነው ።
ሜዳ ፡ የወል ፡ ስም ፡ ግዑዝ ፡ ጾታ ፡ ነጠላ ፡ ሙያው ፡ የመስተዋድድ ፡ ተገዥ ።
የዘቢጥ ፡ መስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ቅጽላዊ ፡ ሜዳን ፡ ይገልጻል ።
በዘቢጥ ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ መስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ በየት ፡ እየፈሰሰ ፡ እንደ ፡ ሄደ ፡ ያመለክታል ።
በ-ማድረጊያ ፡ ነጠላ ፡ መስተዋድድ ፡ በቅሎን ፡ ይገዛል ።
ሠጋር ፡ የግብር ፡ ቅጽል ፡ ተከታይ ፡ በቅሎን ፡ ይገልጻል ።
በቅሎ ፡ የወል ፡ ስም ፡ የወል ፡ ጾታ ፡ ነጠላ ፡ ሙያው ፡ የመስተዋድዱ ፡ «በ» ተገዥ ።
በሠጋር ፡ በቅሎ ፡ መተስዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ በምን ፡ እየፈሰሰ ፡ እንደ ፡ ሄደ ፡ያመለ ክታል ።
ሲ - ሁኔታን ፡ አመልካች ፡ ጥገኛ ፡ መስተፃምር ፡ ነው ፤ መንግሥቱ ፡ በዘቢጥ ፡ ሜዳ፡ ላይ፡ በበቅሎ ፡ ፈሰሰ ፡ የሚለውን ፡ ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ጥገኛ፡ ሐረግ ፡ አድርጎ ፡-------- ----------------ቢያቦነው ፡ ከሚለው ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ጋራ ፡ አያይዞታል ።
ፈሰሰ ፡ የማይሻገር ፡ አድራጊ፡ ዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡ ነጠላ ፡ ቍጥር ፡ የዋህ ፡ ኀላፊ ፡ ፫ኛ ፡ መደብ ፡ ወንዴ ፡ ጾታ ፡ ሕገኛ ፡ የጥገኛ ፡ ሐረጉ ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡
ሲፈስ ፡-------- ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ የሁኔታ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ቢያቦነው ፡ የሚለውን ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ይገልጻል ።

አንድ ፡ ያልተወሰነ ፡ አመልካች ፡ ቅጽል ፡ ተከታይ ፡ ጎረምሳን ፡ ይገልጻል ።

ያለ ፡ አፍራሽ ፡ ነጠላ ፡ መስተዋድድ ፡ መጠን ፡ የሚለውን ፡ ቃል ፡ ይገዛል ።

መጠን ፡ የነገር ፡ ስም ፡ ግዑዝ ፡ ጾታ ፡ ነጠላ ፡ ሙያው ፡ የአፍራሽ ፡ መስተዋድድ ፡ ተገዥ ፡ ነው ።

ያለመጠን ፡ መስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ አገባቡ ፡ እንደ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ እብሪት ፡ የነፋው ፡ የሚለውን ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ይገልጻል ።

እብሪት ፡ የነገር ፡ ስም ፡ ግዑዝ ፡ ነጠላ ፡ ሙያው ፡ ባለቤት ፡ ባለቤትነቱም ፡ ለጥገኛ ፡ ሐረጉ ፡ አንቀጽ ፡ ለነፋው ፡ ነው ።

የ-ቅጽል ፡ አድራጊ ፡ ጥገኛ ፡ መስተፃምር ፡ ነው ፤ ያለመጠን ፡ እብሪት ፡ ነፋው ፡ የሚለውን ፡ ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ አድርጓል ።

ነፋ ፡ ተሻጋሪ ፡ ግቢር ፡ ዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡ ነጠላ ፡ የዋህ ፡ ኀላፊ ፡ ፫ኛ ፡ መደብ ፡ ወንዴ ፡ ጾታ ፡ ሕገ ፡ ወጥ ፡ የጥገኛ ፡ ሐረጉ ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡

ው-ዐጸፋዊ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ነጠላ ፡ ወንዴ ፡ ጾታ ፡ ሙያው ፡ ቀጥተኛ ፡ ተሳቢ ፡ ተሳቢ ነቱም ፡ ለማሰሪያ ፡ አንቀጹ ፡ ለነፋ ፡ ነው ፤ ዐጸፋነቱም ፡ ለጎረምሳ ፡ ነው ።

እብሪት ፡ የነፋው ፡ - - - ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ነው ፤ ጎረምሳ ፡ የሚለውን ፡ ቃል ፡ ምን ፡ ዐይነት ፡ ወጣት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይገልጸዋል ።

ጎረምሳ ፡ የወል ፡ ስም ፡ ወንዴ ፡ ጾታ ፡ ነጠላ ፡ ሙያው ፡ ባለቤት ፡ ባለቤትነቱም ፡ ቢያቦ ነው ፡ ለሚለው ፡ ለጥገኛ ፡ ሐረጉ ፡ አንቀጽ ፡ ለአቦነን ፡ ነው ።

ከ-ወደ ፡ አቅጣጫን ፡ የሚያመለክቱ ፡ ድርብ ፡ የቦታ ፡ መስተዋድዳን ፡ ኋላ ፡ የሚለውን ፡ ተውሳከ ፡ግስ ፡ ይገዛሉ ።

ኋላ ፡ የዋህ ፡ የቦታ ፡ አንዳንድዬም ፡ የጊዜ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ እንደ ፡ ስም ፡ ሆኖ ፡ ለመስተ ዋድዳኑ ፡ ተገዥ ፡ ሆኗል ።

ው-ዐጸፋ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ፫ኛ ፡ መደብ ፡ ወንዴ ፡ ነጠላ ፡ ሙያው ፡ ለመንግሥቱ ፡ ዐጸፋ መሆን ፡ ነው ። ከወደ ፡ መንግሥቱ ፡ ኋላ ፡ መጥቶ ፡ ተብሎ ፡ መጻፍ ፡ ይገባው ፡ የነበረውን ፡ ከወደ ፡ ኋላው ፡ አሰኝቶ ፡ አሳጥሮታል ።

ከወደ ፡ ኋላው ፡ መስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ እንደ ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ገብቶ ፡ ቦዝ ፡ አንቀጹን ፡ መጥቶን ፡ ይገልጻል ።

መጥቶ ፡ የማይሻገር ፡ አድራጊ ፡ ነጠላ ፡ ኀላፊ ፡ ፫ኛ ፡ መደብ ፡ እንደ ፡ ቅጽል ፡ ቅጽልነ ቱም ፡ ለጎረምሳ ፡ ነው ።

በ-ማድረጊያ ፡ ነጠላ ፡ መስተዋድድ ፡ ዱላን ፡ ይገዛል ።

ጎመዳም ፡ የግብር ፡ ቅጽል ፡ ተከታይ ፡ ዱላን ፡ ይገልጻል ።

ዱላ ፡ የቁሳቁስ ፡ ስም ፡ ግዑዝ ፡ ነጠላ ፡ ሙያው ፡ የመስተዋድዱ ፡ የ«በ»ተገዥ ፡ ነው ።

በጎመዳም ፡ ዱላ ፡ ቢያቦነው ፡ የሚለውን ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ይገልጻል ።

ቢ -ሁኔታን ፡ አመልካች ፡ ጥገኛ ፡ መስተፃምር ፡ ነው ፤ በጎመዳም ፡ ዱላ ፡ አቦንነው፡ የሚ
ለውን፡ ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ አድርጎ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ጓን ፡ ከሚለው ፡
መደበኛ ፡ ሐረግ ፡ ጋራ ፡ አያይዟል ።
አቦነነ ፡ ተሻጋሪ ፡ ገቢር ፡ ዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡ ነጠላ፡ ቊጥር ፡ የዋህ ፡ ኀላፊ ፡ ፫ኛ ፡ መደብ፡
ወንዴ ፡ ጾታ ፡ ሕገኛ ፡ ለጥገኛ ፡ ሐረጉ ፡ ባለቤት ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡ ነው ።
ቢያቦነው ፡ ----ተውሳከ ፡ ግሳዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ የአኳኋን ፡ ተውሳከ ፡ ግስ፡ ጓን፡ የሚለ
ውን ፡ ግስ ፡ ይገልጻል ።
ው-ዐጸፋዊ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ነጠላ ፡ ወንዴ ፡ ጾታ ፡ ሙያው ፡ ዐጸፋ ፡ (ድጋሚ) ፡ ዐጸፋ
ነቱም ፡ ለጎረምሳ ፡ ነው ።
እንደ ፡ ማንጸሪያ ፡ ነጠላ ፡ መስተዋድድ ፡ ኳስን ፡ ይገዛል ።
የ-ቅጽል ፡ አድራጊ ፡ ውስጠ ፡ ታዋቂ ፡ ጥገኛ ፡ መስተፃምር ፡ ነው ። የከረረች ፡ ይል፡ የነበ
ረውን ፡ መስተዋድዱ ፡ እንደ ፡ ውጦ ፡ አስቀርቶታል ። ከረረች ፡ የሚለውን ፡ ነጠላ ፡ አረ
ፍተ ፡ ነገር ፡ ቅጽላዊ ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ አድርጓል ።
ከረረ ፡ የማይሻገር ፡ አድራጊ ፡ ዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡ ነጠላ ፡ የዋህ ፡ ኀላፊ ፡ ፫ኛ ፡ መደብ ፡
ወንዴ ፡ ጾታ ፡ ሕገኛ ፡ ለጥገኛ ፡ ሐረጉ ፡ ባለቤት ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡ ነው ።
ች-ዐጸፋ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ነጠላ ፡ ሴቴ ፡ ጾታ ፡ ሙያው ፡ የባለቤት ፡ ዝርዝር ፡ ዝርዝር
ነቱም ፡ ለኳስ ፡ ነው ።
የከረረች ፡ ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ኳስን ፡ ይገልጻል ።
ኳስ ፡ የቁሳቊስ ፡ ስም ፡ ግዑዝ ፡ ነጠላ፡ ሙያው፡ የመስተዋድዱ ፡ የ«እንደ»፡ ተገዥ፡ነው።
እንደ ፡ ኳስ፡ መስተዋድዳዊ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ፡ ተውሳከ፡ግሳዊ፡ ጓንና ፡ ነጠረ ፡ የሚሉትን ፡
ግሶች ፡ ይገልጻል ።
ወደ ፡ መገሥገሻ ፡ ነጠላ ፡ መስተዋድድ ፡ ሰማይን ፡ ይገዛል ።
ሰማይ ፡ የወል ፡ ስም ፡ ግዑዝ ፡ ነጠላ ፡ ሙያው ፡ የመስተዋድዱ፡ የ «ወደ»፡ ተገዥ፡ ነው።
ወደ ፡ ሰማይ፡ ተውሳከ፡ ግሳዊ ፡ ንኡስ፡ ሐረግ ፡ የቦታ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ጓንን ፡ ይገልጻል ።
ጓነ ፡ የማይሻገር ፡ አድራጊ ፡ ዐቢይ፡ ነጠላ፡ ቊጥር ፡ የዋህ ፡ ኀላፊ ፡ ፫ኛ ፡ መደብ፡ ወንዴ፡
ጾታ ፡ ሕገኛ ፡ ሙያው ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽነቱም ፡ መንግሥቱ ፡ ለሚ
ለው ፡ ስም ፡ ነው ።
ና- ወደረኛ ፡ መተስፃምር፡ መንግሥቱ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ጓንና ፡ መንግሥቱ ፡ አራት ፡ ክንድ፡
ያህል ፡ ርቆ ፡ ነጠረ ፡ ተብለው ፡ የተጻፉትን ፡ ነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ አያይዟል ።
አራት ፡ ያህል ፡ ያልተወሰነ ፡ የአኀዝ ፡ ቅጽል ፡ ክንድን ፡ ይገልጻል ።
ክንድ ፡ የወል ፡ ስም ፡ ነጠላ ፡ ግዑዝ ፡ ሙያው ፡ ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ተውሳከ ፡ ግስነቱም ፡
ነጠረ ፡ ለሚለው፡ ግስ ፡ ነው፤ ሰውዬው ፡ ምን፡ ያህል፡ ስፍራ፡ እንደ፡ ራቀ፡ ያመለክታል።
አራት ፡ ክንድ ፡ ያህል ፡ ርቆን ፡ ይገልጻል ።
ርቆ ፡ የማይሻገር ፡ አድራጊ ፡ ነጠላ ፡ ኀላፊ ፡ ፫ኛ ፡ መደብ ፡ እንደ ፡ ቅጽል ፡ ቅጽልነቱም ፡
ለመንግሥቱ ፡ ነው ።

ነጠረ ፡ የማይሻገር ፡ አድራጊ ፡ ዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡ ነጠላ ፡ የዋህ ፡ ኅላፊ ፡ ፫ኛ ፡ መደብ ፡ ወንዴ ፡ ጾታ ፡ ሕገኛ ፡ ሙያው ፡ ማሰሪያ ፡ አንቀጽ ፡ ማሰሪያነቱም ፡ ለመንግሥቱ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ፡ ቃላት ።

ቃላት ፡ ሰዎች ፡ ሐሳባቸውን ፡ እየገለጹ ፡ የሚለዋወጡባቸው ፡ ነገሮች ፡ ናቸው ። ቃላት ፡ እኛ ፡ የምንፈልገውን ፡ ነገር ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ እየተነጋገርን ፡ ለማስፈጸም ፡ ከማስ ቻላቸው ፡ በላይ ፡ ባለመገባባት ፡ ከሚፈጠር ፡ ሁከት ፡ ያድኑናል ። ቃላት ፡ በሕዝብ ፡ መመላለሻና ፡ መገናኛ ፡ መሥመሮች ፡ ይመሰላሉ ። ሰዎች ፡ በእነዚህ ፡ ጉዳያቸውን ፡ እንዲፈጽሙ ፡ እንደዚሁም ፡ በቃላት ፡ ይፈጽማሉ ። የሰው ፡ ልጆች ፡ በሐሳብ ፡ መግባ ባትንና ፡ መለዋወጥን፡ በሚያደርጉበት ፡ ጊዜ፡ ቃላት ፡ ዋና፡ የመጠቃቀሚያቸው፡ ወይም፡ የመፈራቀቂያቸው ፡ ቍልፎች ፡ ናቸው ።

ስለዚህ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያዳም ፡ ልጆች ፡ ያለቋንቋ ፡ ጉዳያቸውን ፡ በሚያጠግብ ፡ አኳኋን ፡ ለመፈጸም ፡ ስለማይችሉ ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ በጥንቃቄ ፡ ያጠናቸዋል ።

## የቃላት ፡ አጠናን ፡

ቃላትን ፡ በየወገን ፡ በየወገናቸው ፡ እያደረጉ ፡ ማጥናት ፡ ሐሳብን ፡ ለመግለጽ ፡ ባስፈለገ ፡ ጊዜ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ መንገድ ፡ ይረዳል ፤ ወይም ፡ ያገለግላል ። ቃላት ፡ በተመ ሳሳይነት ፡ ወይም ፡ በተወራራሽነትና ፡ በተቃራኒነት ፡ ወይም ፡ በብቸኝነት ፡ ይጠናሉ ።

ተመሳሳይ ፡ ወይም ፡ ተወራራሽ ፡ የሚባሉ ፡ ቃላት ፡ አንድ ፡ ዐይነት ፡ ወይም ፡ የተቀራረበ ፡ ትርጓሜን ፡ የሚሰጡት ፡ ናቸው ። ቃላትን ፡ በማናቸውም ፡ በኩል ፡ ብንመ ረምራቸው፡ (ብንመለከታቸው)፡ ፍጹም ፡ የሆነ ፡ ተመሳሳይነት ፡ አናገኝባቸውም ። ነገር፡ ግን ፡ በጣም ፡ ስለሚቀራረቡ ፡ አንዱ ፡ ያንደኛውን ፡ ትርጓሜ ፡ ይገልጸዋል ፡ ብለን ፡ እንገ ምታለን። ስለዚህ፡ አገላለጻቸውን፡ ለማወቅ፡ ደኅና ፡ አድርጎ፡ መመልከት ፡ ያስፈልጋል።

ተመሳሳይ ፡ ቃላት ፡ በመልካም ፡ ነገር ፡ ወይም ፡ በመጥፎ ፡ ነገር ፡ ይመሳሰላሉ ። እንደዚህም ፡ ማለት ፡ መጥፎው ፡ ቃል ፡ ከመጥፎው ፡ ቃል ፡ ጋራ ፡ ወይም ፡ ጥሩው ፡ ቃል ፡ ከጥሩው ፡ ቃል ፡ ጋራ ፡ ወይም ፡ መናኛው ፡ ቃል ፡ ከመናኛው፡ ጋራ ፡ ይመሳሰላሉ፡ ማለት ፡ ነው ።

ተቃራኒ ፡ ማለት ፡ ተቃዋሚ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ የመዠመሪያው ፡ ቃል ፡ የሚሰጠውን ፡ ትርጓሜ ፡ የሚቀጥለው ፡ ቃል ፡ የሚያፈርሰው ፡ ሲሆን ፡ ነው ። አንድ ፡ ቃል ፡ ያንድ ፡ ቃልን ፡ ፍች ፡ ሲለውጥ ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ ሁለት ፡ ነገርን ፡ ስለማይሠራ ፡ መጥፎውን ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ለመለወጥ ፡ የተፈለገ ፡ እንደሆን ፡ የመጥ ፎው ፡ ቃል ፡ ተቃዋሚ ፡ መልካሙ ፡ ቃል ፡ ይነገራል ። ጥሩውንም ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ መጥፎ ፡ ነገር ፡ ለመለወጥ ፡ የተፈለገ፡ እንደሆን ፡ የጥሩው፡ ተቃዋሚ ፡ መጥፎው፡ ቃል፡ ይነገራል።

የፊተኛውን ፡ ሐሳብ ፡ በማስታወስ ፡ ማንኛውንም ፡ ቃል ፡ ፍጹም ፡ ተቃራኒ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ለማመን ፡ ያስቸግራል ። በዚህም ፡ ላይ ፡ እንዳንደነቃቀፍ ፡ የሚረዳን፡ ነገር፡

አንድ ፡ ቃል ፡ አንድ ፡ ነገርን ፡ ለመግለጽ ፡ የመጣ ፡ መሆኑን ፡ ማወቅ ፡ ነው ። እንግዲህ ፡ እንዲህ ፡ ከሆነ ፡ እያንዳንዱ ፡ ቃል ፡ ራሱን ፡ የቻለ ፡ ሆኖ ፡ የተለየ ፡ ነገርን ፡ ለመግለጽ ፡ የተሠራ ፡ (የመጣ) ፡ ነውና ፤ ፍጹም ፡ ተመሳሳይ ፡ ነው ፡ በማለትና ፡ ፍጹም ፡ ተቃራኒ ፡ ነው ፡ በማለት ፡ እንዳንቸገር ፡ መጠንቀቅ ፡ አለብን ።

አንዳንድ ፡ ቃላት ፡ ተመሳሳይ ፡ ወይም ፡ ተቃራኒ ፡ አይገኙላቸውም ። ስለዚህ ፡ እንደዚህ ፡ ያሉትን ፡ ቃላት ፡ በሁለት ፡ ወይም ፡ በሦስት ፡ ወይም ፡ በብዙ ፡ ቃላት ፡ እየ ፈታን ፡ (እየተረጐምን) ፡ እናጠናቸዋለን ፤ እነዚህም ፡ የደግ ፡ ወይም ፡ የመጥፎ ፡ ትርጓሜ ፡ እንዳላቸው ፡ አይጠረጠርምና ፤ በያገባባቸው ፡ ማጥናት ፡ አለብን ።

<u>ቃላትን ፡ የማጥናት ፡ ጥቅም ፡</u>

ተመሳሳይ ፡ ቃላትን ፡ በማጥናት ፡ ቃላት ፡ በአረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ እንዳይደጋ ገሙ ፡ ለማድረግ ፡ እንችላለን ። ከዚህ ፡ በፊት ፡ ስም ፡ እንዳይደገም ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ በስም ፡ ፈንታ ፡ እየገባ ፡ (እየተተካ) ፡ እንደሚገባ ፡ አስረድተናል ። እንደዚሁም ፡ አንዱ ፡ ቃል ፡ ላንዱ ፡ ቃል ፡ ልዋጭ ፡ ሆኖ ፡ የግል ፡ ተግባሩን ፡ ሳይለቅ ፡ ይገባል ።

ተቃራኒ ፡ ቃላት ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ በአዎንታ ፡ የሚነገሩ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ወደ ፡ አሉታ ፡ ሳይለወጡ ፡ የአሉታን ፡ ትርጓሜ ፡ እንዲሰጡ ፡ ወይም ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ በአሉታ ፡ የሚነገሩ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ወደ ፡ አዎንታ ፡ ሳይለወጡ ፡ የአዎንታን፡ ስሜት፡ እንዲሰጡ ፡ ይረዱናል ።

<u>አስረጅ</u> ፡- ትርጕማቸውን ፡ እሥር ፡ እሥራቸው ፡ ተመልከት ።

(ሀ) ጭምት ፡ ክልፍልፍ ፡
ልጁ ፡ ክልፍልፍ ፡ አይደለም ።
ልጁ ፡ ጭምት ፡ ነው ።

(ለ) እንቢ ፡ እሺ ፡
ሞትን ፡ እንቢ ፡ አላልሁትም ።
ሞትን ፡ እሺ ፡ አልሁት ።

(ሐ) አስደሰተ ፡ አስቀየመ ፡
ካሣን ፡ አላስደሰትሁትም ።
ካሣን ፡ አስቀየምሁት ።

(መ) ወሰደ ፡ ተቀበለ ፡

መኰንን ፡ ደመወዙን ፡ አልወሰደም ፤ ስለዚህ፡ ሳይቀበል ፡ ወደ ፡ መንገድ ፡ ሄደ፡ ማለት ፡ የሚገባ ፡ አይመስለኝም ።

ቃላት ፡ በመጥበቅና ፡ በመላላት ፡ ወይም ፡ አነባበባቸውን ፡ ሳይለውጡ ፡ ትርጓ ሜያቸውን ፡ ይለውጣሉ ። አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ተሻጋሪ ፡ ግስ ፡ በመጥበቅና ፡ በመላላት ፡ ገቢርና ፡ ተገብሮን ፡ በአርእስቱ ፡ ያስገኛል። ሌሎቹ፡ ግን ፡ በግስ ፡ ስልታቸው ፡ ይለያሉ።

ጥኀተ ፡ ጥበብ ፡ ዘሥነ ፡ ጽሑፍ ።

ምሳሌ ፦

| በመጥበቅ ፡ | በመላላት ፡ | በመጥበቅ ፡ | በመላላት ፡ | በመጥበቅ ፡ | በመላላት ፡ |
|---|---|---|---|---|---|
| መካድ ፡ | መካድ፡ | መጻፍ ፡ | መጻፍ፡ | አለ፡(በስፍራ፡ላይ)አለ፡(ተናገረ)፡ | |
| መሳም ፡ | መሳም፡ | መቀርደድ፡ | መቀርደድ፡ | አለ ፡ (ለገንዘብ) ፡ | |
| መነስነስ፡ | መነስነስ፡ | መደርደር፡ | መደርደር፡ | አለ ፡ በረዳትነት ፡ | |
| | | | | ድኅነትችግረኛነትድኅነትመዳን | |

ተመኩሳይያን ፡ (ሞክሼ) ፡

ንባባቸው ፡ አንድ ፡ ዐይነት ፡ የሆኑ ፡ ቃላት፡

ደረሰ ፡ 1 መጽሐፍን ፡ ደረሰ ፡ (ጻፈ) ።
» 2 አንበሳው ፡ ደረሰ ፡ (መጣ) ።
ደራ ፡ 1 ጫወታው ፡ ደራ ፡ (ደመቀ ፡ ተሟሟቀ) ።
» 2 ጣራው ፡ ደራ ፡ (ዘባ) ።
አገደ ፡ 1 ከብቶችን ፡ ያግዳል ፡ (ይጠብቃል) ።
» 2 ልጁን ፡ በኩርማን ፡ መሬት ፡ አገደው ፡ (ወሰነው) ።
» 3 ውኃውን ፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ አግደውታል ፡ መሰለኝ፡ (አቁመውታል ፡ መሰለኝ) ።
አፈሠ፡ 1 አቶ ፡ ፈለቀ ፡ ሽፍቶቹን ፡ በድንገት፡ አገኘና፡ ሁሉንም ፡ አፈሣቸው፡(ያዛቸው)።
» 2 ዘንድሮ ፡ ይህን ፡ መሬት፡ ደኅና ፡ አድርጌ፡ አርሼው ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ ብዙ ፡ እህል ፡ በአፈሥሁለት ፡ ነበር ፡ (በአገኘሁበት ፡ ነበር) ።
» 3 ላሞቹ ፡ በለምለም ፡ መሠማሪያ ፡ ስለ ፡ ዋሉ ፡ ደኅና ፡ አድርገው ፡ አፍሠው ፡ (በልተው) ፡ ነበር። ይሁን ፡ እንጂ ፡ እንዳበላላቸው ፡ መጠን ፡ ብዙ ፡ ወተት ፡ አልወጣቸውም ።
ጠላ ፡ 1 እባክሽን ፡ አየለች ፡ አንድ ፡ ብርጭቆ ፡ ጠላ ፡ ስጭኝ ።
» 2 አየለን ፡ ምን ፡ እንዳደረግሁት ፡ ሳላውቅ ፡ ጠላኝ ።
መጠጥ ፡ 1 ልጄ ፡ መብራቱ ፡ ከትምህርት ፡ ቤት ፡ እየሮጠ ፡ ሲመጣ ፡ ወድቆ ፡ ጉልበቱ ፡ ተልጦ ፡ ነበር ፤ አሁን ፡ ቍስሉ ፡ መጠጥ ፡ ብሎለታል ።
» 2 አብዛኞቹ ፡ ወጣቶች ፡ መጠጥን ፡ ንቀዋል ።
ባለጠላ 1 ሴትዮዋ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ባሏ ፡ በቤት ፡ ስለሚነዘንዛት ፡ ባለጠላ ፡ ሆናለች ።
» 2 ባለጠላ ፡ የሆኑ ፡ (ጠላ ፡ የሚጠምቁ) ፡ በጠላው ፡ ሽያጭ ፡ ይከብራሉ ።
ማለፊያ፡1 የነርሱን ፡ አሳብ ፡ እንጃ ፡ እንጂ ፡ የፈለቀስ ፡ አሳብ ፡ በጣም ፡ ማለፊያ ፡ ነው ።
» 2 ወንዙን ፡ ጎርፍ ፡ ስለ ፡ ሞላው ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ ማለፊያ ፡ የለኝም ።
ሽፍታ 1 ካንድ፡ ሥፍራ፡ ወዳንድ፡ ሥፍራ፡ እየተዘዋወሩ፡ በጫካ፡ ውስጥ፡ሆነው፡ በጦር፡ መሣሪያ፡ እያስፈራሩ፡ ሰላማዊውን፡ ሕዝብ ፡ የሚዘርፉ ፡ ሽፍቶች፡ ይባላሉ ።
» 2 እማማ፡ ወተቱን፡ መናጥ፡ ይዣለሁ፡ ቅቤውም፡ ሊወጣ፡ ነው፤ ሽፍታ፡ ሆኗል።
ትራስ ፡ 1 ያለትራስ ፡ መተኛት ፡ ትልቅ ፡ አደጋ ፡ ያመጣል ።
» 2 ልጅህ ፡ በክረምት ፡ ወደ ፡ ትምህርት፡ ቤት፡ ስትሄድ ፡ ጃንጥላ ፡ ብትገዛላት ፡ ይሻላል ፤ ለምን ፡ በከንቱ ፡ በዝናም ፡ ትራስ ?

አግዝ ፡ 1 ቤቴን ፡ ልቀቅልኝ ፤ ዕቃህንም ፡ አሁኑን ፡ አግዝ ።
» 2 ወንድምህ ፡ ሲሠራ ፡ ዝም ፡ ብለህ ፡ አትመልከት ፤ ጠጋ ፡ ብለህ ፡ አግዘው ።
ግን ባር፡ 1 ተስፋዬ ፡ ትናንትና ፡ ወድቆ ፡ ግንባሩን ፡ ተፈንክቷል ።
» 2 ልጆች ፡ ሲሰለፉ ፡ ረግኸርሞቹ ፡ በግንባር ፡ እንዲሆኑ ፡ ያስፈልጋል ።

## ተመሳሳይ ፡

### የስም ፡ ተመሳሳይ ፡

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| መሙሊያ፡ | ማንቆርቆሪያ፡ | ብላቴና ፡ | ሕፃን ፡ | ባልጀራ፡ | ጓደኛ ፡ | እኩያ ፡ | አቻ ፡ |
| ብልጫ ፡ | ከፍተኛነት ፡ | ቆዳ ፡ | አንጋሬ ፡ | » | ባልደረባ ፡ | እንቅፋት ፡ | መሰናክል ፡ |
| ደጋጎች፡ | መንፈሳውያን፡ | ቢልታ ፡ | ቀልድ ፡ | ባተሌ ፡ | ታታሪ ፡ | ዙፋን ፡ | አልጋ ፡ |
| ብርዕ ፡ | መጻፊያ ፡ | ቀፎ ፡ | ባዶ ፡ | ገበዝ ፡ | ቤተ፡አበ ፡ | አጨባበጥ ፡ | አያያዝ ፡ |
| ማገር ፡ | ማጥበቂያ ፡ | ሙሽት ፡ | ቁርስ ፡ | አለሌ ፡ | ሸርሙጣ፡ | አሲድ ፡ | ራብ ፡ |
| ብርክ ፡ | መንቀጥቀጥ፡ | ማደያ ፡ | ወለል ፡ | » | አመንዝራ ፡ | ወገግታ፡ | ፈገግታ ፡ |
| ፍርሀት፡ | መባባት ፡ | ፍዳ ፡ | በቀል ፡ | አተላ ፡ | ዝቃጭ ፡ | ሥቃይ ፡ | መከራ ፡ |
| ዳተኛነት፡ | ዝግተኛነት፡ | ቂም ፡ | ቋሳ ፡ | ምንጣፍ ፡ | ጉዝጓዝ፡ | ደባ ፡ | ተንኮል፡ |
| ጭቅነት፡ | ገራድነት ፡ | አካል ፡ | ገላ ፡ | ተድላ ፡ | ደስታ ፡ | አለኝታ፡ | ተስፋ ፡ |
| አዛዥ ፡ | መጋቢ ፡ | ዳዋ ፡ | አረም ፡ | ሐዘን ፡ | ትካዜ ፡ | ወዝ ፡ | ላብ ፡ |
| ረዳት ፡ | አጋዥ ፡ | » | ጢሻ ፡ | ምስል ፡ | ጣዖት ፡ | አለት ፡ | ጭንጫ ፡ |
| ጉድፍ፡ | ቁሻሻ ፡ | ዜና ፡ | ታሪክ ፡ | ገንዘብ ፡ | ንዋይ ፡ | ዳቦ ፡ | ኅብስት ፡ |
| አረንዛ፡ | ድንጋያም ፡ | መዲና ፡ | መናገሻ ፡ | ዱለት ፡ | ሸንጎ ፡ | ነት ፡ | ቁርበት ፡ |
| ቆፈን ፡ | ብርድ ፡ | ሕመም ፡ | በሽታ ፡ | ችሎት ፡ | አደባባይ፡ | » | ጀንዲ ፡ |
| ፈሊጥ ፡ | ዘዴ ፡ | በረከት ፡ | ሀብት ፡ | ዱለት ፡ | መቆናቆን ፡ | አውጫጭኝ፡ | አፈርሳታ፡ |
| ጸጋ ፡ | ስጦታ ፡ | እድሞ ፡ | ቅጽር ፡ | ሴራ ፡ | አድማ ፡ | ቃባ ፡ | ወዶማ ፡ |
| » | ችሮታ ፡ | » | ግንብ ፡ | ረብ ፡ | ፋይዳ ፡ | » | ኩልኩልት፡ |
| እልቂት፡ | ፍጅት፡ | መቃወም፡ | መከራከር | » | ጥቅም ፡ | ጠብ ፡ | ጥል ፡ |
| | | | | አበሳ ፡ | በደል፡ | ወሬ ፡ | ዜና ፡ |
| | | | | » | ኃጢአት፡ | | |
| | | | | ጎሞር ፡ | መስፈሪያ፡ | | |

### የቅጽል ፡ ተመሳሳይ ፡

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| እባብ ፡ | ተንኮለኛ ፡ | በክት ፡ | ጥንብ ፡ | ድውይ፡ | ሕመምተኛ፡ | ባካና ፡ | ባተሌ ፡ |
| ብልኀ ፡ | መሠሪ ፡ | ገሣድ ፡ | ግልጽ ፡ | ቆቅ ፡ | ንቁ ፡ | ቡከን ፡ | ፈሪ ፡ |
| » | ዐዋቂ ፡ | ግዙፍ ፡ | ወፍራም ፡ | ብልጥ፡ | ጮሌ ፡ | ቦዘንተኛ፡ | ሥራ ፈት፡ |
| » | ብልጥ ፡ | ለዛ፡ቢስ፡ | ጣመ፡ቢስ፡ | ፀር ፡ | ጠላት ፡ | ብርቱ፡ | ኀበዝ ፡ |
| በድን ፡ | ሙት ፡ | አንጋፋ ፡ | በኵር ፡ | መልቲ፡ | አታላይ ፡ | አብሽቅ ፡ | አናዳጅ ፡ |
| » | ሬሳ ፡ | ወዛም ፡ | ደማም ፡ | አባያ ፡ | ሰነፍ ፡ | ቅይጥ ፡ | ውጥንቅጥ ፡ |
| ብላሽ ፡ | ከንቱ ፡ | | | | | | |

## የግስ፡ ተመሳሳይ።

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ተጋ፡ | ነቃ፡ | አሻ፡ | ተገባ፡ | » | ሰረሰረ፡ | ደፈረሰ፡ | ጎሸ፡ |
| አየለ፡ | በረታ፡ | ፋረ፡ | ጫረ፡ | ተፍለከለከ፡ | ተልወሰወሰ፡ | ከመረ፡ | ቆለለ፡ |
| አበተ፡ | አሰረ፡ | በተነ፡ | ዘራ፡ | « | ተርመሰመሰ፡ | » | ጎቸ፡ |
| ተወ፡ | ለቀቀ፡ | ተራወጠ፡ | ተፋጠነ፡ | ቆፈረ፡ | ኳተ፡ | ዐሸ፡ | አፍተለተለ፡ |
| ቸከ፡ | አደፈ፡ | ጋረጠ | ወጋ፡ | » | ማሰ፡ | ወቃ፡ | ደበደበ፡ |
| ጎነጠ፡ | ጎዳ፡ | በቃ፡ | ጸድቅ፡ሆነ | ደበነ፡ | ደረቀ፡ | ረጨ፡ | ፈነጠቀ፡ |
| አመነ፡ | ተስፋ፡አደረገ፡ | » | ቆመ፡ | ዘፈቀ፡ | ነከረ፡ | አፈፈ፡ | ከረከመ፡ |
| አሟረ፡ | ቀነቀነ፡ | ቀዳ፡ | ደነበቀ፡ | ከተተ፡ | አገባ፡ | አፈፈ፡ | አስተካከለ፡ |
| ቆጋ፡ | ገረፈ፡ | ቋጨ፡ | ገመደ፡ | ፈጀ፡ | ጨረሰ፡ | ተቆረቆረ፡ | ተመሠረተ፡ |
| ደቃ፡ | መታ፡ | » | አከረረ፡ | » | አቃጠለ፡ | » | ተቆጨ፡ |
| ጫጨ፡ | ኮሰሰ፡ | ነጠፈ፡ | ተወ፡ | » | አንቀረቀበ፡ | መሠረተ፡ | በገረ፡ |
| ላመ፡ | ደቀቀ፡ | » | ጡትጣለ | ሳገ፡ | ሻጠ፡ | ተንቆራጠጠ፡ | ወዲያና፡ |
| አሰናዳ፡ | አዘጋጀ፡ | አወከ፡ | አስቸገረ፡ | በላ፡ | ሸመሸመ፡ለከበት፡ | | ወዲህ፡ አለ፡ |
| ወደደ፡ | አፈቀረ፡ | » | በጠበጠ፡ | » | ተሳተፈ፡ | ነከሰ፡ | ያዘ፡ |
| ሞለፈፈ፡ | ላጠ፡ | » | አቋረጠ፡ | » | ከስከሰ፡ | አበሰ፡ | ጠረገ፡ |
| አገደ፡ | ከለከለ፡ | » | አሰናከለ፡ | » | ኮመኮመ፡ | » | ቀባ፡ |
| አወከ፡ | አስቸገረ፡ | ደራ፡ | ደመቀ፡ | አነሰ፡ | ተቀነሰ | ቸረ፡ | መጸወተ፡ |
| አሳፈረ፡ | አዋረደ፡ | » | ተሟሟቀ፡ | » | አጠረ፡ | » | ሰጠ፡ |
| ነካ፡ | ጎነጠ፡ | አሜን፡ | ይሁን፡ | » | አልበቃ፡ አለ፡ | » | ለገሠ፡ |
| ዋጀ፡ | ገዛ፡ | ተነኮለ፡ | አጫረ፡ | ወተወተ፡ | ቸከቸከ፡ | አበበ፡ | አጌጠ፡ |
| አወራ፡ | ተናገረ፡ | ረካ፡ | ጠገበ፡ | » | ነዘነዘ፡ | » | ፈካ፡ |
| ቦነነ፡ | አለቀ፡ | አዳነ፡ | ተበዠ፡ | አከረ፡ | (መሬቱን)፡ አደሰ፡ | » | ፈነዳ፡ |
| በነነ፡ | ጤሰ፡ | ተዋሰ፡ | ተያዘ፡ | ተቀዳጀ፡ | ደፋ፡ (ዘውድ)፡ | አበቀ፡ | ጨመረ፡ |
| ሰላ፡ | ተባ፡ | « ወሰደ፡ | (በውሰት)፡ | ተሰናከለ፡ | ታወከ፡ | ጎሰጎሰ፡ | አመቀ፡ |
| ሞረደ፡ | አተባ፡ | ከነከነ፡ | ቅር፡አለ፡ | ወዛ፡ | ተቅለጠለጠ፡ | አደብ፡ገዛ፡ | ዕረፍት፡ አደረገ፡ |
| » | ሳለ፡ | አገለለ፡ | ጎራ፡አለ፡ | ከሸነ፡ | አሳመረ፡ | ከመከመ፡ | አስተካከለ፡ |
| ጃጀ፡ | ሳተ፡ | አዛወረ፡ | ቀየረ፡ | ዐተረ፡ | አበጥ፡ አለ፡ | አወሳ፡ | አስታወሰ፡ |
| አከለ፡ | ጨመረ፡ | » | ለወጠ፡ | ባለገ፡ | ተሞላቀቀ፡ | መሰለ፡ | አሳሳተ፡በመምሰል፡ |
| ቦዘነ፡ | ሥራ፡ፈታ | ዛለ፡ | ደከመ፡ | አደገ፡ | ከፍ፡ አለ፡ | ቦደነ፡ | ወገን፡ አበጀ፡ |
| ተማፀነ፡ | ይግባኝ፡አለ፡ | ቀጠበ፡ | መጠነ፡ | ራደ፡ | ተንቀጠቀጠ | በለጠ፡ | ተረፈ፡ |
| ሄደ፡ | ነጎደ፡ | ተጠራ፡ | ተሰየመ፡ | ተቃና፡ | ተፎካከረ፡ | ተበተበ፡ | ተርበተበተ፡ |
| ተጣጣረ፡ | ተፍጨረጨረ | ቧጨረ፡ | ቧጠጠ፡ | ደነባ፡ | ወሰነ፡ | ለከለከ፡ | ጠጣ፡ |
| ሞተ፡ | ዐረፈ፡ | » | ጫረ፡ | ባነነ፡ | ቃዠ፡ | ቆዘመ፡ | አዘነ፡ |
| » | አለፈ፡ | ቀደደ፡ | ሸረከተ፡ | ክች፡አለ፡ | ደረቀ፡ | ቀጠፈ፡ | ቆረጠ፡ |
| ተኛ፡ | አንቀላፋ፡ | ነደለ፡ | በሳ፡ | » | ደነገጠ፡ | » | ዋሸ፡ |

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ገራ ፡ | አሠለጠነ ፡ | » | አሰበ ፡ | » | ደረደረ፡(ለርሻ)፡ | ጓጓ ፡ | ተመኘ ፡ |
| » | ልክ፡አስገባ፡ | አተተ ፡ | ዘረዘረ ፡ | አፈለ፡ | ጠገበ፡/በኃይል፡ | ዳጠ ፡ | ደፈጠጠ፡ |
| ዳኘ ፡ | ፈረደ ፡ | ቦረቦረ፡ | ቦደሰ፡ቆሰለ | ሰነጠበ፡ | በጣ ፡ | ተለወሰ፡ | ተበከለ ፡ |
| በየነ፡ | አሻሻለ፡በፍርድ፡ | ደራ ፡ | ዘባ ፡ | ተጀጀበ ፡ | ወፈረ ፡ | ተሳነ ፡ | አቃተ ፡ |
| አሄደ ፡ | አበራየ ፡ | ባዘነ ፡ | ተንከራተተ ፡ | ደከመ ፡ | ታከተ ፡ | ቀባ ፡ | ለቀለቀ ፡ |
| ሮጠ ፡ | ከነፈ ፡ | ባጠጠ፡ | ተሞላቀቀ፡ | ባሰ ፡ | ከፋ ፡ | ተቆጨ ፡ | ተናደደ ፡ |
| » | በረረ ፡ | አበጠረ፡ | አነፈሰ ፡ | ባተ ፡ | ገባ ፡ | ቃረ ፡ | አፋጨ ፡ |
| ዘረዘረ ፡ | መነዘረ፡ | » | አሳመረ ፡ | ዳዳ ፡ | ነሸጠ ፡ | በደለ ፡ | ሳተ ፡ |
| አሰረ ፡ | ቀፈደደ ፡ | ገደመ፡ | ከለለ፡ለቦታ፡ | ዳሰ ፡ | ሸረከተ ፡ | ገደረ ፡ | ሸጠ ፡ |
| አሰረ ፡ | ቨረነፈ ፡ | ኮቸመ ፡ | አሳመረ ፡ | ቀመቀመ፡ | ሰፋ፡(እያጠፈ)፡ | ገደደ ፡ | ጠመመ፡ |
| ቆራ ፡ | አመለከተ ፡ | ሞከከ ፡ | በሰለ ፡ | ኮተኮተ ፡ | ዳከመ ፡ | ጎደበ ፡ | ቆፈረ ፡ |
| » | ጠቆመ ፡ | በጀ ፡ | ጠቀመ ፡ | » | ነገር፡አነሣ፡ | » | ኳተ ፡ |
| » | ጠቀሰ ፡ | » | ረባ ፡ | ቀማ ፡ | ነጠቀ ፡ | አጸና ፡ | አጸደቀ ፡ |
| አስታጎለ፡ | አሰናከለ ፡ | ጋተ ፡ | አጠጣ ፡ | ሸሸ ፡ | ራቀ ፡ | ገደገደ ፡ | ተከለ ፡ |
| » | አዳፈነ ፡ | ዶለ ፡ | ጨመረ ፡ | ጨቀጨቀ፡ | ነዘነዘ፡ | ዛተ ፡ | ፎከረ፡ |
| አደገ ፡ | ጨመረ ፡ | አዘናጎለ፡ | አዘዋወረ፡ | » | አሰለቸ ፡ | ገጨ ፡ | መታ ፡ |
| » | ከፍ ፡ አለ ፡ | ሠዋ ፡ | አረደ፡ | » | ዘበዘበ ፡ | ገታ ፡ | አቆመ ፡ |
| አጎረ ፡ | ዘጋ ፡ | » | አሳልፎ፡ሰጠ | አፈገ ፡ | አጫነቀ፡ | ደላ ፡ | ተመቸ ፡ |
| አደበ ፡ | ታገሠ ፡ | ቆየ ፡ | ዘገየ ፡ | አሸገ ፡ | ዘጋ ፡ | ኖረ ፡ | ተቀመጠ፡ |
| » | ዐረፈ ፡ | ሰማ ፡ | አዳመጠ፡ | አረተ ፡ | አሰረ ፡ | ጣረ ፡ | ለፋ ፡ |
| አከተ ፡ | አከማቸ ፡ | ወተወተ፡ | ነዘነዘ፡ | ተለያየ ፡ | ተበታተነ፡ | ቀጨ ፡ | ሰበረ ፡ |
| » | ሰበሰበ ፡ | » | ነሰተ ፡ | አዋደደ፡ | አስማማ ፡ | » | ባጭር፡አስቀረ፡ |
| ፀነሰ ፡ | አረገዘ ፡ | ገመሰ፤እሁለት፡ከፈለ | | ሚነነ ፡ | መነመነ ፡ | ሳበ ፡ | ጎተተ ፡ |
| | | | | » | አለቀ ፡ | ደደቀ ፡ | ደነጎረ ፡ |

## ተቃራኒ ፡

### የስም ፡ ተቃራኒ ፡

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ሥርጥ ፡ | መዟሪያ ፡ | ውጭ ፡ | ግቢ ፡ | አግድመት፡ | ቁልቁለት፡ | ብሥራት ፡ | መርዶ ፡ |
| ጧት ፡ | ማታ ፡ | አልጋ ፡ | መደብ ፡ | ሜዳ ፡ | ገደል ፡ | ጉድጓድ ፡ | ኩሳይ ፡ |
| ግርድ ፡ | ምርት ፡ | ብስና ፡ | ግማት ፡ | አረሀ፡ | አፋፍ ፡ | ባዛ ፡ | አርባጫ፡ |
| ሰማይ፡ | ምድር ፡ | ደላጎ ፡ | ነት ፡ | ጥግ ፡ | » | አዳጋ ፡ | » |
| ቀልድ፡ | ቁም፡ነገር፡ | ጮማ ፡ | ጉፋያ ፡ | ክርክር ፡ | ስምምነት፡ | | |
| ጠብ ፡ | ሰላም ፡ | ተድላ ፡ | ግዞት ፡ | | | | |

### ጾታዊ ፡ ተቃራኒ ፡

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| አባት ፡ | እናት ፡ | አክሥት ፡ | አጎት ፡ | ጊደር ፡ | ወይፈን ፡ | ሴቴ ፡ | ወንዴ ፡ |
| እኅት ፡ | ወንድም ፡ | በሬ ፡ | ላም ፡ | ባዝራ ፡ | ድንጉላ ፡ | ቄብ ፡ | ወጠጤ፡ |

## የቅጽል ፡ ተቃራኒ ፡

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ቀይ ፡ | ጥቍር ፡ | ብርቱ ፡ | ደካማ ፡ | ጎብዝ ፡ | ሰነፍ ፡ | ንቁ ፡ | ሬሳ ፡ |
| ቅርብ ፡ | ሩቅ ፡ | ጭምት ፡ | ክልፍልፍ ፡ | ጎረምሳ ፡ | ኮረዳ ፡ | » | ፈዛዛ ፡ |
| ሠራተኛ ፡ | ሥራ ፡ ፈት ፡ | » | ክንፍንፍ ፡ | ጥሩ ፡ | መናኛ ፡ | » | ሙት ፡ |
| ዐመለ ፡ ወርቅ ፡ | ዐመለ ፡ ቢስ ፡ | » | ቅብዝብዝ ፡ | ብቸኛ ፡ | መሳይ ፡ | ደንቆሮ ፡ | ብልኅ ፡ |
| ኩሩ ፡ | ትሑት ፡ | ደፋር ፡ | ፈሪ ፡ | ጨዋ ፡ | ባለጌ ፡ | ቡሩክ ፡ | ርጉም ፡ |
| ጠባብ ፡ | ሰፊ ፡ | መናፍቅ ፡ | እምነተኛ ፡ | ታማኝ ፡ | ከዳተኛ ፡ | አሮጌ ፡ | አዲስ ፡ |
| ታላቅ ፡ | ታናሽ ፡ | አዋኪ ፡ | ጸጥተኛ ፡ | በጥባጭ ፡ | ርጉ ፡ | ሕያው ፡ | በድን ፡ |
| ረዥም ፡ | አጭር ፡ | ንፉግ ፡ | ቸር ፡ | ብዙ ፡ | ጥቂት ፡ | » | ሬሳ ፡ |
| ቀጭን ፡ | ወፍራም ፡ | ልባም ፡ | ቀልበ ፡ ቢስ ፡ | ጎታታ ፡ | ቀልጣፋ ፡ | ታታሪ ፡ | በክት ፡ |
| አስተዋይ ፡ | ልበ ፡ ቢስ ፡ | » | ልበ ፡ ውልቅ ፡ | ጥላ ፡ ቢስ ፡ | ደርባባ ፡ | » | ሰነፍ |
| » | አእምሮ ፡ ቢስ ፡ | » | ዐቅለ ፡ ቢስ ፡ | ከውካዋ ፡ | ጎዳዳ ፡ | ረኀጥ ፡ | ንቁ ፡ |
| ደመ ፡ ቢስ ፡ | ደማም ፡ | ድፍርስ ፡ | ጥሩ ፡ | በሽተኛ ፡ | ጤነኛ ፡ | » | ጎበዝ ፡ |
| ዕድለኛ ፡ | ዕድለ ፡ ቢስ ፡ | ውድ ፡ | ርካሽ ፡ | ወዛም ፡ | አመዳም ፡ | ናቂ ፡ | አክባሪ ፡ |
| ሠራተኛ ፡ | ልግመኛ ፡ | ክብረ ፡ ቢስ ፡ | ክቡር ፡ | ፈጣን ፡ | ዳተኛ ፡ | ስጉ ፡ | ግድ ፡ የለሽ ፡ |
| ቀሪ ፡ | ሂያጅ ፡ | ቋሚ ፡ | ተቀማጭ ፡ | ገቢ ፡ | ወጪ ፡ | ሰላማዊ ፡ | በጥባጭ ፡ |

## የግስ ፡ ተቃራኒ ፡

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ጎሸ ፡ | ጠራ ፡ | ቀለዘ ፡ | ወጀለተ ፡ | ገታ ፡ | ለቀቀ ፡ | ለማ ፡ | ጠፋ ፡ |
| ዘጋ ፡ | ከፈተ ፡ | ጠጠረ ፡ | ላላ ፡ | ነቀፈ ፡ | አመሰገነ ፡ | አማ ፡ | አሞገሰ ፡ |
| እጣ ፡ | አገኘ ፡ | ራራ ፡ | ጨከነ ፡ | አከለ ፡ | አሳነሰ ፡ | በጠሰ ፡ | ቀጠለ ፡ |
| ነሣ ፡ | ሰጠ ፡ | ለመነ ፡ | ሰጠ ፡ | አመነ ፡ | ካደ ፡ | ረሳ ፡ | አስታወሰ ፡ |
| አከበረ ፡ | አዋረደ ፡ | ጠላ ፡ | ወደደ ፡ | ጠባ ፡ | ጣለ ፡ (ለጡት) ፡ | ናደ ፡ | ካበ ፡ |
| አጐደለ ፡ | ሞላ ፡ | ዘራ ፡ | ለቀመ ፡ | በተነ ፡ | ሰበሰበ ፡ | ዘለዘለ ፡ | መተረ ፡ |
| ጦፈ ፡ | በረደ ፡ | አዘነ ፡ | ተደሰተ ፡ | ወዛ ፡ | ነጣ ፡ | » | ቆነቆነ ፡ |
| ነፋ ፡ | አስተነፈሰ ፡ | ተከፋ ፡ | » | ገባ ፡ | ወጣ ፡ | ነደደ ፡ | በረደ ፡ |
| ነፃ ፡ | ረከሰ ፡ | ነቃ ፡ | ተኛ ፡ | ኖረ ፡ | ሞተ ፡ | » | ጠፋ ፡ (ለእሳት) ፡ |
| ሠባ ፡ | ጎፈየ ፡ | » | አንቀላፋ ፡ | ቸረ ፡ | ሣሣ ፡ | ተቀመጠ ፡ | ቆመ ፡ |
| ራሰ ፡ | ደረቀ ፡ | ረታ ፡ | ተሸነፈ ፡ | » | ነፈገ ፡ | » | ተነሣ ፡ |
| ሳመ ፡ | ነከሰ ፡ | ተቀበለ ፡ | ተቃወመ ፡ | ሸጠ ፡ | ገዛ ፡ | ሾመ ፡ | ሻረ ፡ |
| ቆመ ፡ | ሄደ ፡ | ሰበሰበ ፡ | በተነ ፡ | ፈታ ፡ | አገባ ፡ | ሰበረ ፡ | ጠገነ ፡ |
| ሮጠ ፡ | ዝግ ፡ አለ ፡ | ራቀ ፡ | ቀረበ ፡ | » | አሰረ ፡ | ቀላ ፡ | ጠቆረ ፡ |

## በሐረግ ፡ የሚፈቱ ፡ ቃላት ፡

| | | | |
|---|---|---|---|
| አለባሚ ፡ | ልቡና ፡ ሰጭ ፡ | ተሲያት ፡ | ዘጠኝ ፡ ሰዓት ፡ |
| መባቻ ፡ | የወር ፡ መዠመሪያ ፡ ቀን ፡<br>መግቢያ ፡ ቀን ፡ | ሐምራይ ፡ | የበሰለ ፡ ወይን ፡ ዐይነት ፡ ቀለም ፡ |
| | | መክፈያ ፡ | ሽንት ፡ መሸኛ · |

አእምሮ ፡ ጠባይ ፡ የተፈጥሮ ፡ ዕውቀት ፡
አሳባሪ፡ ማቋረጫ ፡ መንገድ ፡
ግጭት፡ የሁለት፡ ኀይል፡መገናኘት፡
አለት ፡ ንጣፍ ፡ ደንጊያ ፡
የጨለማ፡ዘመን፡ የክፋትና ፡ የድንቁርና ፡ ዘመን ፡
መቦዘን ፡ ያለሥራ ፡ መቀመጥ ፡
በተሐ ፡ በጣም ፡ ያልፈላ ፡ ጠጅ ፡
ቅምጥ ፡ የማሽላ ፡ ነዶ ፡ (ወደ፡ ድራ ውማ ፡ ሳይመጣ) ፡
አንቲካ ፡ የጥንት ፡ ሥራ ፡
ነቁጥ ፡ ሁለት ፡ ነጥብ ፡
ብልት ፡ የሥጋ ፡ ዐይነት ፡ ወይም፡ የሰውነት ፡ ክፍል ፡
ዓመተ ፡ ስማዕታት ፡ የመከራ ፡ ዘመን ፡
በጠጥ ፡ የፍየል ፡ ፍግ፡
እብቅ ፡ ጤፍ፡ተወቅቶ፡ጭዱ፡ከተነሣ፡ በኋላ ፡ የሚገኝ ፡ ገለባ ፡
ፖለቲክ ፡ ያስተዳደርና፡ የነገራት፡ ዘዴ፡
አቦል ፡ የመዠመሪያ፡ቡና፡(ተወቅጦ፡ በተፈላበት ፡ ጊዜ፡ ነው) ፡
እብድ፡ አእምሮ ፡ የተለየው ።
ሳጋ ፡ የእንጨት ፡ ቤት፡ ሲሠራ፡ የሚሻጥ ፡ እንጨት ፡
ቃታ ፡ ከመሮጥ፡ የተነሣ፡ የሚነሣ፡ ሲቃ፡
» በጠመንዣ ፡ ውስጥ፡ የሚ ገኝ ፡ ተሞልቃቂ ፡
ባልጩት፡ ስለታም ፡ ደንጊያ ፡
ቀፎ ፡ የንብ፡ ቤት ፡
መባነን ፡ በድንገት፡ መንቃት፡
» በእንቅልፍ፡ ልብ፡መለፍለፍ፡
ቆቅ ፡ እንደ ፡ ዶሮ፡ ያለች፡ በዱር ፡ የምትኖር ፡
» ጠርጣሪ፡ወይም፡ገንጋኝ፡ሰው፡
ኮረኮንቻ ፡ ድንጋያማ ፡ መሬት ፡
አሚን ፡ የመዠመሪያ፡ ሚስት፡ወይም፡ ባል ፡
አምቦ ፡ ጨው ፡ ጨው ፡ የሚል ፡ መሬት ፡ ወይም ፡ ውኃ ፡
ገዳም ፡ ገለልተኛ ፡ ሥፍራ ፡

መክፈያ ፡ የደመወዝ ፡ መስጫ ፡
በዓለ፡ሠዊት፡ የሸት ፡ ወራት ፡
ብርቅ ፡ እንግዳ ፡ ነገር ፡
ቦዳ ፡ ቀይ ፡ መሬት ፡
ገና ፡ የጌታችን ፡ ልደት ፡ ቀን ፡
ገና ፡ የቁርቁስት ፡ ጫወታ ፡
ዐዛባ፡ የከብት ፡ ፍግ ፡
መግደፍ ፡ ቀለምን ፡ መሳት ፡
» ጠምን ፡ መፍታት ፡
መደርደር ፡ በደንብ ፡ ማስቀመጥ ፡

መጽሔታዊ ፡ መስተዋታዊ ፡ ድርሰት ፡
መስተዋት ፡ ልናየው ፡ የማ ንችለውን ፡ ነገር ፡ ገልጾና ፡ አጉልቶ፡እንደሚያሳየን፡መስ ተዋታዊ ፡ ወይም ፡ ሥዕላዊ፡ ድርሰትም ፡ ሊገለጽ ፡ የሚ ገባውን ፡ ነገር፡ አሰማምሮ፡ የሚያስረዳ ፡ ነው ።

ዜናን ፡ አኀልማሽ ፡ ድርሰት ፡
አንድ ፡ ነገርን ፡ ከተዠመረ በት ፡ ጊዜ፡ አንሥቶ ፡ እስከ፡ መጨረሻው ፡ ድረስ ፡ በማ ጋነን ፡ የሚያስረዳ ፡ ነው ።
የኅሊናን ፡ አሳብ ፡ መመዘኛ ፡ ድርሰት ፡
በዐይን ፡ የታየውንና ፡ በኅ ሊና ፡ የተሰማውን ፡ ነገር ፡ መገመቻ ፡ ወይም ፡ ሚዛን ፡ መስጫ ፡ ድርሰት ፡ ነው ።
ሥዕላዊ ፡ ድርሰትና፡ ሥዕላዊ ፡ ቅጽል ፡
በሚሰጡት፡ትርጓሜ፡ እንደ፡ ሥዕል ፡ግልጽ ፡ አድርገው፡ ስለሚያሳዩ፡ተሰየሙ፡እንጂ፤ በርግጡ ፡ በሥዕል ፡ አያሳዩ ምና፡ ተጠንቅቆ ፡ ማጥናት ፡ ይገባል ።

# ፫ኛ ፡ ክፍል ፡ ምሥጢርን ፡ የሚያጎሉ ፡ ን ግ ግ ሮ ች ፡

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ፡ ተረትና ፡ ምሳሌ ።

ተረትና ፡ ምሳሌ ፡ የጥንት ፡ አባቶቻችን ፡ አንድ ፡ ነገርን ፡ ጎላ ፡ ባለ ፡ አጭር ፡ ዘዴ ፡ ይገልጹበት ፡ የነበረው ፡ ምሳሌያዊ ፡ ንግግር ፡ ነው ። ተረት ፡ የተባለበት ፡ የቈየ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ነው ። ተረትና ፡ ምሳሌ ፡ በየጊዜው ፡ እየጨመረ ፡ የሚሄድ ፡ አገላለጽ፡ ነው፡ እንጂ ፤ የሚወሰን ፡ አይደለም ።

አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ያማርኛ፡ ተረትና ፡ ምሳሌ፡ መልካሙን ፡ የግብረ፡ ገብነትን ፡ ትምህርት ፡ ይዞ ፡ ስለሚገኝ ፤ ወጣቶች ፡ እየተመገቡ ፡ እንዲያድጉበት ፡ ያስፈልጋል ።

### ተረትና ፡ ምሳሌ ፡ ከነትርጕማቸው ፡

1 የምትታጠቀው ፡ ቀሚስ ፡ ሳይኖራት፡ የምትደርበው ፡ ኩታ፡ አማራት፡- ማለት፡ ለጊዜው ፡ ዐቅሟ ፡ የሚፈቅድላትን ፡ ከማድረግ ፡ ይልቅ ፡ ዐቅሟ ፡ የማይፈቅድላትን ፡ ለማድረግ ፡ ትጣጣራለች ፡ ማለት ፡ ነው ።

2 ፍርድ ፡ አያውቅ ፡ ዳኛ ፡ ተገን ፡ አያውቅ ፡ እረኛ ፡- አንድ ፡ ጉትት ፡ እረኛ ፡ መንጎቹን ፡ ወደ ፡ ለመለመ ፡ መሠማሪያ ፡ እንደማያውላቸውና ፡ ሊያርፉበትም ፡ የሚገባቸውን ፡ ምሳግ ፡ እንደማይፈልግላቸው ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁም ፡ አንድ ፡ የተፈጥሮ ፡ አስተያየት ፡ የሌለው ፡ ዳኛ ፡ በመንጋ ፡ የተመሰሉትን ፡ ሕዝብ ፡ ያላገባብ ፡ ፍርድ ፡ እያጓደለ ፡ ያጉላላቸዋል ፡ ማለት ፡ ነው ።

3 ሳይገድሉ ፡ ጎፈሬ ፡ ሳያስረግጡ ፡ ወሬ ፡- ያልሠሩትን ፡ ሥራ ፡ ሠርቻለሁ ፡ ማለት ፡ እንደሚያዋርድና ፡ እንደሚያስንቅ ፡ ወሬንም ፡ ከምንጩ ፡ ሳያስረግጡ ፡ ማውራት ፡ ከክፉ ፡ አደጋ ፡ ላይ ፡ ይጥላል ፡ ማለት ፡ ነው ።

4 ደባ፡ ራሱን ፡ ስለት ፡ ድጉሱን ፡-በጣም ፡ የሰላ ፡ ጎራዴ ፡ የራሱን ፡ መሸፈኛና ፡ ከለላ ፡ የሚሆነውን ፡ ሰገባ ፡ እንደሚቀደው ፡ በጣም ፡ ደባ ፡ የሚያበዛ ፡ ሰው ፡ በዚያው ፡ በደባው ፡ ይጠፋል ።

5 ሲሞቱ ፡ ገመድ ፡ ሲሾሙ ፡ ዘመድ ፡ አይታጣም ፡-ምንም ፡ ሲቸግር ፡ ቢውል፡ አንድ ፡ ሰው ፡ በሞተ ፡ ጊዜ ፡ ለመገነዣ ፡ የሚሆን ፡ ፈትል ፡ አይጠፋም ፤ እንዲሁም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ በተሾመ ፡ ጊዜ ፡ እበላ ፡ ባይ ፡ አሰፍሳፊ ፡ ከየሥፍራው ፡ ወይም ፡ ከየሥርቻው ፡ እየተለቃቀመ ፡ የሚመጣ ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ አይታጣም ፡ ማለት ፡ ነው ።

6 ቀበቶዬ ፡ ላልቷል ፡ የሚያጠብቅልኝ ፡ እፈልጋለሁ ። ርቦኛል ፡ ምግብን ፡ እፈልጋለሁ ፡ ማለት ፡ ነው ።

7 አንድ ፡ የሥራ ፡ መሪ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ በዕረፍት ፡ ጊዜው ፡ ተቀምጦ ፡ ምግቡን፡ ያላምጣል ። አንድ ፡ ሥራ ፡ አስኪያጅ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ጊዜውን ፡ በመጠበቅ ፡ ከሥራ ፡ ሰዓቶቹ ፡ ውጭ ፡ ለሥራው ፡ ተስማሚ ፡ የሚሆነውን ፡ የሥራ ፡ ዐቅድ ፡ በብርቱ ፡ ያስባል ፤ እንደዚህም ፡ ማለት ፡ የሥራ ፡ ጊዜውን ፡ ብቻ ፡ ሳይተማመን ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ይሠራል ፡ ማለት ፡ ነው ።

8 ሥራ ፡ ፈት ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ አንድ ፡ ነገርን ፡ ሲመለከት ፡ ላም ፡ ነው ። እንደዚሁ ፡ አጦርጢሪ፡ ላም ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ፡ ቀና ፡ ብላ ፡ ሁለት፡ ገሮቿን ፡ ወደ ፡ ዐይኖቿ ፡ ቀልሳ ፡ ሣር ፡ መብላቷን ፡ ትታ ፡ ስትመለከት ፡ እኩል ፡ ሰዓት ፡ ያህል ፡ ታጠፋለች ። አንዳንድ ፡ ሰውም ፡ ሥራውን ፡ ወይም ፡ የሥራውን ፡ ሐሳብ ፡ ትቶ ፡ አንድ ፡ የማይጠቅም ፡ ከንቱ ፡ ነገርን ፡ ሲመለከት ፡ ለሥራው ፡ የ ተወሰነውን ፡ ጊዜና ፡ የሥራ ፡ ዐቅድ ፡ ያባክናል። እንደዚህ ፡ ያለውም፡ ሰው ፡ ዕድሜ፡ ካለፈ ፡ አይመለስም፡ የሚለውን፡ አማርኛ ፡ አያስተውልም ፡ ማለት ፡ ነው ።

9 አቶ ፡ ማን ፡ አለብኝ ፡ ምሥጥ ፡ ነው ። አቶ ፡ ማን ፡ አለብኝ ፡ ማለት ፡ በራሱ ፡ ፈቃድ ፡ ብቻ ፡ ነዋሪና ፡ ለሰው ፡ ድካም ፡ የማያስብ ፡ ነው ። ምሥጥም ፡ በበረሃ ፡ አገር ፡ ውስጥ ፡ በሰው ፡ ርስት ፡ ላይ ፡ ኩይሳን ፡ ተራራ ፡ አስመስሎ፡ በአፈር፡ ሲክብ ፡ ይገኛል። እንዲሁም ፡ ሰው ፡ ለጥቅሙ ፡ በሠራው ፡ ቤት ፡ በሥር ፡ እየወጣ ፡ ምርጊቱን፡ በመናድና፡ እንጨቱን ፡ እየጋጠ ፡ በመሰባበር ፡ የሰውን ፡ ንብረት ፡ ያፈርሳል ። በዚህ ፡ ረገድ ፡ እነዚህ ፡ ትንንሽ ፡ ነፍሳት ፡ ይህን ፡ ካብ፤ ወይም ፡ ትልቅ ፡ ቋጥኝ ፡ መስሎ ፡ የሚታየውን ፡ አፈር ፡ የሚሠሩና ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ አዳራሽን ፡ የሚያፈርሱ ፡ አይመስሉም ። እንደዚሁም ፡ ባስተያየት ፡ ደጎና ፡ መስሎ ፡ የሚታየው ፡ ሰውዬ ፡ በማይታወቅ ፡ መንገድ ፡ ያዋቂዎችን ፡ ምክር ፡ ቸለል ፡ በማለት ፡ ሰውን ፡ ሲያጠፋና ፡ የሰውን ፡ ንብረት ፡ ሲያፋልስ፡ ይገኛል ።

10 በውቀቱ ፡ የተመካ ፡ ጥንቸል ፡ ነው ። ለዚህ ፡ አንድ ፡ ታሪክ ፡ ይተረካል ። ጥንቸልና ፡ ዔሊ ፡ እሽቅድምድም ፡ ሊያደርጉ ፡ ተዋዋሉና ፡ የመድረሻው ፡ ቦታ ፡ ተወስኖላቸው ፡ እሽቅድምድማቸውን ፡ ዠመሩ ። ወዲያው ፡ ትንሽ ፡ እንደ፡ ሮጡ ፡ ጥንቸሉ ፡ ዔሊውን ፡ ረዥም ፡ መንገድ ፡ ትቶት ፡ ሂደና ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ ቢመለከት ፡ ዔሊውን፡ ከመነሻው ፡ ቦታ ፡ ምንም ፡ ያህል ፡ እንዳልራቀ ፡ አየ ። ስለዚህ ፡ ጥንቸሉ ፡ በፍጭነቱ፡ ተመክቶ ፡ ይህ ፡ ጎታታ ፡ እስከ ፡ ነገም ፡ እዚያ ፡ አይደርስም ፡ አለና ፡ እንቅልፉን ፡ ለማሳለፍ ፡ ባንድ ፡ ዛፍ ፡ ሥር ፡ ተኛ ። ዔሊው ፡ ግን ፡ ተስፋ ፡ ባለመቍረጥ ፡ እንደዚያው ፡ እየተጎተተ ፡ ወደ ፡ እሽቅድምድሙ ፡ መጨረሻ ፡ ሥፍራ ፡ ሊደርስ ፡ ሲል ፡ ጥንቸሉ ፡ ከንቅልፉ ፡ ነቅቶ ፡ ቢመለከተው ፡ ቀድሞት ፡ እንደ፡ ደረሰ ፡ ተረዳው ። ስለዚህ ፡ አዬ ፡ ከእንግዲህስ ፡ ወዲያ ፡ አልደርስበትም ፡ ብሎ ፡ ተስፋ ፡ ቈረጠ ። ድሉም ፡ ያቶ ፡ ዔሊ ፡ ሆነ ፡ ይባላል ። ይህ ፡ ተረት ፡ የሚያስተምረን ፡ ተስፋ ፡ ያልቈረጠ ፡ የመጨረሻውን ፡ ድልና ፡ ዕድል ፡ ማግኘቱንና ፡ በውቀቱ ፡ ወይም ፡ ባቅሙ ፡ የተመካ ፡ ዕውቀቱ፡ ወይም፡ ትምክሕቱ ፡ አደጋ ፡ አስገኚ ፡ መሆኑን ፡ ነው ።

11 እሞኝ ፡ ደጅ ፡ ሞፈር ፡ ይቈረጣል ። አንድ ፡ ሰው ፡ ቸር ፡ በመሆኑ፡ ከሀብቱ፡ ለተቸገሩ ፡ ሲሰጥ ፡ ያዩ ፡ ሁሉ ፡ እገሌ ፡ ቤት ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ይገኛል ፡ እያሉ ፡ በማታለል ፡ ከእጁ ፡ እስኪያጣ ፡ ድረስ ፡ የሰበሰበውን ፡ ይወስዱበታል ። ከመጠኑ፡ ያለፈ፡ ደግነት ፡ ሙልጭ ፡ ያስወጣል ።

12 ካይን ፡ ጆሮ ፡ አይታመንም ። በውነቱ ፡ አንዳንድ ፡ ሰዎች፡ ዐይናቸው፡ እያየ፡ ልባቸው ፡ ካለማስታዋሉ ፡ የተነሣ ፡ አንዳች ፡ ነገር ፡ ሲወድቅ ፡ ሲሰበር ፡ ሲፈስና ፡ ሲበላሽ ፡ እየተመለከቱ ፡ አብረዋቸው ፡ (የነበሩትን)፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ ወይም ፡ አብሯቸው፡ ያለውን ፡ ሰው ፡ ምን ፡ ወደቀ ? ምን ፡ ተሰበረ ? ምን፡ ፈሰሰና ፡ ተበላሸ ? ብለው እንዳዲስ፡ ነገር ፡ ይጠይቃሉ ። ማንኛውም ፡ ፍጡር ፡ ልቡ ፡ ጭምር ፡ ካላየ ፡ ዐይኑ፡ ብቻ ፡ አፍጦ ፡ ቢመለከት ፡ አይገነዘበውም ፡ ንብ ፡ የሌለው ፡ ቀፎ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ለዚሁም፡ እንደዚህ፡ እየተባለ፡ ይተረታል፤ አንድ፡ ሴትዮ፡ ባሏ ፡ በጠና ፡ ታመው ፡ ጣር ፡ ይዟቸው ፡ ሲንፈራገጡ ፡ ዝም ፡ ብላ ፡ ትመለከት ፡ ነበረች ። ባኳኋናም ፡ ሰው ፡ ዬው ፡ ተደንቀው ፡ እባክሽ ፡ ሄደሽ ፡ ጎረቤት ፡ ጥሪ ፡ አሏት ፤ እርሷ ፡ ግን ፡ ፈጥና ፡ በመሄድ ፡ ፈንታ ፡ አዬ ፡ ጌታ ፡ መሞትዎ ፡ ነው ፡ እንዴ ? ብላ ፡ ብትጠይቃቸው ፡ ኋላ ፡ የማንን ፡ ስልቻ ፡ ሳለፋ ፡ ታዪኛለሽ ፡ አሏት ፡ ይባላል ።

<u>፲፫ኛ ፡ መልመጃ ፡</u>

(ሀ) የሚከተሉትን ፡ ሐረጎች ፡ አስረዳ ።

1 እየተጎሳቆለና ፡ እየደገደገ ፡

2 አምሳ ፡ ሎሚ ፡ ላንድ ፡ ሰው ፡ ሸክሙ ፡ ነው ፤ ላምሳ፡ ሰው፡ ግን፡ ሽታው፡ ነው።

3 የድኃ ፡ መድኅኒት ፡ ጭንቀት ፡

4 ብረት ፡ ካልፈላ ፡ አይላላ ።

5 እንግዳ ፡ ሳይመጣ ፡ ሁሉ ፡ ሴት ፡

6 መታለል ፡ ገደል ፡ መንከባለል ፡

7 ዕንቍላሎችህ ፡ ተፈልፍለው ፡ ዶሮችህን ፡ እስክታገኛቸው ፡ ድረስ ፡ አትቍጠራቸው ።

8 ያገሩን ፡ ሰርዶ ፡ ባገሩ ፡ በሬ ፡

9 የሰው ፡ አገሩ ፡ ምግባሩ ፤ የከብት ፡ አገሩ ፡ ጌታው ፡

10 ያፍ ፡ ወለምታ ፡ በቅቤ ፡ አይታሽም ።

11 (ሀ)ልብ ፡ ወለድ ፡ (ሐ) ጥራዝ ፡ ነጠቅ ፡ (ሠ)ሕገ ፡ ውጥ ፡
(ለ) ሰው ፡ ጤፉ ፡ (መ) ኩታ ፡ ገጠም ፡ (ረ) ግንደ—በል ፡

(ለ) በሚከተሉት ፡ ቃላት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ሥራ ።

ጠገተ ፡ ጉር ፡ ጉርጥ ፡ ጉብል ፡ ጊድራ ፡ ጊጤ ፡ ጋመ ፡ ግላስ ፡ ተረዳ ፡ ግፍልፍል ፡ ጎመዳም ፡ ጎለመ ፡ ጉማጅ ፡ ጎመራ ፡ ጎረበ ፡ ጎሸመጠ ፡ ጎተነ ፡ ጎፈየ ፡ ደፈደፈ ፡ ድግ ፡ ወባት ፡ ወደረ ፡ ወጌሻ ፡ ሠረገ ።

(ሐ) የሚከተሉትን ፡ ቃላት ፡ ግለጻቸው ።

ማየ፡ አይኅ፡ ዘወርዋራ ፡ መንገድ ፡ ግር፡ ብለው ፡ ትውክልት፡ መደ ኀኒት ፡ በጣቅ፡ በጫወታ ፡ ማሳለፍ ፡ እምብዛም ፡ አርጅተው ፡ ጥቀርሻ ፡ እርም ፡ ታህል ፡ ጊዜ ፡ ዐይ ኖቼን ፡ ስለ ፡ ከሠትህልኝ ፡ ዘል ፡ ማን ፡ ዘል ፡ ማለት ፡

(መ) በሚከተሉት ፡ ቃላት ፡ ጥገኛ ፡ ሐረጎችን ፡ ሥራ ።

ተመረኰዘ ፡ ጠረበ ፡ መረዘ ፡ በዘበዘ ፡ ጎለመሰ ፡ ዐተር ፡ አርነት ፡ ገነዘ ፡ ደነዘዘ ፡ ጠረዘ ፡

(ሠ) ለሚከተሉት ፡ ቃላት ፡ ተቃራኒ ፡ ስጥ ።

ሸተ ፡ ሰማዕት ፡ በደለኛ ፡ መጋረጃ ፡ እንጀራ ፡ ከርክር ፡ ምሽት ፡ ወዛ ፡ ቀለጠ ፡ ሰፋ ፡ አጣላ፡ ደረቀ ፡ አሮጌ ፡ ወጣት፡ አመነ ፡ ሰነፈ፡ አዘነ ፡ ነፈገ ፡ ከፋ፡ ተዋረደ ፡ አጠፋ፡

(ረ) ተስማሚ ፡ አርእስት ፡ መርጠህ ፡ የሚከተሉትን ፡ ምሳሌዎች ፡ አስገባና ፡ ድርሰት ፡ ጻፍ ።

1 ድር ፡ ቢያብር ፡ አንበሳ ፡ ያስር ።
2 ያልጠረጠረ ፡ ተመነጠረ ፡
3 መታፈር ፡ በከንፈር ፡
4 የሺ ፡ ፍልጥ ፡ ማሰሪያው ፡ ልጥ ፡
5 አንገት ፡ የተፈጠረው ፡ አዙሮ ፡ ለማየት ፡ ነው ።

ልዩ ፡ ልዩ ፡ ተረቶችን ፡ የያዘ ፡ ድርሰት ፡

አንድ ፡ ሀብታም ፡

ከብዙ ፡ ዓመታት ፡ በፊት ፡ አቶ ፡ ሞልቶት ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡ ሀብታም ፡ ሰው ፡ በሸዋ ፡ ይኖር ፡ ነበር ። ይህም ፡ ሰው ፡ የበለጸገና ፡ ትሕትና ፡ ያለው ፡ ሰው፡ በመሆኑ፡ብዙ፡ ሰዎች ፡ ያከብሩትና ፡ ይፈሩት ፡ ነበር ። ከደግነቱም ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ለሰዎች ፡ ያላራጣ፡ ገንዘቡን ፡ ያበድር ፡ ስለ ፡ ነበር ፡ ድሆች ፡ ጎረቤቶቹን ፡ ያግዝ ፡ ነበር ።

አንድ ፡ ተንኰለኛ ፡ ሰው ፡ ገንዘቡን ፡ ተበድሮ ፡ እየተሰወረ ፡ ሲኖር ፡ ከዕለታት፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ለጉዳዩ ፡ ወደ ፡ አደባባይ ፡ ወጥቶ ፡ ሳለ ፡ ሰውዬውን ፡ በድንገት ፡ አገኘው። ተበዳሪውም ፡ እስካሁን ፡ ድረስ ፡ ረስቶት ፡ ይሆናል ፡ ስለዚህ ፡ ስለ ፡ ገንዘቡ ፡ አይጠይቀ ኝም ፡ እያለ ፡ ሲያወጣ ፡ ሲያወርድ፡ የወጋ ፡ ቢረሳ ፡ የተወጋ ፡ አይረሳምና ፡ ሀብታሙ ፡ ተበዳሪውን ፡ በሰላም ፡ ካነጋገረው ፡ በኋላ ፡ በስውር ፡ ማመልከቻ ፡ ጽፎ ፡ ከሰሰው ።

ሰነፍ ፡ እረኛ ፡ ከሩቅ ፡ ይመልሳል ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ሁሉ ፡ ይህ ፡ ባለጸጋ ፡ ባጠ ገቡ ፡ ሳለ ፡ ወዲያው ፡ ጉዳዩን ፡ እንደ ፡ ፈጸመ ፡ ሳይጠይቀው ፡ ቆይቶ ፡ አሁን ፡ ተረስቶ፡ በነበረው ፡ ገንዘብ ፡ ሊዛለል ፡ ነው ። ተበዳሪውም ፡ ምን ፡ ያምጣ ፡ ድኃ ፡ ምን ፡ ያግባ ፡ ውኃ ፡ የሚባለውን ፡ ተረት ፡ እያሰላሰለ ፡ «መበደሩንስ ፡ ተበድሬ ፡ ነበር ፡ ነገር ፡ ግን ፡ አሁን ፡ የምከፍለው ፡ የለኝም ፡ ብዬ ፡ ለዳኞች ፡ ብነግራቸው ፡ አንድ ፡ አስተያየት ፡ ያደር ጉልኛል» ፡ በማለት ፡ ተስፋ ፡ አደረገ ። እንደዚሁም ፡ በዳኛ ፡ ፊት ፡ ቀረበና ፡ ሲጠየቅ ፡

አመነ ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ ምንም ፡ የሌለው ፡ መለጫ ፡ ድኃ ፡ መሆኑን ፡ ለዳኞቹ ፡ አመለከታቸው ። ዳኞቹም ፡ ፍርድ ፡ አያውቅ ፡ ዳኛ ፡ ተገን ፡ አያውቅ ፡ እረኛ ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ያሉ ፡ ነበሩና ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ከቆየስ ፡ አሁን ፡ ልትጠይቀው ፡ አይገባህም፡ ብለው፡ በሀብታሙ ፡ ላይ ፡ ፈረዱበት ።

በዚህ ፡ ነገር ፡ አቶ ፡ ሞልቶት ፡ ተናዶ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ። አቶ ፡ ቢሰውር ፡ ሊጠይቀው ፡ ቢመጣ ፡ ሲናደድና ፡ ሲበሳጭ ፡ አገኘው ። እሱም ፡ ጥቂት ፡ ትዕግሥት ፡ እንዲያደርግ ፡ ከነገር ፡ ክፉ ፡ ቍጭት ፡ ካውሬ ፡ ክፉ ፡ ድርጭት ፡ የተባለውን ፡ ተረት ፡ ከዚህ ፡ በፊት ፡ አልሰማህምን ? ባይሆንስ ፡ እንዴት ፡ እስከዚህ ፡ ድረስ ፡ ትበሳጫለህ ? አይሆንም ! ከቶ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ሥራ ፡ እንዳይደግምህ ፤ ስለዚህ ፡ ለወደ ፡ ፊቱ ፡ አባት ፡ ካነሰው ፡ ምግባር ፡ ያነሰው ፡ የተጎዳና ፡ የተበላሸ ፡ መሆኑን ፡ እያሰብህ ፡ ገንዘብህን ፡ አታበድር ፡ ብሎ ፡ መከረው ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አቶ ፡ ሞልቶት ፡ ለካ ! ሰዶ ፡ ማሳደድ ፡ ቢያምርህ ፡ ዶሮህን ፡ በቆቅ ፡ ለውጥ ፡ ተብሎ ፡ የተነገረው ፡ ይህን፡ የመሳሰለ፡ ችግር ፡ ለሚገጥማቸው ፡ ሰዎች ፡ ኖሯል ፡ ብሎ ፡ ከዚያ ፡ ጊዜ ፡ ዠምሮ ፡ ገንዘብ ፡ ማበደሩን ፡ አቋረጠ ፡ ይባላል ።

ነገር ፡ ግን ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ያንድ ፡ ሰው ፡ ኃጢአት ፡ ለዘወትር ፡ ወይም ፡ ለሁል ጊዜ ፡ ተደብቆ ፡ አይኖርምና ፤ ይህ ፡ ተበዳሪ ፡ እንደ ፡ ልማዱ ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ ሲያታልል ፡ በፖሊሶች ፡ እጅ ፡ ተያዘና ፡ ታሰረ ፤ ቅጣቱንም ፡ በሚገባ ፡ ተቀበለ ። ይኸውላችሁ ፡ እውነትና ፡ ትጋት ፡ እያደር ፡ ይገለጣል ፡ የተባለው ፡ ይህ ፡ ነው ። አስቀድሞ ፡ ገና ፡ በሕፃንነቴ ፡ ሳለሁ ፡ አባቶቻችን ፡ የአቡነ ፡ ዘበሰማያት ፡ ጦር ፡ ሲወጋ ፡ እንጂ ፡ ሲወረወር ፡ አይታይም ፡ እያሉ ፡ ሲያወሩ ፡ እሰማ ፡ ነበር ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ እውነት ፡ መሆኑን ፡ እስካሁን ፡ አላረጋገጥሁም ።

ስለዚህ ፡ የታገሠ ፡ ሰው ፡ የጠላቱን ፡ አወዳደቅ ፡ ለማየት ፡ ይችላልና ፡ ማንኛውንም ፡ ነገር ፡ በተቻለ ፡ መጠን ፡ በትዕግሥት ፡ መጠበቅ ፡ ይገባል ።

## ያልተተረጐሙ ፡ ተረትና ፡ ምሳሌዎች ፡

1 ልጅቱ ፡ ለቤተ ፡ ሰቦቹዋ ፡ እንደ ፡ ንብ ፡ ነች ።
2 አንገት ፡ የተፈጠረው ፡ አዙሮ ፡ ለማየት ፡ ነው ።
3 ለተቸገረ ፡ የማያዝን ፡ እንብርት ፡ የለውም ።
4 ቀኑ ፡ የጨለመበት ፡ መንገዱ ፡ ዘንግ ፡ ነው ።
5 አድሮ ፡ ቃሪያ ፡ ሆንሁ ፡ እንጂ ፤ አባቴስ ፡ አስተምሮኝ ፡ ነበር ።
6 ለቤቱ ፡ ምሰሶ ፡ አያስፈልገውምና ፡ ይልቁንስ ፡ ወንበር ፡ ፈልግ ።
7 አቶ ፡ እንደ ፡ ልቡ ፡ ሲናገር ፡ ወናፍ ፡ ነው ።
8 አላዋቆች ፡ ባልታዘዙበት ፡ ሥፍራ ፡ ተገኝተው ፡ ነገር ፡ ሲበሉ ፡ (ይገኛሉ) ፡ ይውላሉ ።

9 ሀኬተኛ ፡ ሰው ፡ ሥራው ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ድብ ፡ ነው ።
10 በሕይወቴ ፡ የሌሊት ፡ ወፍ ፡ መሆንን ፡ አልመኘም ።
11 በኑራቸው ፡ ያልተደሰቱ ፡ ባልና ፡ ሚስት ፡ ዘወትር፡ ውሻና ፡ ድመት ፡ ናቸው ።
12 ሰነፍ ፡ ሥራ ፡ ሲያይ ፡ ወደ ፡ ጎኑ ፡ ይሄዳል ።
13 እቶ ፡ ማን ፡ አለብኝ ፡ ምሥጥ ፡ ነው ።
14 በዕውቀቱ ፡ የተመካ ፡ ጥንቸል ፡ ነው ።
15 ልጆቼን ፡ ንጉንቸር ፡ መሆንን ፡ በመከልከል ፡ ድመት ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ አስተ
ምራቸዋለሁ ።
16 ባልንጀራዬን ፡ እንዳልረዳው ፡ እጄ ፡ አጭር ፡ ነው ።
17 መልካም ፡ አባት ፡ ለልጆቹ ፡ እጁን ፡ እኪሱ ፡ ይከታል ።
18 እባክህ ፡ ወንድሜ ፡ ልብህን ፡ ስጠኝ ።
19 መጽሐፍ ፡ የማይወድ ፡ ተማሪን ፡ በጁ ፡ አስተምረው ።
20 ዘር ፡ ዘርተህ ፡ ስንዴና ፡ እንክርዳዱን ፡ ለይ ።
21 ያልተማረ ፡ (ሞኝ) ፡ ሲናገር ፡ ዐጥንት ፡ ይሰብራል ።
22 ለነገረኛ ፡ ሰው ፡ ዠርባህን ፡ ስጠው ።
23 ምሥጢርህን ፡ ለጥርሰ ፡ ፍንጭት ፡ ሰው ፡ አታጫውት ።
24 ተኳሽ ፡ በሁለት ፡ ዐይኖቹ ፡ አያነጣጥርም ።
25 የባለጌ ፡ ሰው ፡ ኪሱ ፡ ቀዳዳ ፡ ነው ።
26 ምሥጢረኛ ፡ ምላስ ፡ የለውም ።
27 በዚህ ፡ ዓለም፡ ሥራ፡ የማይሠራ፡ ሰው፡ አፈር፡ ልብሱ፡ ደንጊያ ፡ ትራሱ፡ ነው ።
28 ከርሞ ፡ ጥጃ ።
29 ወንጌል ፡ አስተማሪ ፡ በጎቹን ፡ ሊመግብ ፡ ማልዶ ፡ ይነሣል ።
30 ወንድሜ ፡ ነቀዝ ፡ የበላው ፡ እህል ፡ አትሁን ።
31 አያድሩበት ፡ ቤት ፡ አያምሻሹበት ።
32 በበጋ፡ እሞኝ፡ ቤት፡ ተንጋጋ፤ በክረምት፡ እንደ፡ ጭልፊት ፡ በየቤትህ፡ ክትት ።
33 እንካን ፡ አያውቅ ፡ እባክህን ፡ ማን ፡ ነገረው ?
34 ሾላ ፡ በድፍን ።
35 ታጥቦ ፡ ጭቃ ።
36 በቅሎ ፡ ገመዱዋን ፡ በጠሰች ፡ ቢለው ፡ በራሷ ፡ አሳጠረች ፡ አለው ።
37 ሥራ ፡ ለሠሪው ፡ እሾህ ፡ ላጣሪው ።
38 ላም ፡ ባልዋለችበት ፡ ኩበት ፡ ለቀማ ፡
39 ላም ፡ እሳት፡ ወለደች፡ እንዳትልሰው፡ ፈጀች ፤ እንዳትተወው፡ ልጅዋ፡ ሆነባት።
40 ካገሩ ፡ የወጣ ፡ አገሩ ፡ እስኪመለስ ፡ ቢጭኑት ፡ አህያ ፡ ቢለጉሙት ፡ ፈረስ ።
41 የሆድ ፡ ምቀኛው ፡ አፍ ፡ ነው ።
42 በልብ ፡ አምኖ ፡ በአፍ ፡ መንኖ ፤
43 የምኖርበት ፡ ሜዳ ፡ የምወጣበት ፡ ቀዳዳ ፡ የለም ።

44 መቼ ፡ መጣሽ ፡ ሙሽራ ? መቼ ፡ ቆረጠምሽ ፡ ሽንብራ ?
45 በሠም የተጣበቀ ፡ ጥርስ ፡ ቢሥቁበት ፡ አያደምቅ ፤ ቢበሉበት ፡ አያደቅ ።
46 የባለቤት ፡ ሰነፍ ፡ ቤቱን ፡ ያዋርዳል ።
47 የፊት ፡ ወዳጅህን ፡ በምን ፡ ቀበርኸው ? በሻሽ ፡ የኋላው ፡ እንዳይሸሽ ።
48 ለተሾመ ፡ ይሚገቱለታል ፡ በተሻረ ፡ ይመሰክሩበታል ።
49 ዕውር ፡ ሲቀናጣ ፡ ዘንጉን ፡ ወርውሮ ፡ ፍለጋ ፡ ይገባል ።
50 የገደለ ፡ ባልሽ ፡ የሞተ ፡ ወንድምሽ ፡ አዘንሽ ፡ ቅጥ ፡ አጣ ፡ ከቤትሽ፡ አልወጣ።
51 እየቈራረጣችሁ ፡ አንበሳው ፡ ሄደ ፤ ነምሩም ፡ ሞተላችሁ ።
52 በቅሎ ፡ ግዙ ፡ ግዙ ፡ አንድ ፡ ጨው ፡ ላያግዙ ።
53 ቀኑ ፡ እስኪያልፍ ፡ ያባትህ ፡ ባሪያ ፡ ይግዛህ ።
54 ካልታረደ ፡ አይታይ ፡ ስባቱ ፤ ካልተናገረ ፡ አይታይ ፡ ብልኀቱ ።
55 ብርሌ ፡ ከነቃ ፡ አይሆንም ፡ ዕቃ ።
56 ቧልትና ፡ ቅዘን ፡ ቤትን ፡ ያጠፋል ።
57 ውል ፡ ያውላል ፤ ታንኳ ፡ ያሻግራል ፡
58 የነቶሎቶሎ ፡ ቤት ፡ ግድግዳው ፡ ሰንበሌጥ ።
59 ሰኔ ፡ መቃጠሪያ ፡ ኅዳር ፡ መገናኛ ።
60 የነሐሴ ፡ ውኃ ፡ ጥሩ ፡ ነው ፡ የሚጠጣው ፡ የለም ፡ የድኃ ፡ ነገር ፡ ፍሬ ፡ ነው ፡ የሚሰማው ፡ የለም ።
61 እንግዳ ፡ ፊት ፡ ወርቅ ፡ ኋላ ፡ ብር፡ ኋላ ፡ ብረት ፡
62 ያህያ ፡ ሥጋ ፡ አልጋ ፡ ሲሉት ፡ አመድ ፡
63 ድኃ ፡ አየሁ ፡ ዐይኔን ፡ አመመኝ ።
64 የማይተማመን ፡ ባልንጀራ ፡ በእየወንዙ ፡ ይማማላል ።
65 ሞት ፡ ላይቀር ፡ ፍርሀት ፤ ዐመል ፡ ላይቀር ፡ ቅጣት ፡
66 ጉልቻ ፡ የላቀኝ አመድ ፡ ያጠለቀኝ ፡ አለዐማኑኤል ፡ ማን ፡ ጠየቀኝ ?
67 ጨኸት ፡ ለቁራ ፡ መብል ፡ ላሞራ ፡
68 ባመጣሽው ፡ ዳኛ ፡ ትሆን ፡ አሳረኛ ።
69 ዳገት ፡ እርሙ ፡ ሚዳ ፡ ወንድሙ ፡
70 አፍ ፡ ሲያርፍ ፡ ወዳጅን ፡ ያማል ።
71 ዐባይ ፡ አንተ ፡ አየሽኝ ፡ ከደረት ፤ እኔም ፡ አየሁህ ፡ ከጉልበት ።
72 የአቡነ ፡ ዘበሰማያት ፡ ጦር ፡ ሲወረወር ፡ እንጂ ፤ ሲወጋ ፡ አይታይም ።
73 አንተም ፡ ሌባ ፡ እኔም ፡ ሌባ ፤ ምን ፡ ያጣላናል ፡ በሰው ፡ ገለባ ።
74 እብድ ፡ ቢጨምት ፡ እስከ ፡ እኩለ ፡ ቀን ።
75 አይቡ ፡ ዳኛ ፡ ቅቤው ፡ መልከኛ ።
76 አይቡን ፡ሲያዩት ፡ አጓቱን ፡ ጠገቡት ።
77 አፍንጫን ፡ ቢመቱት ፡ ዐይን ፡ ያለቅሳል ።
78 እርሷ ፡ ሰንፋ ፡ ራቷን ፡ ገንፎ ፡ አድርጋ ፡ ቢያጎርሷት ፡ ተኮሳት ።

79 ላይኛው ፡ ከንፈር ፡ ለከርከር ፤ ታችኛው ፡ ከንፈር ፡ ለምስክር ።
80 የዝኆን ፡ ክሳትና ፡ የባለጺጋ ፡ ክሳት ፡ አይታወቅም ።
81 ከመንታ ፡ የተንጠለጠለች ፡ ወፍ ፡ ሁለት ፡ ክንፉን ፡ ትነደፍ ።
82 አለ ፡ በለኝ ፡ ቀለቢን ፡ ሞተ ፡ በለኝ ፡ ከፈኔን ።
83 ኮሶ ፡ ሲጠጣ ፡ ስቅጠጥ ፤ ወተት ፡ ሲጠጣ ፡ ሽምጥጥ ።
84 ፈረሰኛ ፡ የወሰደውን ፡ እግረኛ ፡ አይመልሰውም ።
85 ጌታዋን ፡ የምታምን ፡ ውሻ ፡ ፍሪዳ ፡ ሲታረድ ፡ ወንዝ ፡ ወረደች ።
86 ከወገብ ፡ በላይ ፡ ታቦት ፡ ከወገብ ፡ በታች ፡ ጣዖት ።
87 የዋጋ ፡ ብልጥ ፡ ልብ ፡ ይመልጥ ።
88 ያመጣሁት ፡ ውሻ ፡ ነከሰኝ ፤ ያነደድሁት ፡ እሳት ፡ ጠበሰኝ ።
89 እብድ ፡ የያዘው ፡ መልክ ፡ አይበረክትም ።
90 ከአጋም ፡ የተጠጋ ፡ ቍልቋል ፡ ዘላለም ፡ ሲያለቅስ ፡ ይኖራል ።
91 ባንድ ፡ ዙፋን ፡ ሁለት ፡ ንጉሥ ፤ ባንድ ፡ አፍ ፡ ሁለት ፡ ምላስ ፡ የለም ።
92 ዝም ፡ ባለ ፡ አፍ ፡ ዝንብ ፡ አይገባበትም ።
93 ከፊት ፡ ከወጣ ፡ ገሮ ፡ በኋላ ፡ የበቀለ ፡ ቀንድ ፡ በለጠው ።
94 በዕውር ፡ ይጠቃቀሷል ፡ በደንቈሮ ፡ ይንሾኳሾኳል ።
95 የተቸገረ ፡ ዱቄት ፡ ከነፋስ፡ይጠጋል ።
96 ሄዳ ፡ ጉበት ፡ ይነሡአታል ፤ ታናሽ ፡ ታላቅ ፡ ስደዱልኝ ፡ አለች ።
97 የክፉ ፡ ልጅ ፡ እናት ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ ታዝናለች ።
98 ዐይን ፡ ካላዩበት ፡ ግንባር ፡ ነው ።
99 ሆድን ፡ በጎመን ፡ ቢደልሉት ፡ ጉልበት ፡ በዳገት ፡ ይለግማል ።
100 ተጎንብሶ ፡ የሚበላን ፡ ተኝተህ ፡ ቀላውጠው ።
101 ጉንፋን፡ የታመመ ፡ ውሻና፡ ልጅንና፡ ፍየልን ፡ ይዞ፡ የተደበቀ ፡ አይሰወሩም።
102 ይሆናል ፡ ብዬ ፡ ጎሽ ፡ ጠመድሁ ፤ የማይሆንልኝ ፡ ቢሆን ፡ ፈትቼ ፡ ሰደድሁ።
103 በገዛ ፡ ራሱ ፡ እባብ ፡ ጠመጠመ ።
104 የተነቃነቀ ፡ ጥርስ ፡ ሳይወልቅ ፡ አያርፍም ።
105 ዥርባዬን አሳከከኝ ፤ ተንጠራርቼ ፡ ማከክ ፡ ተሳነኝ ።
106 ሰዶ ፡ ከማሳደድ ፡ የያዙትን ፡ ማጥበቅ ፡
107 አጥብቆ ፡ ጠያቂ ፡ የናቱን ፡ ሞት ፡ ይረዳል ።
108 ዳቦ ፡ ሲያይ ፡ ልብ-ልቡን ፡ ዳገት ፡ ሲያይ ፡ ጥግ-ጥጉን ።
109 ለቀሊል ፡ ሰው ፡ ምሥጢር ፡ መንገር ፡ በቀዳዳ ፡ አቁማዳ ፡ ጤፍ፡ መቋጠር ።
110 አይቶ ፡ አጣ ፡ ቤት ፡ ጎመን ፡ የተቀቀለ ፡ ዕለት ፡ ሲጨበጨብና ፡ ሲጨፈር ፡ ይታደራል ።

111 ያይንን፡ ጨንቃራ፡ ሰው፡ ያየዋል፤ የልብን፡ ጨንቃራ፡ እግዚአብሔር፡ ያየዋል።
112 ፈረንጆች ፡ እንደ ፡ መርፌ ፡ ፈትል ፡ ይገቡ ፡ እንደ ፡ ወርካ ፡ ይሰፉ ።

113 የፋቂ ፡ ሰነፍ ፡ አንዱን ፡ ሳይፍቅ ፡ አንዱን ፡ ይወዝፍ ።

114 እህል ፡ ሲጠፋ ፡ ወፍጮ ፡ ይሰላል ፡ እህል ፡ ሲገኝ ፡ ወፍጮ ፡ ይደንዛል ።

115 የነምር ፡ ዐይን ፡ ከፍየል ፡ የፍየል ፡ ዐይን ፡ ከቅጠል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ፡ ምጸት ፡ ንግግር ።

ምጸት ፡ ንግግር ፡ የሚባለው ፡ የተቃራኒን ፡ ወይም ፡ የማሾፍን ፡ ሁኔታ ፡ የሚ ገልጽ ፡ ንግግር ፡ ነው ። ያለመልክ ፡ መልክ ፡ ያለሥራ ፡ ሥራ ፡ ያለዐቅም ፡ ዐቅምና ፡ ያለባሕርይ ፡ ባሕርይ ፡ እየሰጡ ፡ የሚሸረድዱበት ፡ አነጋገር ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

፩ መስፍን ፡ የገዛት ፡ በቅሎ ፡ ስትሠግር ፡ ለትንግርት ፡ ትታያለች ።

በምጸት ፡ ረገድ ፡ መስፍን ፡ የገዛት ፡ በቅሎ ፡ መጋዣ ፡ መሆኗን ፡ የሚያመለክት፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ነው ።

2 ወይዘሮ ፡ ዓይን ፡ ዓለምን ፡ የመሰለች ፡ ቆንጆ ፡ በመንደራችን ፡ አትገኝም ።

በሁለተኛው ፡ ቍጥር ፡ የተነገረው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ወይዘሮ ፡ ዓይን ፡ ዓለም ፡ ጥፉ ፡ መልክ ፡ እንዳላት ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

3 ወርቅ ፡ ዓለማየሁ ፡ የጀግኖች ፡ ጀግና ፡ ከመሆኑ ፡ የተነሣ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ያነሣሡታል ።

4 አዬ ! አዬ ፡ ደግ ! አዬ ፡ ርኅሩኅ ! አሁን ፡ እርሱ ፡ ይሙት !

5 አንተን ፡ የመሰለ ፡ ጀግና ! የረገጥኸው ፡ ድንጋይ ፡ ሲፈነቀል ፡ ማን ፡ ዝን ብህን ፡ እሽ ፡ ይላታል ?

6 ፈለቀ ፡ ይህን ፡ ሥራ ፡ እንዲሠራ ፡ ዐቅሙ ፡ አይፈቅድለትም ።

7 እርሱ ፡ እንዳንተ ፡ ጎኑ ፡ ወይም ፡ ደረቱ፡ ሰፊ ፡ አይደለም ።

8 እርሷ ፡ እኮ ፡ ዘፈን ፡ አታውቅም ፤ እውን ፡ አየለች ፡ እውነት ፡ አይደለም ?

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ፡ ምሳሌያዊ ፡ ንግግር ።

ምሳሌያዊ ፡ ንግግር ፡

ነገርን ፡ (ምሥጢርን) ፡ አጕልቶ ፡ ወይም ፡ አራቆ ፡ የሚያስረዳ ፡ አ . ነገር ፡ ነው።

ለጊዜው ፡ ለምሳሌ ፡ እንዲሆኑ ፡ የተጻፉት ፡ የሚከተሉት፡ ናቸው ።

### ያማርኛ ፡ ግጥሞች ፡

ያማርኛ፡ ግጥሞች ፡ ሐረጎች ፡ በየስልታቸው፡ በስንኝ ፡ እየተከፋፈሉ፡ ዜማ፡ እንደ ማይሰብሩ ፡ ሆነው ፡ ቤት ፡ እየመቱ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ምሳሌያውያን ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ የሚደርሱ ፡ ናቸው ። ቅኔዎች ፡ እንደ ፡ ስድ ፡ ንባብ ፡ አሳብን፡ አቃንተው ፡ እየገለጹ ፡ ደስ ታን፡ ሐዘንን፡ ምስጋናንና ፡ ነቀፌታን ፡ በትክክል፡ ያስረዳሉ ። ግጥሞች ፡ ከስድ ፡ ንባብ፡

ይልቅ ፡ ባጭሩ ፡ ብዙ፡ ምሥጢር፡ ያለበትን ፡ ነገር፡ አጣፍጠው ፡ ስለሚያጎርሱ ፡ በጣም፡ የተወደዱ ፡ ናቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ስድ ፡ ንባብ ፡ በቀላሉ ፡ ስለማያደርሱ ፡ እንደ ፡ መወደዳቸው ፡ መጠን ፡ አይሠራባቸውም ።

ብዙ ፡ የግጥሞች ፡ ዐይነቶች ፡ አሉ ፡ ይሁን ፡ እንጂ ፡ አብዛኛውን ፡ የሚሠራባቸው፡ የሚከተሉት ፡ ናቸው ።

(ሀ) ኅብር ፡ ቅኔ ፡ ወይም ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡- በውስጡ ፡ ወርቁንም ፡ ሠሙንም ፡ የሚያስ ተባብር ፡ ቃል ፡ ወይም ፡ ሐረግ ፡ ያለበት ፡ ግጥም ፡ ወይም ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ነው ። ኅብር ፡ የሚባለው ፡ ቃል ፡ የመጣው ፡ ኀብረ ፡ ከሚባለው ፡ ግሥ ፡ ነው ፤ ትርጓሜውም፡ ካንድ ፡ ነገር ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ የሆነ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ማንኛውም ፡ ኅብር ፡ ቅኔ ፡ ደስታንና ፡ ምስጋናን ፡ ከሚገልጸው ፡ በቀር ፡ « ውስጠ፡ ወይራ» ፡ ይሆናል ፤ ውስጠ ፡ ወይራም ፡ የተባለበት ፡ ምክንያት ፡ በግልጽ ፡ ሊነገር ፡ ያል ተፈለገውን ፡ ነገር ፡ በምሥጢራዊ ፡ ኀይለ ፡ ቃሉ ፡ ስለሚያስረዳ ፡ ነው ።

ኅብር ፡ ንግግር ፡

1 እባክህ ፡ ወንድሜ ፡ በጥላት ፡ አትለውሳት ።
2 መከራችንን ፡ ስንዝቅ ፡ ማንም ፡ አልረዳንም ።
3 ልጅቱ ፡ እንዳቺ ፡ በቆላ ፡ ስላደገች ፡ ደጋን ፡ አታውቅም ።
4 በቤታችን ፡ አጠገብ ፡ ያለችው ፡ ጽጌ ፡ ባልታሰበ ፡ ሰዓት ፡ አበበች ።

(ለ) ሠም ፡ ለበስ ፡ ቅኔ ፡ ወይም ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ የሚባለው ፡ ተፈላጊውን ፡ ነገር ፡ በግ ልጽ ፡ ሳያስረዳ ፡ ፍሬ ፡ ነገሩን ፡ በምሳሌው ፡ በትርጓሜ ፡ የሚያመጣ ፡ ግጥም ፡ ወይም ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ነው ።

ሠም ፡ ለበስ ፡ ግጥም ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ የተደረሰበት ፡ ምክንያት ፡ ካልታ ወቀ ፡ ምሥጢሩ ፡ በቀላሉ ፡ አይገኝም ፤ በዚህ ፡ ውስጥ ፡ ከባድ ፡ ኀይለ ፡ ቃል ፡ የተገኘ በት ፡ ግጥም ፡ ወይም ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጠ ፡ ወይራ ፡ ይባላል ።

ሠም ፡ ለበስ ፡ ውስጠ ፡ ወይራ ፡

ወጣት ፡ አዝመራችን ፡ ተገማሽሮ ፡ ሲሸት ፡
አዕዋፈ ፡ ሰማይ ፡ በቁም ፡ ጠረጠሩት ፡
ተነሡ ፡ እባካችሁ ፡ እናብጅ፡ ወንጭፍን ፡
እንድናበርርበት ፡ የሰማይ ፡ ወፎችን ።
ከአዕዋፎቹም ፡ በጣም ፡ የሚጎዱት ፡
ነጫጮቹ ፡ ናቸው ፡ ርግብ ፡ የሚመስሉት ።

ሠም ፡ ለበስ ፡ ንግግር ፡

1 ከዚህ ፡ ማሳ ፡ ላይ ፡ ኮሽሽላው ፡ በጥንቃቄ ፡ ተለቃቅሞ ፡ ከነርዝራዡ ፡ ካል ጠፋ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ መልካም ፡ ዘርን ፡ ቢዘሩበት ፡ ጥሩ ፡ እህልን ፡ አይሰጥም ።

2 ለዚህ ፡ መድኀኒቱ ፡ እንደ ፡ ውጋት ፡ እየነጠቁ ፡ መጣል ፡ ነው ።

3 እባክህን ፡ የኔ ፡ ወንድም ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ቀኝ ፡ እጅህን ፡ አውሰኝ ።

(ሐ)ሠምና፡ ወርቅ፡ ቅኔ፡- ፍሬ ፡ ነገሩን ፡ ወይም ፡ ወርቁን ፡ ሳይሰውር ፡ በምሳሌ ፡ የሚ ያስረዳ ፡ ግጥም ፡ ወይም ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ነው ፤ ሠምም ፡ የሚባለው ፡ ፍሬ ፡ ነገር ፡ የተ መሰለበት ፡ ነገር ፡ ነው ። ሠም ፡ ቀላጭ ፡ ወርቅ ፡ ነጣሪ ፡ ናቸው ።

ሠምና ፡ ወርቅ ፡ ንግግር ፡

በእርሻ ፡ ልባችን ፡ እውነት ፡ ዘርን ፡ እንዝራበት ።

አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ በልባቸው ፡ ጽላት ፡ ማመዛዘንን ፡ ጽፈው ፡ ያጠናሉ ።

እናታችን ፡ ኢትዮጵያ ፡ ዐይነ ፡ ሥውር ፡ ሆና ፡ ስትኖር ፡ ሐኪሙ ፡ ጠቅል፡ የጋረ ዳትን ፡ የድንቁርና ፡ ሰንኮፍ ፡ ገፎ ፡ ዐይኗን ፡ አበራላት ።

በመጽሐፈ ፡ መስተዋት ፡ ብዙ ፡ ጒድለት ፡ እንዳለብን ፡ እናያለን ፤ ስለዚህ፡ ጒድ ለታችንን ፡ ለማረም ፡ ዕድል ፡ የሚሰጠንን ፡ መጽሐፈ ፡ መስተዋት ፡ ዘወትር ፡ እን መልከትበት ።

(መ) ፡ አንጻር ፡ ቅኔ ፡ ወይም ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡- በማመሳሰል ፡ ወይም ፡ በማወዳደር ፡ ምሥጢርን ፡ እያጎላ ፡ የሚገልጽ ፡ ግጥም ፡ ወይም ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ነው ።

አንጻር ፡ ንግግር ፡

1 አርበኞቻችን ፡ እንደ ፡ ጎፈሪያም ፡ አንበሳ ፡ እየጎደሩ ፡ ጫካ ፡ ጫካውን ፡ ባያ ነጠንጡ ፡ ኖሮ ፡ ተውጠን ፡ እንቀር ፡ ነበር ።

2 እንደ፡ ቅዱሳን ፡ ሐዋርያት ፡ የዓለም ፡ ብርሃን ፡ መሆን ፡ ራስን ፡ ክዶ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ የዚህን ፡ ዓለም ፡ ጥቅም ፡ እፍታ ፡ በመፈለግ ፡ አይደለም ።

3 እንደ ፡ ወሪራ ፡ ላም ፡ አደር ፡ ላደር ፡ ካላራወጡት ፡ ለጥ ፡ ሰጥ ፡ አይልም ።

4 አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ በምን ፡ ምክንያት ፡ እንደ፡ ሆነ ፡ አላውቅም ፡ እንደ ፡ ባዶ፡ ቅል ፡ ይጮሃሉ ።

(ሠ( ተሰብአት፡-ሕይወት ፡ የሌላቸው ፡ ነገሮች ፡ በሰው ፡ ደረጃ ፡ ገብተው፡ እንደሚሠሩ፡ አስመስሎ ፡ የሚያሳይ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ነው ።

1 ትምህርትን ፡ በማይፈልግ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ድንቁርና ፡ ቤቱን ፡ ይሠራበታል ።

2 የድንቁርና ፡ ባሕር ፡ ብዙ ፡ ሕዝቦቹን ፡ አስምጧል ።

3 ክረምት ፡ ተራሮች ፡ ሜዶች ፡ ሸንተረሮችና ፡ ሸለቆች ፡ ልጆቹን ፡ በያመቱ ፡ ሁለት ፡ ወይም ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ያለብሳቸዋል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በጋ ፡ የተባለ ፡ ሽፍታ ፡ ይገ ፋቸዋል ። ይሁን ፡ እንጂ ፤ ክረምት ፡ ተመርሮ ፡ ከማልበስ ፡ አያቋርጥም ።

4 አዝርዕት ፡ ዛሬ ፡ ጧት ፡ እጅ ፡ ለእጅ ፡ ተያይዘው ፡ ሲላቀሱ ፡ ዕፀዋት ፡ ዳንስ፡ ይረግጡ ፡ ነበር ።

5 እንቅልፍ ያለግርብረት ፡ የሚጠፍር ፡ ዳኛ ፡ ነው ።

6 አቶ ፡ ደመና ፡ ሰማይ ፡ እርሻውን ፡ በመብረቅ ፡ ያርሳል ።

# ፩ኛ ፡ ክፍል ፡ ያሳብ ፡ መግለጫዎች ፡

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ፡ አንቀጽ ።

አንድ ፡ አርእስት ፡ መርጠን ፡ ድርሰት ፡ ስንጽፍ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ አነስተኛ ፡ ክፍል፡ እንከፍለዋለን ። ያንድ ፡ ድርሰት ፡ አነስተኛው ፡ ክፍልም ፡ አንቀጽ ፡ ተብሎ ፡ ይጠራል ። አንቀጽ ፡ አንድ ፡ አሳብን ፡ ሲገልጽ ፡ እንደሚገባው ፡ መጠን ፡ አድርጎ ፡ ያስረዳል ። የአንቀጽ ፡ አጻጻፍ ፡ ልክ ፡ እንደ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ተገላጩን ፡ ነገር ፡ አስፋፍቶ ፡ ስለሚያስረዳ ፡ ጥቂት ፡ ከአረፍተ ፡ ነገር ፡ ይለያል ። እንግዲህ ፡ ይህ ፡ የድርሰት ፡ አነስተኛ ፡ ክፍል ፡ አንቀጽ ፡ ብለን ፡ የሰየምነው ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች፡ በስምምነት፡ ሆነው ፡ አንድ ፡ አሳብ ፡ የሚሰጡበት ፡ ክፍል ፡ ነው ።

ላንቀጽ ፡ የቃላትን ፡ ስንኝ ፡ (አሰካክ)ወይም ውበት) ፡ አድምቀው ፡ ላንባቢው ፡ እንደሚያጠግብ ፡ አድርገው ፡ የሚያጎርሱ ፡ የሚከተሉት ፡ ናቸው ።

(ሀ) ያሳብ ፡ ስምምነት ፡

(ለ) የቃላት ፡ አሰካክ ፡

(ሐ) የኀይለ ፡ ቃል ፡ አገላለጽ ፡

(መ) የአረፍተ ፡ ነገር ፡ አዠማመር ፡

### (ሀ) ያሳብ ፡ ስምምነት ፡

የተሰጠው ፡ አርእስት ፡ ተስፋፍቶ፡ መገለጽ ፡ ወይም፡ በተስማሚ ፡ ምሳሌ ፡ ጎልቶ ፡ መሰጠት ፡ ስላለበት ፡ እያንዳንዱ ፡ አንቀጽ ፡ የአርእስቱ ፡ ገላጭ ፡ መሆን ፡ አለበት ። እያንዳንዱ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ በተነገረበት ፡ ክፍል ፡ ላንቀጹ ፡ ማውራት ፡ አለበት ፡ እንጂ ፡ አንቀጹን ፡ ለቆ ፡ መዘላበድ ፡ የለበትም ። ያንድ ፡ አንቀጽ ፡ ስምምነት ፡ ጥሩ ፡ ሆኖ ፡ መደራጀቱ ፡ የሚታወቀው ፡ አንቀጹ ፡ እንደ ፡ ወይን፡ ዘለላ ፡ ተጨምቆ ፡ አንድ ፡ አረፍተ፡ ነገርን ፡ ለመሆን ፡ የቻለ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ነው ።

### አስረጅ ፡ ያልተያያዘ ፡ አሳብ ፡

1 አስተማሪያችን ፡ ከብስክሌት ፡ ላይ ፡ ወደቀ ።

ዓምና ፡ ካይሮንና ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ጐብኝቶ ፡ ነበር ፡

<u>ትክክለኛ ፡ አሳብ</u> ፡- ዓምና ፡ ካይሮንና ፡ ኢየሩሳይምን ፡ የጐበኘው ፡ አስተማሪያችን ፡ ከብስክሌት ፡ ላይ ፡ ወደቀ ።

2 <u>ያልተያያዘ ፡ አሳብ ፡</u>

የባሕር ፡ ዛፍ ፡ ቅጠልና ፡ እንጨት ፡ ለማገዶና ፡ ለቤት ፡ መሥሪያ ፡ ይጠቅማል፤ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ የሚበቅለው ፡ በወይና ፡ ደጋና ፡ በደጋ ፡ አገር ፡ ነው ።

<u>ትክክለኛ ፡ አሳብ ፡</u>

የባሕር ፡ ዛፍ ፡ ቅጠልና ፡ እንጨት ፡ ለቤት ፡ መሥሪያና፡ ለማገዶ፡ ስለሚጠቅም ፡ ባገራችን ፡ አብዛኛውን፡ ጊዜ፡ የሚተከለው ፡ በወይና ፡ ደጋና ፡ በደጋ ፡ ነው ።

(ለ) የቃላት ፡ አሰካክ ፡

አንድ ፡ ድርሰትን ፡ እየካብን ፡ በምናሳድግበት ፡ ጊዜ ፡ አያያዞችንና ፡ ንኡስ ፡ ሐረጎችን ፡ እንዳስፈላጊነታቸው ፡ መጠን ፡ በአረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ እናስገባቸዋለን ። ልዩ ፡ ልዩ ፡ ቃላት ፡ በአረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ሲገቡ ፡ በቅደም ፡ ተከተልነት ፡ ካልጻፍናቸው ፡ ድርሰታችን ፡ ላንባቢ ፡ በቀላል ፡ ግልጽ ፡ ሊሆንለት ፡ አይችልም። ስለዚህ ፡ አንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ወይም ፡ ቃል ፡ ከፊተኛውና ፡ ከመጪው ፡ መተባበር ፡ አለበት ።

አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ያሳብ ፡ መቀራረብ ፡ ያንቀጹን ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ መተባበር፡ ያስገኛል ። የቃላት፡ አሰካክን ፡ ሕግ ፡ ለመከተል ፡ አስቀድሞ፡ ለተነገረው ፡ አሳብ፡ ተስማሚ ፡ ወይም ፡ ተቃዋሚ ፡ በሚሆኑት ፡ መስተፃምራን ፡ መሥራት ፡ ያስፈልጋል ።

አስረጅ ፡- ያልተካከለ ፡

ልብስ ፡ አጣቢው ፡ ጥሩ ፡ አድርጎ፡ አጥቦ ፡ ተኩሰልኝ ፡ ልብሴን ፡ ትናንትና ።

ትክክለኛ ፡

ትናንትና ፡ ልብስ ፡ አጣቢው ፡ ልብሴን ፡ ጥሩ ፡ አድርጎ ፡ አጥቦ ፡ ተኮሰልኝ ።

ያልተደራጀ ፡- ወይፈኑን ፡ ሲገርፍ ፡ እያጣደፈ ፡ አቶ ፡ ፈለቀን ፡ አየሁት ።

ትክክለኛ ፡- አቶ ፡ ፈለቀ ፡ እያጣደፈ ፡ ወይፈኑን ፡ ሲገርፍ ፡ አየሁት ።

(ሐ) የኀይለ ፡ ቃል ፡ አገላለጽ ፡

ቃላት ፡ በደንብ ፡ ተሰካክተው ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ያለብዙ ፡ ድካም ፡ ምን ፡ ማለቱ ፡ ነው፡ ሳይል፡ የሌላውን፡ ሰው፡ አሳብ ፡ በቀላል፡ እንዲያገኝበት፡ ጥገኛው፡ አሳብ፡ ከመደበኛው ፡ አሳብ ፡ ሥር ፡ ተጠግቶ ፡ ይጻፋል ። በማናቸውም ፡ አኳኋን ፡ ቢሆን ፡ የአንቀጹ ፡ የመጀመሪያው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ አርእስቱን ፡ ይይዛል ። የኀይለ ፡ ቃል፡ አገላለጽ ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ የሚገኘው ፡ በማመሳሰል ፡ ወይም ፡ የቃላትን ፡ ስፍራ ፡ በማዘዋወር ፡ ወይም ፡ ቃላትን ፡ እንደ ፡ ደረጃቸው ፡ በማሳካት ፡ ነው ። ዋናውን ፡ አሳብ ፡ ጥገኛ ፡ ጥገኛውን ፡ አሳብ ፡ ዋና ፡ ማድረግና ፡ አስፈላጊ ፡ ያልሆኑትን ፡ ቃላት ፡ በአረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ማስገባት ፡ የጽሑፉን ፡ አሳብ ፡ ያበላሻል ።

ስለዚህ ፡ የኀይለ ፡ ቃል ፡ አገላለጽ ፡ ተግባር ፡ ያንድ ፡ ጽሑፍ ፡ አሳብ ፡ ጎልቶ ፡ የሚታይበትን ፡ ዘዴ ፡ ማመልከት ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

1 በማነጻጸር ፡ ተፈላጊውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ መግለጽ ፡

(ሀ) የፈለቀ፡ ውሸት ፡ እንደ ፡ መጫኛ ፡ ቆሞ ፡ ሲሄድ ፡ የወርቅ ፡ አለማሁ ፡ ይድሃል ።

(ሀ) እንደ ፡ ውኃ ፡ ሙላት ፡ ፈረሰኛ ፡ እያጋፈተ ፡ ያስፈራራናል ።

2 በምሳሌ ፡ መግለጽ ፡

(ሀ) ብልጽግና ፡ ካባን ፡ በከፍተኛ ፡ ዋጋ ፡ እንደ፡ መግዛት ፡ ድኅነት ፡ መጎና ጸፊያን ፡ በቀላሉ ፡ ያስባል ።

3 በአረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ሊነገር ፡ የተፈለገውን ፡ የአረፍተ ፡ ነገር ፡ መግ ለጫ ፡ በመዠመሪያ ፡ መጻፍ ፡

(ሀ) ከባሕር ፡ ውስጥ ፡ ወንድሙን ፡ አወጣው ።

(ለ) ከትቢያ ፡ ተነሥቶ ፡ እዚህ ፡ በመድረሱ ፡ አቶ ፡ ማንደፍሮ ፡ እንግዲ ፡ ፈጣሪውን ፡ አመሰገነ ።

(ሐ) ከፋት ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ተመችቶት ፡ ይኖራል ፤ ቅንነት ፡ ግን ፡ ከመ ደኅየቱ ፡ የተነሣ ፡ መሰደዱ ፡ ነው ።

(መ) እንደ ፡ ዝንብ ፡ በትልቅ ፡ ሰው ፡ ፊት ፡ ውርውር ፡ በማለቱ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ አዝነውበታል ።

4 ፈላጊ ፡- ቃላትን ፡ እንደ ፡ ደረጃቸው ፡ ማንሣት ፡ ነው ።

(ሀ) መንግሥቱ ፡ ሰነፍ ፡ ደደብና ፡ ጋግርታም ፡ ነው ።

(ለ) ሰውዬው ፡ ተናጋሪ ፡ ደፋር ፡ ቀጥርጠኛና ፡ ጨካኝ ፡ ነው ።

5 በድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ዋናውን ፡ አሳብ፡ በመደበኛው ፡ ውስጥ፡ ማድረግ ፡

ስሕተት ፡ ተክለ ፡ ጻድቅ ፡ እንደ ፡ ሴት ፡ ወይዘሮ ፡ ስለሚሽኮረመም ፡ መንግ ሥቱ ፡ አንዷን ፡ እንጀራ ፡ አንድ ፡ ጉርሻ ፡ አደረጋት ።

ትክክል ፡- ተክለ ፡ ጻድቅ ፡ መንግሥቱ ፡ አንዷን ፡ እንጀራ ፡ አንድ ፡ ጉርሻ ፡ ሲያ ደርጋት ፡ እያየ ፡ እንደ ፡ ሴት ፡ ወይዘሮ ፡ ይሽኮረመማል ።

6 ካንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ስሜቱ ፡ ሳይለወጥ ፡ የማያስፈልጉትን ፡ ቃላት ፡ ማውጣት ፡

(ሀ) መሸሻ ፡ ከባልንጀራው ፡ ሳይማከር ፡ የሚሠራው ፡ ሥራ ፡ ደስ ፡ የማያ ሰኝ ፡ መሆኑን ፡ ያውቃልና ፤ ከባልንጀራው ፡ ሳይማከር ፡ ማናቸውንም ፡ ነገር ፡ አይሠ ራም ።

መንገሻ ፡ ከባልንጀራው ፡ ሳይማከር፡ ማናቸውንም ፡ ነገር ፡ አይሠራም።

(ለ) አቶ ፡ ከበደ፡ «ገንዘብህ ፡ መካን ፡ እንዳይሆንብህና ፡ እንዳይባክንብህ፡ በወለድ ፡ አበድረው» ፡ አለኝ ።

አቶ ፡ ከበደ ፡ ገንዘብህን ፡ አራባው ፡ (አሠራው) ፡ አለኝ ።

7 ቢቻል ፡ በንኡስ ፡ ወይም ፡ በጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ፋንታ ፡ አንድ፡ ቃል፡ ማስገባት።

የወይዘሮ ፡ ወርቂት ፡ ልጅ ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ሰነፍ ፡ የሆነ ፡ ልጅ ፡ ነው ።

የወይዘሮ ፡ ወርቂት ፡ ልጅ ፡ አሞት ፡ ቢስ ፡ (አሞት ፡ የለሽ) ፡ ነው ።

(መ) የአረፍተ ፡ ነገር፡ አዠማመር ፡

አንድ ፡ አሳብን ፡ እየገለጽን ፡ ስናስረዳ፡ የአረፍተ ፡ ነገሮቹ ፡ ርዝመትና ፡ እጥረት፡ አንድ ፡ ዐይነት ፡ እንዳይሆን ፡ መጠንቀቅ ፡ አለብን ። አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ዘወትር ፡ ባንድ፡ ዐይነት ፡ አካሄድ ፡ እንዳይዠምሩ ፡ ማሰብ ፡ አለብን ። የዚህም ፡ ጥቅሙ ፡ ዐይን ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ነገሮችን ፡ በማየት ፡ እንደሚደሰት ፡ ሁሉ ፡ አንጎልም ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ አሳቡ ፡ አንድ ፡ ቢሆን ፡ ሽልምልምና ፡ ጌጠኛ ፡ አሠራርን ፡ በመጎምዠት ፡ እንዲቀበል ፡ ለማድረግ ፡ ነው ።

አስረጅ ፡

1 ዓለማየሁ፡ ያቶ ፡ ሽዋን፡ ግዛው ፡ ልጅ፡ ሥራውን፡ በትክክል፡ ፈጽሞ ፡ ከሁሉ ፡ በፊት ፡ ስላስረከበ ፡ ሥራ ፡ አስኪያጁ፡ አመስግነው፡ በማስታወሻ ፡ መዝገባቸው፡ ጻፉት፡

2 ጢት ፡ ማታ ፡ መፋጀት ፡ ቤተ ፡ ሰብን ፡ ጤና ፡ ከመንሣቱ ፡ በላይ ፡ ጎረቤትን፡ ያውካል ።

3 በእንግሊዝና ፡ በአሜሪካ ፡ አገር ፡ ወይዘሮ ፡ ጥበቧ ፡ ቤተኛ ፡ ሆናለች ፤ በኢትዮጵያም፡ ማረፊያ ፡ ለማግኘት ፡ በአይሮፕላን፡ በየከተሞቻችን ፡ ማንዣበብ ፡ ዠምራለች።

4 ሁል ፡ ጊዜ ፡ መበሳጨት ፡ ከበሽታ ፡ ላይ ፡ ይጥላል ።

የአንቀጽ ፡ ማስረጃ ፡

ሙሶሊኒ፡ ባ፲፱፻፳፯ ፡ ዓመተ፡ ምሕረት ፡ «የሸዋ ፡ ሕዝብ ፡ ይህን ፡ አገር ፡ በግድ፡ አስገብሮ ፡ ሕዝቡን ፡ በግፍ ፡ ይገዛዋል ፤ የኩልነት ፡ መብት ፡ የለውም» ፡ ብሎ፡ ሐሰት፡ የመላበትን ፡ ክስ ፡ ለዓለም ፡ ማኅበር ፡ አቀረበ። ይህም ፡ ሐሰት ፡ መሆኑን ፡ የሚያስረዳ ፡ ምርኮኞች ፡ ተብለው ፡ ከሚጠሩት ፡ ውስጥ ፡ ልጆች ፡ ሆነው ፡ ደጃች ፡ ባልቻና ፡ ፊታውራሪ ፡ ሀብተ ፡ ጊዮርጊስን ፡ ንጉሥ ፡ ምኒልክ ፡ አምጥተው ፡ ካሳደጓቸው ፡ በኋላ ፡ ለታላቅ ፡ ማዕርግ ፡ ማብቃታቸው ፡ ነው ።

በዚህም ፡ ምክንያት ፡ ከዕለታት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ሁለቱ ፡ መኳንንት ፡ ጕዞ ፡ እየተጓዙ ፡ እተማረኩበት ፡ ስፍራ ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ ደጃች ፡ ባልቻ ፡ « ይኸውልዎ ፡ የተማረክንበት» ፡ ብለው ፡ ለፊታውራሪ ፡ ሀብተ ፡ ጊዮርጊስ ፡ አስታወቋቸው ። ፊታውራሪ ፡ ሀብተ ፡ ጊዮርጊስም ፡ « ይህ ፡ ስፍራስ ፡ የተባረክንበት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የተማረክንበት ፡ አይደለም » ብለው ፡ እውነተኛውን ፡ መልስ ፡ ሰጧቸው ፡ ይባላል ።

ተክለ ፡ ጻድቅ ፡ መኵሪያ ፡

ምዕራፍ፡ ፲፰ ፡ ንባብ ።

መግለጫ ፡

ንባብ ፡ በማንኛውም ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ ተጽፎ ፡ የሚገኘውን ፡ ነገር፡ ወይም ፡ አሳብ፡ ለሰው ፡ በድምፅ ፡ የምናሰማበት ፡ ወይም ፡ በዝምታ ፡ የምናነብበት ፡ ዘዴ ፡ ነው ።

(ሀ) ጮክ ፡ ብሎ ፡ ማንበብ ፡ (ድምፃዊ ፡ ንባብ) ፡

(ለ) ዝም ፡ ብሎ ፡ ማንበብ ፡ (ድምፅ ፡ አልባ ፡ ንባብ) ፡

(ሀ) ድምፅን ፡ አሰምቶ ፡ ማንበብ ፡ የሌሎችን ፡ አሳብ ፡ መናገር ፡ ነው ።

አንድ ፡ ሰው ፡ የደራሲውን ፡ አሳብ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ አነባበቡ ፡ ላዳማጮቹ ፡ ለማሰማት ፡ ይሞክራል ።

አንድ፡ አንባቢ ፡ ተዘናንቶ፡ የሚያነበውን፡ ነገር ፡ ከራሱ፡ እንደ ፡ ፈለቀ ፡ ያህል፡ እያደረገ ፡ የቃላትን ፡ ወይም ፡ የአረፍተ ፡ ነገሮችን ፡ ትርጓሜ ፡ ባነባበቡ ፡ ይገልጻል።

አንድ ፡ ሰው ፡ ድምፁን ፡ ከፍ ፡ አድርጎ ፡ እንዲያነብ ፡ የሚያስፈልጉ ፡ ስፍሮች፡ አሉ ። እነርሱም ፡ ፍርድ ፡ ቤት ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ የራዲዮ ፡ ጣቢያና ፡ የሕዝብ ፡ መኖሪያ ፡ ቤቶች ፡ ናቸው ።

ድምፅን ፡ ከፍ ፡ አድርጎ ፡ የማንበብ ፡ ጥቅም ፡ በጣም ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ነው ። ለምሳሌ ፡ እንደ ፡ ማስታወቂያ ፡ ያለ ፡ ሁሉም ፡ እንዲያውቀው ፡ አስፈላጊ ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ ያወቁ ፡ ሰዎች ፡ ላላወቁ ፡ ሰዎች ፡ ይገልጻሉ ። እንደዚሁም ፡ ማመልከቻ ፡ ሲቀርብና ፡ ፍርድ ፡ ሲሰጥ ፡ በሁለቱ ፡ ባላጋሮች ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ነገር ፡ ይነበባል ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ባልንጀራሞች ፡ ወይም ፡ ቤት ፡ ሰቦች ፡ ከመካከላቸው ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ እንዲያነብላቸው ፡ የሚፈልጉበት ፡ ጊዜ ፡ አለ ። ይልቁንም ፡ አንድ ፡ የታመመ ፡ ሰው ፡ የሰው ፡ ናፍቆት ፡ ስለሚያድርበት ፡ የሚያጽናና ፡ ነገር ፡ እየፈለጉ ፡ ቢያነቡለት ፡ ስለሚወድ ፡ በዚህ ፡ ረገድ ፡ በጣም ፡ ይሠራበታል ።

(ለ) ዝም ፡ ብሎ ፡ አንድ ፡ መጽሐፍን ፡ መመልከት ፡ ያንድ ፡ ደራሲን ፡ አሳብ ፡ እንደ ፡ መቅዳት፡ ያለ ፡ ነው ። እንደዚህ ፡ ያለው ፡ ዘዴ ፡ ብዙ ፡ ነገሮችን ፡ አሳውቆ ፡ አንባቢውን ፡ ወደ ፡ ተመራማሪነት ፡ ይመራዋል ። አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ ከመጻሕፍት ፡ ጋራ ፡ በመወዳጀታቸው ፡ ብዙ ፡ ጥቅምን ፡ ያገኛሉ ። ለምሳሌ ፡ እንደነኤዲሰንና ፡ እንደነአብርሃም ፡ ሊንኮልን ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ሌሊት ፡ ከቀን ፡ ቢደክም ፡ ከፍ ፡ ያለውን፡ ዕውቀት ፡ ያገኛል ።

መጻሕፍት፡ ተናግረው ፡ የማያስቀይሙና፡ ምሥጢርን፡ የማያባክኑ ፡ ታማኝ፡ ወዳጆች ፡ ናቸው። ስለዚህ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ከነርሱ ፡ ጋራ ፡ በጥብቅ ፡ የተወዳጀ ፡ እንደሆንና፡ ሙሉ ፡ መንፈሱን ፡ የሰጣቸው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አእምሮውን ፡ ይገነቡለታል ። ነገር፡ ግን፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ያሳብ ፡ ተቃዋሚ ፡ መጻሕፍት ፡ ይገኛሉና ፡ ከነርሱ ፡ በስተቀር ፡ መሆኑን ፡ ማስተዋል ፡ አለብን ።

## ነጥቦች ፡

ነጥቦች ፡ ቃላትን ፡ በየወገን ፡ በየወገናቸው ፡ እያደረግን ፡ የምንለይባቸው፡ ሙክፈያዎች ፡ ናቸው ። የነጥቦችን፡ ትርጉም ፡ ለመለየት ፡ ይቻላል። ይኸውም፡ ከፍተኛና፡ዝቅተኛ ፡ ስፍራቸውን ፡ በማጥናት ፡ ነው። ቃላትንና ፡ ቃላትን ፡ ወይም ፡ ጥገኛና ፡ ንኡስ ፡ ሐረጎችን ፡ በነጠላ፡ ሠረዝ ፡ ድርብ ፡ ድብልቅና ፡ ድርብ ፡ አረፍተ፡ ነገሮችን ፡ በድርብ ፡

ሠረዝ ፡ እንደዚሁም ፡ ባንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ መጨረሻ ፡ ላይ፡ ሙሉ ፡ ነጥብን ፡ ወይም፡ ትእምርተ ፡ ጥያቄን ፡ ወይም ፡ ትእምርተ ፡ አንክሮን ፡ ወይም ፡ ትእምርተ ፡ ሥላቅን ፡ እና ስገባለን ።

1 ክረምት ፣ ተራሮች ፡ ሜዶች ፡ ሸንተረሮችና ፡ ሸለቆች ፡ ልጆቹን ፡ ባመት ፡ ሁለት ፡ ወይም ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ያለብሳቸዋል ፤ ነገር ፡ ግን፡ በጋ፡ የተባለ ፡ ሽፍታ ፡ ይቀማቸዋል ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ ክረምት ፡ ተመርሮ ፡ ከማልበስ ፡ አያቋርጥም ።

ባንደኛው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ነጥብ ፡ ነጠላ ፡ ሠረዝ ፡ ድርብ ፡ ሠረዝና ፡ ሙሉ ፡ ነጥብ ፡ በየሥፍራቸው ፡ እንደ ፡ ገቡ ፡ አስተውል ።

2 ቀንቃኝ ፡ ነፋስ ፡ ለተቀባዮቹ ፡ ለአዝርዕትና ፡ ለዕፀዋት ፡ በጋለ ፡ መንፈስ ፡ ስለ ፡ አወረደላቸው ፡ ኅብሩ ፡ በማይታወቅ ፡ ሁናቴ ፡ ትናንትና ፡ ከሰዓት ፡ በኋላ ፡ እስክስታ ፡ ረገጡ ፡ (ወረዱ) ።

3 አንድ ፡ አርጋቸው ፡ ይህ ፡ ጠረጴዛ ፡ የተሠራው ፡ ከምንድር ፡ ነው ?

4 አቶ ፡ ወንድም ፡ አገኘሁ ፡ የበለጸገበት ፡ ዘዴ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ሥራ ፡ ፈቶ ፡ በቤት ፡ እየተጋደመ ፡ ስለሚውል ፡ ነዋ ! !

5 የልጁን ፡ ኳስ ፡ ተንጠራርቶ ፡ ሊማውረድ ፡ የሚችለው ፡ ዘኬዎስ ፡ እንጂ ፡ ሌላ፡ እኮ ፡ አይደለም !

ዘኬዎስ ፡ አጭር ፡ ልጅ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ለማውረድ ፡ የማይችል ፡ መሆኑን ፡ በማሰብ ፡ ለቀልድ ፡ የተነገረ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ነው ።

6 ጎሽ ! መልካም ፡ ሠርተሃል ።

7 ፈለቀ ፡ « ዛሬ ፡ ማታ ፡ በትምህርት ፡ ቤታችን ፡ ትያትር ፡ አለ » ፡ አለ ።

| የነጥቦች ፡ ስም ፡ | ምልክቶች ፡ |
|---|---|
| 1 ፡ ነጥብ ፡ | ፡ |
| 2 ፡ ነጠላ ፡ ሠረዝ ፡ | ፣ |
| 3 ፡ ድርብ ፡ ሠረዝ ፡ | ፤ |
| 4 ፡ ሙሉ ፡ ነጥብ ፡ | ። |
| 5 ፡ ትእምርተ ፡ ጥያቄ ፡ | ? |
| 6 ፡ ትእምርተ ፡ አንክሮ ፡ | ! |
| 7 ፡ ትእምርተ ፡ ሥላቅ ፡ | ! |
| 8 ፡ ትእምርተ ፡ ጥቅስ ፡ | « » |

እነዚህ ፡ ነጥቦች ፡ እንዴት ፡ እንደ፡ገቡ ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ በተጻፉት፡ በሰባቱ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ ተመልከት ።

ሌሎች ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ የሚሠራባቸው ፡ ምልክቶች ፡

፩ ፡ ቅንፍ ፡ ያንድ ፡ ቃልን ፡ ወይም ፡ የቃላትን ፡ ፍች ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

(ሀ) በሻሀ ፡ ውረድ ፡ ባለፈው ፡ ሳምንት ፡ በጦር ፡ ስለ ፡ ተወጋ ፡ በጠና ፡ ታሞ፡ ዛሬ ፡ ጧት ፡ ባንድ ፡ ሰዓት ፡ ሞተ ፡ ( ዐረፈ ) ።

(ለ) ወይዘሮ ፡ ይመኙሻል ፡ ልጃቸው ፡ ከፎቅ ፡ ላይ ፡ መውደቁን ፡ ስለ ፡ ሰሙ ፡ ደንግጠው ፡ በቁመናቸው ፡ ፈረጡ ፤ (ቆመው ፡ ነበሩና ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ ሳይሉ፡ ባሉበት ፡ ቦታ ፡ ላይ ፡ ወደቁ ፡ ማለት ፡ ነው ) ።

፲፱፦ ጭረት ፡ በቃላትና ፡ በቃላት ፡ መካከል ፡ ሲገባ ፡ እስከ ፡ ማለትን ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

(ሀ) ካዲስ ፡ አበባ ፡ —ሐረር ፡ በመኪና ፡ መጣሁ ።

(ለ) ካዲስ ፡ አበባ ፡ —አሥመራ ፡—ባውቶቡስ ፡ ሁለት ፡ ቀን ፡ ይፈጃል ።

፳ ፡ ንኡስ ፡ ጭረት ፡ -ቃልና ፡ ቃልን ፡ አጋጥሞ ፡ እንዳንድ ፡ ቃል ፡ የሚያናግር ፡ ነው ።

(ሀ) ሥራ-ፈት ፡ (ለ) ፡ ልብ-ወለድ ፡ (ሐ) ፡ አእምሮ-ቢስ ፡

፳፩ ፡ ይዘት ፡ -የቃል ፡ ማሳጠሪያ ፡ (የቃል ፡ መክፈያ ፡ )ነው ፡

(ሀ) ተውሳከ ፡ ግሥ ፡ ተ.ግ.

(ለ) የሐረር ፡ ጠቅላይ ፡ ግዛት ፡ ጽሕፈት ፡ ቤት ፡ የሐረር ፡ ጠ.ግ.ጽ. ቤት ።

፳፪ ፡ ነጠብጣብ ፡-የተዠመረ ፡ ነገር ፡ መቀነሱን ፡ ወይም ፡ በውጥን ፡ መቅረቱን፡ ወይም ፡ መጕደሉን ፡ የሚያመለክቱ ፡ ናቸው ።

(ሀ) እርሳሱን ፡ ለማን ፡ ሰጠኸው ? ለ- - - - - ሰጥቼዋለሁ ።

(ለ) ሰው ፡ እውነተኛውን ፡ ነገር ፡ ተከትሎ ፡ ቢሠራ ፡ ብዙ ፡ ተቃዋሚ ፡ ነገሮች ፡ ይገጥሙታል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በትዕግሥት ፡ ድል ፡ ቢያደርጋቸው ፡ የሚገኘው ፡ ነገር ፡ - - - - - - - ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ፡ ድርሰት ።

ድርሰት ፡ የሚባለው ፡ ቃል ፡ ከግዕዝ ፡ የመጣ ፡ ነው ። ዋናው ፡ ግሱ ፡ «ደረሰ» ፡ ነው ፡ ደረሰ ፡ ማለትም ፡ አንድ ፡ መጽሐፍን ፡ ጻፈ ፡ ማለት ፡ ነው ። ከዚህም ፡ የተነሣ ፡ ጸሐፊው ፡ «ደራሲ» ፡ ተብሎ ፡ ይጠራል ። እንግዴህ ፡ ድርሰት ፡ ማለት ፡ ጽሑፍ ፡ መሆኑን ፡ እንገንዘብ ። በግዕዝ ፡ የቀድሞ ፡ አባቶቻችን፡ ከደረሷቸው፡ መጻሕፍት ፡ አንዳንዶቹ፡ ድርሳን ፡ ዘእገሌ ፡ ተብለው ፡ ይጠራሉ ። አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ድርሳን፡ ያንድ ፡ የቅዱስን፡ የሕይወት ፡ ታሪክና ፡ ገድል ፡ ይዞ ፡ ይገኛል ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ቅዱሱ ፡ ከቸሩ ፡ እግዚአብሔር ፡ በተሰጠው ፡ ሀብት ፡ (ጸጋ) ፡ ድውያንን ፡ ይፈውስ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ይሠራቸው ፡ የነበሩት ፡ ተአምራት ፡ በድርሳኑ ፡ ውስጥ ፡ ይጠቀለሉ ፡ ነበር ።

አንዳንድ ፡ ቅዱሳን ፡ ከሕፃንነታቸው ፡ ዠምረው፡ በእግዚአብሔር ፡ የተመረጡ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ የሕይወት ፡ ታሪኮቻቸውና ፡ የሠሯቸው ፡ ተአምራት ፡ የተያያዙ ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ ተአምር ፡ በሚል ፡ ውስጥ ፡ ተጠቅልለውና ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ የድርሰት ፡ ሥነ ፡ ሥርዐት ፡ ተዘጋጅተው ፡ ይጻፉ ፡ ነበር ።

መልክአ ፡ መድኀኔ ፡ ዓለም ፤ መልክአ ፡ ማርያምና ፡ የየቅዱሳኖቹ ፡ መልክእ ፡ ሁሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ ድርሰት ፡ ነው ። እንደዚህ ፡ ያለውም ፡ ድርሰት ፡ የተሰጠውን ፡ አርእስት ፡ መልክና ፡ ግብር ፡ እያጋነነና ፡ እያሞገሰ ፡ ይገልጻል ። ስለዚህ ፡ በዚህ ፡ መንገድ ፡ የሚጻፈው ፡ ድርሰት ፡ «ሥዕላዊ» ፡ ድርሰት ፡ ተብሎ ፡ ይጠራል ። ሥዕላዊ ፡ ድርሰት ፡ ባይን ፡ የታየውንና ፡ በግብር ፡ የተገለጸውን ፡ በተጌጠ ፡ አማርኛ ፡ እያስማሙና ፡ እያዋሐዱ ፡ የሚገልጹበት ፡ ነው ። ሥዕላዊ ፡ ድርሰት ፡ የተባለበት ፡ አንድ ፡ ሠዓሊ ፡ ባንድ ፡ ሥዕል ፡ ላይ ፡ በውነተኛው ፡ ነገር ፡ ባይኑ ፡ ያየውን ፡ ወይም ፡ ባይነ ፡ ልቡናው ፡ የተመለከተውን ፡ እንደየመልኩ ፡ መጠን ፡ ቆንጆውን ፡ በቆንጆነት ፡ መልክ ፡ ጥፉውን ፡ በመልከ ፡ ጥፉነት ፡ መልካሙን ፡ ግብር ፡ በመልካም ፡ ጠባይነትና ፡ መጥፎውን ፡ ጠባይ ፡ በመጥፎ ፡ ሠራተኛነት ፡ መርምሮ ፡ በተረዳው ፡ መሠረት ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ዘዴ ፡ አሳክቶ፡ እንደሚገልጽ ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ ደራሲ ፡ አንዳንድ ፡ ሠዓሊ ፡ እውነተኛውን ፡ ሥዕሉን ፡ በወረቀት ፡ ላይ ፡ ሳይነድፍ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ቃላት ፡ እያስጌጠ ፡ ሊገለጽ ፡ የሚፈለገውን ፡ ሰው ፡ ወይም ፡ ነገር ፡ ለአእምሮአችን ፡ አጉልቶ ፡ ስለሚያሳይ ፡ ነው

ብዙ ፡ ድርሰቶች ባቀነባባሪያቸው ፡ ተሳክተው ፡ አንድ ፡ ድርሳን ፡ ወይም ፡ አንድ ፡ መጽሐፍ ፡ ለመሆን ፡ ይችላሉ ። የድርሰቱም ፡ ማጠርና ፡ መርዘም ፡ በጸሐፊው፡ አሳብ ፡ ይወሰናል ። የመጽሐፉም ፡ ትልቅነትና ፡ ትንሽነት ፡ እንዳንድ ፡ ድርሰት ፡ በጸሐፊው ፡ አሳብ ፡ ይወሰናል ።

አንድ ፡ ደራሲ ፡ ባንድ ፡ መድኀኒት ፡ ቀማሚ ፡ ይመሰላል ። አንድ ፡ መድኀኒት ፡ ቀማሚ ፡ ሳይማርና ፡ ልምድ ፡ ሳያደርግ ፡ እንዲያው ፡ ከመሬት ፡ ተነሥቶ ፡ መድኀኒት ፡ ቀማሚ ፡ እሆናለሁ ፡ ቢል ፡ ማንም ፡ አይቀበለውም ። አስቀድሞ ፡ አንድ ፡ ነገርን ፡ ከመቀመሙ ፡ በፊት ፡ የሚቀመሙትን ፡ ነገሮች ፡ በያይነታቸው ፡ እየሰበሰበ ፡ በሚያሰናዳበት ፡ ሥፍራ ፡ ማስቀመጥ ፡ አለበት ። ተፈላጊዎች ፡ ነገሮች ፡ በያይነታቸው ፡ ከቀረቡ ፡ በኋላ ፡ ባንድነት ፡ እየተዋሐዱ ፡ (እየተገጣጠሙ) ፡ አንድ ፡ ዐይነት ፡ በሽታ ፡ የሚፈውሱትን ፡ ይቀምማል ። ይህንም ፡ የቀመመውን ፡ መደኀኒት ፡ ለሕዝብ፡ ከመስጠቱ ፡ በፊት፡ በትንንሾችና ፡ በትልልቆች ፡ እንስሳት ፡ ላይ ፡ ይፈትነዋል ። ደኅና ፡ አድርጎ ፡ ግብሩን ፡ አጣርቶና ፡ መጠኑን ፡ ለክቶ ፡ ካወቀ ፡ በኋላ ፡ ለሕዝብ ፡ ይሰጣል ።

እንደዚሁም ፡ ጽሑፉን ፡ ከማዘጋጀት ፡ በፊት ፡ የጽሑፉን ፡ ሥነ ፡ ሥርዐት ፡ ጠንቅቆ ፡ ማጥናት ፡ ላንድ ፡ ደራሲ ፡ ዋና ፡ ተግባሩ ፡ ነው ። ከዚህ ፡ በኋላ፡ የሚጽፈውን፡ ነገር ፡ በየፈርጁ ፡ እያጠና ፡ ይሰበስብና ፡ ባንድነት ፡ እየተቀነባበሩ ፡ ስሜት ፡ የሚሰጡትን ፡ ነገሮች ፡ በየወገናቸው ፡ ጠቅልሎ ፡ ይጽፋቸዋል። ደራሲው ፡ የሚጽፈውን ፡ ነገር፡ ባሳቡ ፡ እንደ ፡ መጣለት ፡ ጽፎ ፡ ሳያሳትም ፡ የጽሑፉን ፡ ቅደም ፡ ተከተልና ፡ ጠቃሚነት ፡ እየመላለሰ ፡ ያርመዋል ። በመጨረሻውም ፡ ጠቃሚነቱ ፡ ተረጋግጦ ፡ ታትሞ ፡ ይወጣና ፡ ለሕዝብ ፡ ይሰጣል ።

መድኀኒት ፡ ቀማሚና ፡ ደራሲ ፡ የሚለያዩበት ፡ ቀማሚ ፡ በዐይን ፡ የሚታዩትንና፡ በእጅ ፡ የሚዳሰሱትን ፡ ነገሮች ፡ እየሰበሰበና ፡ በእጁ ፡ እያገላበጠ ፡ ስለሚቀምማቸው ፡

ነው ። ደራሲው ፡ ግን ፡ በአእምሮው ፡ እየሰበሰበና ፡ እየቀረጸ ፡ ይጽፋል ፡ እንጂ ፡ እንደ ቀማሚው ፡ በእጁ ፡ አይዳስሳቸውም ፡ በዐይኑም ፡ አያያቸውም ። ከተጠቀሱት ፡ ምክን ያቶች ፡ በቀር ፡ እየሰበሰቡ ፡ ቀምሞና ፡ አዘጋጅቶ ፡ ለሕዝብ ፡ በመስጠት ፡ ግን ፡ አንድ ናቸው ። በሥራቸው ፡ ይመሳሰላሉ ። እንሆ ፡ የድርሰት ፡ ሐተታ ፡ መግቢያ ፡ እስከዚህ ነው ።

## የዜና ፡ አሰባሰብ ፡

አንድ ፡ ሰው ፡ ድርሰትን ፡ ሲጽፍ ፡ ወሬን ፡ ለማግኘት ፡ እንዴት ፡ እንደሚችል ፡

ሰው ፡ በተፈጥሮ ፡ አስተያየቱ ፡ ለመመራመር ፡ ከፈለገ ፡ ብዙ ፡ ነገሮች ፡ ባጠገቡ ፡ በዙሪያው ፡ ስለሚገኙ ፡ ለማየትና ፡ ለመረዳት ፡ ይችላል ። ማናቸውም ፡ ነገር ፡ ሰው ራሱ ፡ ሄዶ ፡ ካልመረመረው ፡ ነገሩ ፡ በገዛ ፡ ራሱ ፡ መጥቶ ፡ በሰውዬው ፡ አንጎል ውስጥ ፡ ለመቀረጽ ፡ አይችልም ። ሰው ፡ አስተዋይነቱን ፡ የሚሠራበት ፡ በተቀደሰ ፡ መንፈስ ፡ (በቅንነት) ፡ ሊያውቀው ፡ የሚገባውን ፡ ነገር ፡ ሳይሰለች ፡ በትዕግሥት ፡ እየተራቀቀ ፡ ለማወቅ ፡ የፈለገ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ነው ። ማንኛውም ፡ ተማሪ ፡ በተቻለው ፡ መጠን፡ እየተመራመረ ፡ በሚከተሉት ፡ መንገዶች ፡ ወይም ፡ ዘዴዎች ፡ ቢያጠና ፡ ይሻለዋል ።

፩ ፡ አንድ ፡ ተማሪ ፡ ለማወቅ ፡ ስለሚፈልገው ፡ ነገር ፡ (አርእስት) ፡ ወላጆቹን ፡ ታላላቆቹን ፡ ባልንጀሮቹንና ፡ አስተማሪዎቹን ፡ እየጠየቀ ፡ ቢማር ፡ ብዙ ፡ ነገሮችን ፡ ለማወቅ ፡ ይችላል ።

፪ ፡ ስለሚጠይቀው ፡ ነገር ፡ ባራት ፡ ማዕዘን ፡ መመልከት ፡ ያስፈልገዋል ።

## ያጠያየቁ ፡ ዘዴ ፡

### (ሀ) በዐይን ፡ ለሚታይና ፡ በእጅ ፡ ለሚዳሰስ ፡ ሕይወት ፡ ለሌለው ፡ ነገር ፡

1 ይህ ፡ ነገር ፡ ምንድር ፡ ነው ? ዐይነቱንና ፡ ግብሩን ፡ ለመረዳት ፡ መሞከር ፡

2 ከምን ፡ መጣ ? ከመሬት ፡ ውስጥ ፡ ከዕፀዋት ፡ ከባሕር ፡ ውስጥ ፡ ከእንስሳት ፡

3 ለምን ፡ መጣ ? በምን ፡ ምክንያት ፡ መጣ ? ለምን ፡ ይጠቅማል ?

4 ማን ፡ አመጣው ? የሠራው ፡ ማነው ?

5 እንዴት ፡ አድርጎ ፡ ሠራው ? ያሠራሩን ፡ ዘዴ ፡ ጠይቆ ፡ መረዳት ፡

6 መቼ ፡ አመጣው ? መቼ ፡ ሠራው ?

7 ለዕቃው ፡ እንዴት ፡ ያለ ፡ ጥንቃቄ ፡ ሊደረግለት ፡ ይቻላል ?

አንድ ፡ ተማሪ ፡ በዚህ ፡ ዘዴ ፡ የጠየቀ ፡ እንደሆን ፡ ለጥያቄው፡ ተገቢ፡ መልስ፡ ሊያገኝለት ፡ እንደሚችል ፡ የተረጋገጠ ፡ ነው ።

### (ለ) ለረቂቅ ፡ ነገር ፡

1 አሳቡን ፡ ማን ፡ (ምን) ፡ አመነጨው ?

2 በምን ፡ ምክንያት ፡ አሰበው ፡ (አነቃው) ?

3 እንዴት ፡ አድርጎ ፡ አሳቡን ፡ ገለጸው ?

4 መቼ ፡ ዠመረው ፡ (አሰበው) ?

5 አሳቡ ፡ መቼ ፡ ተጀምሮ ፡ መቼ ፡ ተፈጸመ ?

6 ውጤቱ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ክፉ ፡ ነው ፣ ወይስ ፡ ደግ ?

7 እንደዚህ ፡ አስቦ ፡ ላደረገ ፡ ሰው ፡ ምን ፡ ማድረግ ፡ ይገባል ? መጥፎ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ቅጣት ፣ መልካም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሽልማት ፡ ማወቅ ፡ ያስፈልጋል ።

8 እንደዚህ ፡ ከሆነ ፡ ምን ፡ ማድረግ ፡ ይገባል ? ክፉ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ መራቅ ፡ መልካም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ግን ፡ ምሳሌ ፡ አድርጎ ፡ ለመሥራት ፡ መጣጣር ፡ ይገባል ።

(ሐ) ስለ ፡ እንስሳትና ፡ ዕፀዋት ፡

1 ስሙ ፡ ምንድር ፡ ነው ?

2 ምን ፡ ዐይነት ፡ ዛፍ ፡ ነው ? ምን ፡ ዐይነት ፡ ጠባይ ፡ አለው ?

3 በየት ፡ ይበቅላል ? በደጋ ? በወይና ፡ ደጋ ? ወይስ ፡ በቆላ ?

4 እንዴት ፡ ያለ ፡ ምግብን ፡ ይወዳል ?

የእንስሳት ፡ ምግብ ፡ ለብቻው ፡ እንደ ፡ ሆነና ፡ ያበላላቸውም ፡ ዘዴ ፡ ልዩ፡ እንደ፡ ሆነ ፡ ማወቅ ፡ ያስፈልጋል ።

5 ለሰው ፡ ወይም ፡ ለእንስሳት ፡ እንዴት ፡ ያሉ ፡ ጥቅሞችን ፡ ይሰጣል ?

6 እንዴት ፡ ያለ ፡ ጉዳትን ፡ ያመጣል ?

7 ሰው ፡ በዙሪያው ፡ ላሉት ፡ ዕፀዋትና ፡ እንስሳት ፡ የሚጠቅሙ ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ወይም ፡ የሚጎዱ ፡ ምን ፡ ማድረግ ፡ ይገባል ?

፫ ፡ የሚያጠናውን ፡ አስመጥቶ ፡ ወይም ፡ አለበት ፡ ቦታ ፡ ድረስ ፡ ሄዶ ፡ ማየት ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ ነገር ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ ስለሚያጠናው ፡ ነገር ፡ የሚያጠግብ፡ ወሬ፡ ካልሰማ ፡ ፍላጎት ፡ አያድርበትምና ፤ አስቀድሞ ፡ ስለሚፈልገው ፡ ነገር ፡ ወሬን ፡ መስማት ፡ የበለጠ ፡ ጠቃሚ ፡ ነገር ፡ ነው ።

፬ ፡ ለማወቅ ፡ የሚፈልገውን ፡ ነገር ፡ በዐይኑ ፡ እያየና ፡ እየዳሰሰ ፡ ለማጥናት ፡ የማይችል ፡ በተቻለው ፡ መጠን ፡ ሥዕሎችን ፡ እየመረመረና ፡ ልብ፡ እያደረገ ፡ ሊያጠና፡ ይችላል ።

፭ ፡ መጻሕፍት ፡ ከሰው ፡ ጠይቆ ፡ ሊያገኘው ፡ የማይችለውን ፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ ሕዝቦችን ፡ ባህልና ፡ ጥበብ ፡ በየወገን ፡ በየወገናቸው ፡ ይዘው ፡ ስለሚገኙ ፡ እነርሱን ፡ እየመረመረና ፡ እያስተዋለ ፡ የሚያገኛቸውን ፡ ጠቃሚ ፡ ነገሮች ፡ በአእምሮው ፡ ለማሳደር ፡ ይችላል ። አንድ ፡ ተማሪ ፡ ስለሚፈልገው ፡ አንድ ፡ መጽሐፍን ፡ ብቻ ፡አንብቦ ፡ መተው ፡ አይገባውም ፤ በተቻለው ፡ መጠን ፡ ስለ ፡ እርእስቱ ፡ የሚያወሩትን ፡ እየፈለገ ፡ ማጥናት ፡ ያስፈልገዋል ።

፮ ፡ ብዙ ፡ ነገሮችን ፡ ካወቀ ፡ በኋላ ፡ ጉዳታቸውንና ፡ ጥቅማቸውን ፡ በአንጎሉ ፡ ውስጥ ፡ እየፈለገ ፡ አመዛዝኖ ፡ መለየትና ፡ እንዲህ ፡ ከሆነ ፡ እንደዚህ ፡ መሆን ፡ ይገባዋል ፡ እያለ ፡ ማሰላሰል ፡ አለበት ።

## የዕቃዎች ፡ የዕፀዋትና ፡ የእንስሳት ፡ ስሞች ፡ ለምን ፡ እንደ ፡ ተጻፉ ፡ የሚገልጽ ።

በዚህ ፡ ክፍል ፡ የተጻፉት ፡ ቃላት ፡ ስለ ፡ ሦስት ፡ ነገሮች፡ ተጽፈዋል ፤ እነርሱም፡ የሚከተሉት ፡ ናቸው ።

፩ ፡ ልጆች ፡ የዕቃዎችን ፡ ስሞችና ፡ አገልግሎታቸውን ፡ ሲያውቁ ፡ ከምን ፡ እንደ፡ መጡ ፡ ለምን ፡ እንደ ፡ መጡ ፡ ማን ፡ እንዳመጣቸውና ፡ መቼ ፡ እንደ ፡ መጡ ፡ ባለማወቃቸው ፡ ለመመራመር ፡ ስለማይፈልጉ ፡ እያስረዳን ፡ አረፍተ ፡ ነገሮችንና ፡ ድርሰቶችን ፡ እንድናሠራባቸው ፡ ነው ።

፪ ፡ ልጆች ፡ በውጭ ፡ አገር ፡ መጻሕፍት ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ስሞችን ፡ እያጠኑ ፡ ሲያውቁ ፡ ባማርኛችን ፡ ለማወቅ ፡ ባለመቻላቸው ፡ ሐዘን ፡ ስለ ፡ ተሰማኝ ፡ ለወደ ፡ ፊቱ ፡ በዚሁ ፡ ዐቅድ ፡ እያጠኑ ፡ ያለችግር ፡ ከእንግሊዝኛ ፡ መጻሕፍት ፡ ከሚያገኙዋቸው ፡ ስሞች ፡ ጋራ ፡ እያስማሙ ፡ ለማጥናት ፡ እንዲችሉ ፡ ነው ።

፫ ፡ ልጆች ፡ ስለ ፡ ዕፀዋትና ፡ ስለ ፡ እንስሳት ፡ በጥበብ ፡ (በሥነ ፡ ፍጥረት)፡ጥናት፡ ዐቅድ ፡ እየተከታተሉ ፡ ለመመርመር ፡ እንዲችሉና ፡ ብዙ ፡ ነገሮችን ፡ እያጠኑ ፡ ፍሬ ፡ ፍሬ ፡ ነገራቸውን ፡ በአእምሮአቸው ፡ ውስጥ ፡ እንዲቀርጹት ፡ ነው ።

ቃላቱን ፡ የሰበሰብኋቸው ፡ ካማርኛ ፡ አስተማሪዎች ፡ (መምህራን ፡ ጋራ ፡ እየተ መካከርሁ ፡ ነው ።

### ለሰው ፡ አገልግሎት ፡ የሚገቡ ፡ ነገሮች ፡

**1 ልብስ ፡**

እጀጠባብ ፡
ሱሪ ፡
ቆብ ፡
ኮት ፡
ሸሚዝ ፡
ኩታ ፡
ሰደርያ ፡
የውስጥ ፡ ልብስ ፡
ቀሚስ ፡
መቀነት ፡
ካቦርት ፡
በርኖስ ፡
ጃኖ ፡
ነጠላ ፡
ጋቢ ፡
ጫማ ፡
ባርኔጣ ፡
ጃንጥላ ፡
ሹራብ ፡
ክራቫት ፡
አንገት ፡ ልብስ ፡
ፎጣ ፡
መሐረብ ፡
ጥብጣብ ፡
ቀበቶ ፡
ማተብ ፡

**2 የቤት ፡ ጌጥ፡ (ልብስ) ፡**

ጉትቻ ፡
ድሪ ፡
ቀለበት ፡ (ሐብል) ፡
አንባር ፡
አሸን ክታብ ፡
ወለባ ፡ (ጠጉር ፡ ማሲያዣ) ፡
አልቦ ፡
ልብ ፡ አልማ ፡
ድኮት ፡
መስቀል ፡
ኩክ ፡ ማውጫ ፡

**3 የማዕርግ ፡ ልብስ ፡ (መለዮ) ፡**

ዘውድ ፡
ራስ ፡ ወርቅ ፡
ራስ ፡ ቁር ፡
ጉሜ ፡
ጎፈር ፡
ለምድ ፡
ቢታዋ ፡ (የጎበዝ መለዮ) ፡

ግምጃ ፡ ሱሪ ፡
ቡቃዳዲ ፡ (በራስ፡ ላይ ፡ ታስሮ ፡ ወደ ፡ ታች ፡ የሚወርድ ፡ ሰንደቅ ፡ ዓላማ ) ፡
መዳሊያ ፡

4 የጦር ፡ መሣሪያ ፡

ጦር ፡
ሰይፍ ፡ (ሻምላ) ፡
ጎራዴ ፡
ሐኔ፡ (ጎባጣ ፡ የራያ ፡ ጎራዴ) ፡
ጋሻ ፡
ጠመንዣ ፡ (ነፍጥ) ፡
ሽጉጥ ፡
ጩቤ ፡
ሾተል ፡
መትረየስ ፧
መድፍ ፡
ወረንጦ ፡
ሳንጃ ፡
ጥሩር ፡
ቍር ፧
ታንክ ፡
ቦንብ ፡

5 የቤት ፡ ዕቃ ፡

(ሀ) የወጥ ፡ ቤት ፡ ዕቃ ፡

የሸክላ ፡ ድስት ፡
የብረት ፡ ድስት ፡
የድስት ፡ እፊያ ፡
መጥበሻ ፡
መቁሊያ ፡
ጭልፋ ፡
ማንኪያ ፡
ሹካ ፡
አፍላል ፡
ምንቸት ፡
ማሰሮ ፡
ጣባ ፡ (ወጭት) ፡
ሣሕን ፡
ማማሰያ ፡
የሸሮ ፡ ቅል ፡
የድልኸ ፡ ቅል ፡
የቅመም ፡ ቅል ፡
ማጥለያ ፡

(ለ) የእንጀራ ፡ ቤት ፡ ዕቃ፡

ምጣድ ፡
ሞግድ ፡
አክንባሎ ፡
አሎሎ ፡
ፋጉሎ ፡
ጉልቻ
መስቴ ፡
ገበቴ ፡
ደቅ ፡
ቆሬ ፡
ዋዲያት ፡
ቡሐቃ ፡
ገንዳ ፡
ማሠሻ ፡
መስቅሰቂት ፡
መጨቅጨቂት ፡
መሳቢያ ፡
የመሶብ ፡ እፊያ ፡
እግረ ፡ መሶብ ፡
(ግብር ፡ መብሊያ) ፡
ሌማት ፡

(ሐ) መስፈሪያ ፡ (ለእህል)

ቁና ፡
ርቦ ፡
እፍኝ ፡
ጥርኝ ፡ (የጽፍኝ ፡ እኩሌታ) ፡
ምሸሽ ፡ } 3 ቁና ፡ የሚይዝ ፡
ላዳን ፡
እንቅብ ፡ }
ቀራዋ ፡
ዳውላ ፡

(መ) የወፍጮ ፡ መሣሪያ ፡

ማጉረሻ ፡
መከርተፊያ ፡
መሰለቂያ ፡
መለንቀጫ ፡
መጅ ፡
ቋት ፡
ሙሬ ፡

(ሠ) የወተት ፡ ዕቃ ፡

ማለቢያ ፡
የወተት ፡ ቅል ፡
ማጠራቀሚያ ፡
መናጫ ፡
መስበቂያ ፡
ጋዲ ፡ (ጠፍር ፡ ገመድ) ፡

(ረ) የፈትል ፡ መሣሪያ ፡

መዳመጫ ፡
የብረት } መዳመጫ ፡
የእንጨት ፡ }
ደጋን ፡
መታረሪያ ፡
ቅል ፡ አንገት ፡
እንዝርት ፡
ቋንጣ ፡
ማዳወሪያ ፡
ዋግንቦ ፡
አንከርት ፡
ቀሠም ፡
አገልግል ፡

6 የሸማኔ ፡ መሣሪያ ፡

መን ፡
ዐርብ ፡
የመን ፡ ብር ፡
የመን ፡ እንጨት ፡
መጠቅለያ ፡
መተራትር ፡
ቁምጭር ፡
መጠፈኛ ፡
መወርወሪያ ፡
ማንሸርሸሪያ ፡
መርገጫ ፡
መቂናጥ ፡
የግራና ፡ የቀኝ ፡ ባላ ፡
የፊት ፡ ግንድ ፡ መላሽ ፡
የኋላና ፡ የፊት ፡ ባላ ፡
የፊት ፡ ግንድ ፡
ማበቻ ፡
መቀጠቢያ ፡
ደንቆሮ ፡ (ባላ) ፡

7 የመኝታና ፡ የመቀመጫ ፡ መሣሪያ ፡

አልጋ ፡
የብረት ፡ አልጋ ፡
የጠፍር ፡ አልጋ ፡
የሸራ ፡ አልጋ ፡
የገመድ ፡ አልጋ ፡
ፍራሽ ፡ (ቁርበት) ፡
ትራስ ፡
የአልጋ ፡ ልብስ ፡
አንሶላ ፡ (ነት) ፡
የብርድ ፡ ልብስ ፡
አጎበር ፡

8 የጽሕፈት ፡ መሣሪያ ፡

ወንበር ፡
ጠረጴዛ ፡
ማሥመሪያ ፡
ሣንቲሜትር ፡
እርሳስ ፡
ወረቀት ፡
ብርዕ ፡
ቀለም ፡
ማምጠጫ ፡
ላጲስ ፡
ብልቃጥ ፡
መቅረጫ ፡
ካርቦን ፡
የጽሕፈት ፡ መኪና ፡
የኪስ ፡ ብርዕ ፡ (ወነቶ) ፡

9 የወጌሻ ፡ መሣሪያ ፡

ምላጭ ፡
ዋገምት ፡
አንካሴ ፡
መቆንጠጫ ፡
የጀንጥላ ፡ ብረት ፡ (ጣጤ) ፡
ጉባ ፡
መቀስ ፡
መርፌ ፡
የውኃ ፡ መርጫ ፡
ጥሩንባ ፡ (ጢቆሽ) ፡
ሠም ፡
ሣሕን ፡
ብርጭቆ ፡

10 ያናጢ ፡ መሣሪያ ፡

መላጊያ ፡
መጥረቢያ ፡
መጋዝ ፡
መሰርሰሪያ ፡
መሮ ፡
መለኪያ ፡
ማሥመሪያ ፡
ሣንቲሜትር ፡
ሜትር ፡
ኢንች ፡
ያርድ ፡
ማዕዘን ፡
ሞረድ ፡
መዘውር ፡
ጉጠት ፡ (መቈንጠጫ) ፡
እርሳስ ፡

11 የግንበኛ ፡ መሣሪያ ፡

የውኃ ፡ ልክ ፡
መዶሻ ፡
ድጅኖ ፡
መራጃ ፡
መለሰኛ ፡
መሮ ፡ (የድንጊያ ፡ መብሻና ፡ መጥረቢያ) ፡
ገመድ ፡
መሰላል ፡
ዶማ ፡
አካፋ ፡
የጭቃ ፡ ማመላለሻ ፡ እንደ ፡ ቆርቆሮ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡

12 የእርሻ ፡ መሣሪያ ፡

ሞፈር ፡
ዕርፍ ፡
ድግር ፡
ማረሻ ፡
ወገል ፡
ቅትርት ፡
ቀንበር ፡
ማነቆ ፡
መርገጥ ፡ (የወገል ፡ ጠፍር) ፡
የማነቆ ፡ ጠፈር ፡

ምራን ፡
ጅራፍ ፡
ደንጎራ ፡
አካፋ ፡
ማጭድ ፡ ( ገለዶ ) ፡
መጥረቢያ ፡
ገገሞ ፡
ዶማ ፡
ጠገራ ፡ (ፋስ) ፡
ምሣር ፡
ላይዳ ፡
መንሽ ፡ ( መበርበሪያ ) ፡
ሙጭ ፡
ማርገቢያ ፡
ማጠያ ፡
መሥሪያ ፡ ( በያይነቱ ) ፡
መጫኛ ፡
ስልቻ ፡
መንጫ ፡

13 የበቅሎ ፡ ዕቃ ፡

ኮርቻ ፡ ከነልም ፡ ዕቃው ፡
ፉሎ ፡ ( ልባብ ) ፡
ልጓም ፡
ዛብ ፡
ርካብ ፡
እምቢያጉስ ፡
አቡነ ፡ ዘለብ ፡ ( ወዴላ ) ፡
መቀነቻ ፡
ወፍለቅ ፡
ጥንብ ፡ ከነልባዱ ፡
ቀዳማይ ፡
ደኃራይ ፡
ለኮ ፡ ( መሳቢያ ) ፡
መዘውር ፡
ድብዳብ ፡
ግላስ ፡

በለዲ ፡
ዶቃ ፡ ( ሥሉሴ ) ፡
ቀሚስ ፡
ድግድግ ፡ (መረሻት) ፡
አለንጋ ፡
ዘለበት ፡
መጣብር ፡
አምፋሮ ፡
ቤኔቻ ፡
ዕፀዋት ፡

1 ከፍተኛ ፡ ዛፎች ፡

ባሕር ፡ ዛፍ ፡
ጥድ ፡
ዝግባ ፡
ወይራ ፡
ዋንዛ ፡
ዶቅማ ፡
የጎሣም ፡ ወይራ ፡
ሾላ ፡
ሰሳ ፡
ውልክፋ ፡
ገተር ፡
ሰገድ ፡
ወርካ ፡
ሸፈሬ ፡ (የቆላ ፡ ዛፍ) ፡
ዝዶም ፡ (የቆላ፡ ዛፍ) ፡
ገባ ፡ ( ቁርቁራ ) ፡
ቃውት ፡ ( መተቆማ) ፡
ኮሶ ፡
ብሳና ፡
በደኖ ፡ ( ጆሞ ) ፡
እንኮይ ፡
ዋሸንት ፡
ጋሜ ፡
ሎል ፡
ቧቧ ፡

ብርብራ ፡
ግራር ፡
ቀንጠ ፡
ደሬ ፡
ሽነት ፡ ( ሽግት ) ፡
አሐያ ፡ (ሹንሹና) ፡
አዛምር ፡
መሬንዝ ፡
አንቃ ፡
አባሎ ፡
ሆጭ ፡ ( ኮርች ) ፡
ተምር ፡
አንፋር ፡
ምሣር ፡ ገንፎ ፡
ሸውሸዌ ፡
ሺዬ ፡ ( ሾዬ ) ፡
ጠዴቻ ፡ ( ዴዴሳ ) ፡
ዋጨ ፡ ዋጫ ፡
አጣጥ ፡
አሽቃሞ ፡
ኮክ ፡
ምንታፋላ ፡
ኮማ ፡

2 አነስተኛ ፡ ዛፎች ፡

ግራዋ ፡
ቀጨሞ ፡
አስታ ፡
እንጆሪ ፡
ጨጮ ፡
ጉመሮ ፡
ደደሆ ፡
ጠንበለል ፡
ምስርች ፡
ቀጋ ፡
አጋም ፡
ቀንጠፋ ፡

ቅንጭብ ፡
ድግጣ ፡
ወናሂ ፡ ( ሰንሰል )
ለንቋጣ ፡
ቀጠጥና ፡
ኮሽም ፡
ጣቅማ ፡
ጥቁር ፡ ዱር ፡
ወንዝ ፡ አድምቅ ፡
የእረኛ ፡ ዳቦ ፡
በትረ ፡ ሙሴ ፡
መቃ ፡
ሸመል ፡
ቀርቅሃ ፡
ሸምበቆ ፡
ጥንጁት ፡
ቀረጥ ፡
ጉሎ ፡

3 ቍጥቋጦች ፡

ፍየለ ፡ ፈጅ ፡
የፈረስ ፡ ዘንግ ፡
ዳማ ፡ ከሴ ፡
እንቧይ ፡
እንቧጮ ፡
ችፍርግ ፡
ወይናግፍት ፡
ከስከሶ ፡
ዝንኪላ ፡
ዘርጭ ፡ እንቧይ ፡
ገበር ፡ እንቧይ ፡
ኮሸሽላ ፡
ጉሎ ፡
ቀስተንቻ ፡ ( ሰሪቴ ) ፡
ናጫ ፡
አመራሮ ፡

4 ሐረግ ፡ ( አረግ ) ፡

ጠሮ ፡
የዝሆን ፡ ሐረግ ፡
አዞ ፡ ሐረግ ፡
ሞይደር ፡
ሽምቡርት ፡
ቋንዶ ፡ ሐረግ ፡
ጀንፎቅ ፡
አለብላቢት ፡
ያረግ ፡ ሬሳ ፡
የምድር ፡ እንቧይ ፡
እንዶድ ፡
ላንቁሶ ፡
አሰርኩሽ ፡
እንጎችት ፡
ያሞራ ፡ ምሳ ፡
ያይጥ ፡ ሐረግ ፡

5 የማይበሉ ፡ ቅጠሎች ፡

ዕፀ-ፋርስ ፡
አስተናግርት ፡
መጭ ፡
ልት ፡
ቱልት ፡
አመድማዶ ፡
ግርሽጥ ፡
ቀጠጥና ፡
በጋ ፡ ነፍሴ ፡
ውኃ ፡ አይነካሽ ፡
አሞጭ ፡
ሥራህ ፡ ብዙ ፡
እሁል ፡ ገብ ፡
ጭጎጎት ፡
ጠለንጅ ፡
ፍቅሩ ፡ ጠና ፡
እንደኋሁላ ፡

ወፍ ፡ አንቁር ፡
ኩርንችት ፡
የሽኮኮ ፡ ጎመን ፡
ቀበርቾ ፡
ወገርት ፡
ሰሪቴ ፡ ( ቁስበደጁ ) ፡

6 የሚበሉ ፡ ቅጠሎች ፡

ጎመን ፡
ሰላጣ ፡
ኩርንባ ፡ ( ጥቅል ፡ ጎመን )
አልማ ፡
አውጥ ፡
ሳማ ፡
ሺጊሚጢ ፡ ( ሲጢሚጢ )
አንጣሪያ ፡
የወፍ ፡ ዘረር ፡
ሰናፍጭ ፡

7 የሚበሉ ፡ ተክሎች ፡

ብርቱካን ፡
ሎሚ ፡
ኮክ ፡
መንደሪን፡ (የሱፍ ፡ አፈንዲ)
ዘይቱን ፡
ወሸመላ ፡
ፓፓያ ፡
ሙዝ ፡
ማንጎ ፡
ቱፋሕ፡
ጊሽጣ ፡
ዱባ ፡
ሐብሐብ ፡
ቲማቲም ፡
ባዝንጀር ፡
ቡና ፡
ጫት ፡

ጌሾ ፡
ቁልቋል ፡ ( የባሕር ) ፡
ተምር ፡
ወይን ፡
ሸንኮር ፡ አገዳ ፡
ሮማን ፡
ትርንጎ ፡
ሾላ ፡

8 የአገዳና ፡ የብርዕ፡እህሎች፡

ማሽላ ፡
ጤፍ ፡
ዘንጋዳ ፡
ስንዴ ፡
ገብስ ፡
አጃ ፡
በቆሎ ፡
ዳጉሳ ፡
ጠመዥ ፡

9 ጥራጥሬ ፡ እህሎች ፡

ሽንብራ ፡
ባቄላ ፡
ምስር ፡
ጓያ ፡
ዐተር ፡
አደንጓሬ ፡

10 የቅባት ፡ እህሎች ፡

ኑግ ፡
ተልባ ፡
ሱፍ ፡
ሎዝ ፡
ሰሊጥ ፡

11 ቅመማቅመም ፡

ጤና ፡ አዳም ፡
ድንብላል ፡
ቁንዶ ፡ በርበሬ ፡
በሶ ፡ ብላ ፡
ጦስኝ ፡
ቀረፋ ፡
ከሙን ፡
በርበሬ ፡
እንስላል ፡
ክበብስኒ ፡
እብሽ ፡
አዝሙድ ፡
ቅርንፉድ ፡
አደስ ፡
ጎመን ፡ ዘር ፡

12 የሚበሉ ፡ ሥሮች ፡

እርድ ፡
ድንች ፡
ካሮት ፡
ሚጣጢስ ፡ (ስኳር ፡ ድንች) ፡
ሽንኩርት ፡
ባሮ ፡
ኮረሪማ ፡
ዝንጅብል ፡
መቅመቆ ፡
አስዋቢት ፡
ቀይ ፡ ሥር ፡

13 ቅባት፡የሚወጣቸው፡ተክሎች፡

ወይራ ፡
ጉሎ ፡
እንኮይ ፡
ዶቅማ ፡
ጥጥ ፡

14 ማር ፡

ሰንበሌጥ ፡
ጎመጭ ፡
አክርማ ፡
አሰንዳቦ ፡
ስንደዶ ፡
ገጃዶ ፡
ሙጃ ፡
ቋቁቻ ፡
ጋገር ፡
ኮሳ ፡
ግቻ ፡
ሰርዶ ፡
ጎመጭ ፡
ውራ ፡
ቁጠማ ፡

15 የሚሸቱ ፡ ቅጠሎች ፡

አደስ ፡
ከሴ ፡
ጭቁኝ ፡
አጡምበር ፡

እንስሳት ፡

1 በየብስ ፡ የሚኖሩ ፡

(ሀ) የቤትና ፡ የዱር ፡

ዝሆን ፡
አንበሳ ፡
ቀጭኔ ፡
ጎሽ ፡
አውራሪስ ፡
ግስላ ፡
ነምር ፡
ዥብ ፡
ድብ ፡
ደልጋ ፡ አንበሳ ፡
እሪያ ፡ ( ከርከሮ ) ፡
ዝንጀሮ ፡
ጦጣ ፡
ጉሬዛ ፡
ቀበሮ ፡

ተኩላ ፡ ( የዱ ) ፡
አጋዘን ፡
ድኵላ ፡
ሚዳቋ ፡
ጥንቸል ፡
ሰስ ፡
የሜዳ ፡ ፍየል ፡
ቤሮ ፡ ( አፍን ) ፡
( ሸላ ) ፡ ምጥማጥ ፡
የሜዳ ፡ አህያ ፡
ሳላ ፡
ሽኮኮ ፡
ዦርት ፡
ዝባድ ፡ ( ጥርኝ ) ፡
ትግሪት ( ኤንሹ ) ፡
ብሖር ፡
አሣማ ፡
የሌሊት ፡ ወፍ ፡
ድፋርሳ ፡
ፌቆ ፡
አርጃኖ ፡
አነር ፡
ዋላ ፡
ፋሮ ፡
ዔሊ ፡
አራጅ ፡
ላም ፡
በሬ ፡
ፍየል ፡
በግ ፡
ፈረስ ፡
በቅሎ ፡
አህያ ፡
ውሻ ፡
ድመት ፡
ግመል ፡

ዘንዶ ፡ (በልብ ፡ የሚሳብ) ፡
እባብ ፡ (በልብ ፡ የሚሳብ)
እንሽላሊት ፡
ገበሎ ፡
ጊንጥ ፡
እስስት ፡
አይጥ ፡
ፍልፈል ፡
ናዜራ ፡
አይጠ ፡ መጎጥ ፡

(ለ) በልብ ፡ የሚሳቡ ፡ ትሎች ፡

ቅንቡርስ ፡
ቀንድ ፡ አውጣ ፡
አምሳ ፡ እግር ፡
አባ ፡ ጨጓሬ ፡
ተምች ፡ ( ጌይሪ ) ፡
ቆርድድ ፡

(ሐ) ጥቃቅን ፡ በራሪዎች ፡

ንብ ፡
ተርብ ፡
ጣዝማ ፡
ጥንዚዛ ፡
ቢራቢሮ ፡
ትንኝ ፡
ዝንብ ፡
የእሳት ፡ ራት ፡
ፌንጣ ፡
ዋኙንቢጥ ፡
ቅማል ፡
መዥገር ፡
ቁንጫ ፡
ትኋን ፡
ጉንዳን ፡
ቁጫጭ ፡
ዘመሚት ፡

ምሥጥ ፡
ቀጠጥና ፡
በረሮ ፡
በልበላ ፡
አንበጣ ፡
ነቀዝ ፡
ቅማንዥር ፡
ሞያሌ ፡

(መ) በክንፍ፡የሚበሩ፡አዕዋፍ፡

ቁሪያ ፡
ጨረባ ፡
የሎስ ፡ ( ግልገል ፡ አንሣ ) ፡
የመስቀል ፡ ወፍ ፡
አባ ፡ ቡሎ ፡
ቆቅ ፡
ዶሮ ፡
ሶረን ፡
ድርጭት ፡
ጋግርት ፡
ዝዩ ( ዳክዩ ) ፡
ፓሮት ፡
ጅብሪ ፡
ጉራማይሌ ፡
ጆፌ ፡ አሞራ፡(ጥንብ፡አንሣ)፡
ጎለጎል ፡
ሆድሆዱን ፡
አፈ ፡ ያሬድ ፡
ወንዘረጭ ፡
መነኵሲት ፡
ትኳረጥ ፡
ጭራ ፡ ረዥሜ ፡
ሲላ ፡ ( ጭላት ) ፡
የወንዝ ፡ አሙቴ ፡
ሻምላ ፡
ብቅበቃ ፡

ቀይ ፡ ይብራ ፡
ዥግርግሪት ፡
የገደል ፡ አሞራ ፡
ዥግራ ፡

2 በውኃ ፡ ውስጥ ፡ የሚኖሩ፡ እንስሳት ፡

አርጃኖ ፡
ዓሣ ፡ ዐንበሬ ፡
አቆስጣ ፡
አልቅት ፡
እንባዛ ፡
የውኃ ፡ እናት ፡
አዞ ፡
ጉማሬ ፡

3 በየብስና ፡ በውኃ፡ውስጥ ፡ የሚኖሩ ፡ እንስሳት ፡

መንቆራሪት ፡
ጓጉንቸር ፡
እባብ ፡
ዘንዶ ፡
ዔሊ ፡
ጊንጥ ፡

## ምዕራፍ ፡ ፳ ፡ የድርሰት ፡ አጻጻፍ ።

መግለጫ ፡

ድርሰት ፡ ባይን ፡ የታየውን ፡ በጆሮ ፡ የተሰማውንና ፡ አእምሮ ፡ የወለደውን ፡ አስተያየት ፡ በሥዕለ ፡ ቃላት ፡ አሳክቶና ፡ አስማምቶ ፡ የሚገለጽበት ፡ ጽሑፍ ፡ ነው ።

(ሀ) ድርሰትን ፡ ለመጻፍ ፡ የሚያስፈልጉ ፡ ነገሮች ፡ የሚከተሉት ፡ ናቸው ።

፩ ፡ አርእስትን ፡ መምረጥ ፡

፪ ፡ አርእስቱ ፡ በጠቅላላ ፡ ተገላጭ ፡ መሆኑንና ፡ አለመሆኑን ፡ ለይቶ ፡ ማወቅ ፡

፫ ፡ አስተዋጽኦ ፡ መንደፍ ፡
(ሀ) አሳብን ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ ወዲያው ፡ ማስቀመጥ ፡
(ለ) የተጻፉትን ፡ አስተዋጽኦች ፡ ቅደም ፡ ተከተል ፡ በጥንቃቄ ፡ ማሳካት ፡

፬ ፡ አርእስቱን ፡ መጠበቅ ፡
(ሀ) አንቀጾቹ ፡ ስለ ፡ አርእስቱ ፡ ብቻ ፡ እንዲያወሩ ፡ ማድረግ ፡
(ለ) አንቀጾቹ ፡ ርስ ፡ በርሳቸው ፡ እንዲያያዙ ፡ ማድረግ ፡

፭ ፡ በተቻለ ፡ መጠን ፡ አርእስቱን ፡ ለመግለጽ ፡ ሲሞክር ፡ የሚከተሉትን ፡ ነገሮች ፡ ማስታወስ ፡
(ሀ) ቃላትን ፡ በትክክል ፡ ማስገባት ፡
(ለ) ነጥቦችን ፡ በትክክል ፡ ማስገባት ፡
(ሐ) ድርሰቱን ፡ አንድ ፡ ተራ ፡ ሰው ፡ አንብቦ ፡ እንዲረዳው ፡ ከባድ ፡ በሆኑት ፡ ቃላት ፡ ከመሥራት ፡ መወሰን ፡

፮ ፡ ብርዕን ፡ ማጥራት ፡
(ሀ) ለሌሎች ፡ ግልጽ ፡ ሆኖ ፡ እንዲነበብ ፡ ማድረግ ፡
(ለ) ጽሕፈቱ ፡ ውበት ፡ እንዲያገኝ ፡ ማድረግ ፡

፯ ፡ አመጣጠን ፡

(ሀ) አንዱን ፡ ያለቅጥ ፡ አለማስረዘም ፡
(ለ) ሌላውን ፡ አንቀጽ ፡ እጅግ ፡ አድርጎ ፡ አለማሳጠር ፡

፰ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ የተገለጸውን ፡ ነገር ፡ አለመደጋገም ፡

፱ ፡ ከረዥሙ ፡ ባጭሩ ፡ የጻፍሁት ፡ ድርሰት ፡ --- አለማለትና ፡ --- እንደዚህ ፡ ይመስለኛል ፡ የሚባለውን ፡ ቃል ፡ ማሰሪያ ፡ አለማድረግ ፤ (መቍረጫ ፡ አለማድረግ) ፡

፲ ፡ በድርሰት ፡ ውስጥ ፡ ከብዛት ፡ ይልቅ ፡ አጠር ፡ ብሎ ፡ የተጻፈ ፡ ነገር ፡ ጣፋጭ ፡ መሆኑን ፡ ማሰብ ፡

## የድርሰት ፡ ዐይነቶች ፡ ዋኖቹ ፡ ሦስት ፡ ናቸው ።

፩ ፡ ሥዕላዊ ፡ ድርሰት ፡
፪ ፡ ተራኪ ፡ ድርሰት ፡
፫ ፡ አመዛዛኝ ፡ (የረቂቅ ፡ ነገር) ፡ ድርሰት ፡

## ፩ ፡ ሥዕላዊ ፡ ድርሰት ፡

### መግለጫ ፡

የተሰጠውን ፡ አርእስት ፡ ሁኔታ ፡ ዐይነቱን ፡ መልኩን ፡ ቅርጹን ፡ መኖሪያውን ፡ ልማዱንና ፡ ባሕርዩን ፡ ላንባቢው ፡ ግልጽ ፡ አድርጎ ፡ የሚያስረዳና ፡ በመጨረሻም ፡ የደራሲውን ፡ አሳብ ፡ የሚገልጽ ፡ ነው ።

ሥዕላዊ ፡ ድርሰት ፡ በ፪ ፡ ይከፈላል ።

### (ሀ) ገላጭ ፡

መልኩን ፡ ዐይነቱን ፡ ቅርጹንና ፡ አሠራሩን ፡ መኖሪያውን ፡ ልማዱንና ፡ ባሕርዩን ፡ ያስረዳል ፤ ለምሳሌ ፡ የሚከተሉትን ፡ ድርሰቶች ፡ ተመልከት ።

### በቅሎ ፡

በቅሎ ፡ አራት ፡ እግሮች ፡ ያላት ፡ የቤት ፡ ንስሳ ፡ ናት ። መልኳም ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ግራጫ ፡ ዋርዳ ፡ ሳሙና ፡ ሸክላ ፡ ቡላ ፡ ነው ። ጠንካራና ፡ አደጋ ፡ ቻይ ፡ በመሆኗ ፡ በቆላና ፡ በደጋ ፡ ትኖራለች ፤ ውኃ ፡ ከማይገኝበት ፡ አገር ፡ በቀር ፡ በሁሉ ፡ አገር ፡ ትኖራለች ። ነገር ፡ ግን ፡ በሰሜንና ፡ በደቡብ ፡ አርክቲክና ፡ አንታርክቲክ ፡ በሚባሉት ፡ አገሮች ፡ ውስጥ ፡ ቅዝቃዜው ፡ ከልክ ፡ ያለፈ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ለመገኘት ፡ አትችልም ። ጸጉራም ፡ ያልሆነ ፡ እንስሳ ፡ እዚያ ፡ ለመኖር ፡ ቍሩ ፡ አይፈቅድለትም ። ዘሯ ፡ ከስናርና ፡ ከባዝራ ፡ ወገን ፡ ነው ፤ ስናር ፡ አባቷ ፡ ሲሆን ፡ እናቷ ፡ ባዝራ ፡ ለመሆኗ ፡ የሚያጠራጥር ፡ ነገር ፡ የለም ።

መኖሪያዋ ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ በቤት ፡ ውስጥ ፡ ነው ። ሙቀት ፡ ወዳለበት ፡ ሥፍራ ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ እንድትጠጋ ፡ የምትገደድበት ፡ ምክንያት ፡ ግልጽ ፡ ነው ፤ ቆዳዋና ፡ ሥጋዋ፡

ለስላሳና ፤ ሥሥ ፡ ስለ ፡ ሆነና ፡ ብርድን ፡ ለመቋቋም ፡ ስለማይችል ፡ ከላይ ፡ ከጸጉ፡ ከጎ ንና ፡ ከጎን ፡ መከታ፡ ያለበትን፡ ሥፍራ፡ ዘወትር ፡ ስትፈልግ፡ ትገኛለች። ቆዳዋ፡ ሥሥ፡ ከመሆኑ ፡ የተነሣ ፡ እዚህ ፡ ይግባ ፡ የማይባል ፡ አንጋሬ ፡ የማይወጣው ፡ ሳይገፈፍ ፡ ከኑ ጥንቡ ፡ አብሮ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የሚጣል ፡ ሆኗል ። ስለዚህ ፡ ሙቀት ፡ የሚያስፈልጋት ፡ ከቀንድ ፡ ከብት ፡ ተለይታ ፡ በቤት ፡ ውስጥ ፡ የምታድር ፡ ሆናለች ።

ምግቧ ፡ በጠቅላላ ፡ ማርና ፡ ውኃ ፡ ነው ። ከመስክ ፡ ላይ ፡ ወይም ፡ ከማናቸውም ፡ ሥፍራ ፡ ግጦሽ ፡ ከሚገኝበት ፡ ቦታ ፡ ስትግጥ ፡ ከዋለች ፡ በኋላ ፡ ሲመሽ ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ትሰበሰባለች ። በምትኖርበት ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ልዩ ፡ ሥፍራ ፡ ጋጣ ፡ የሚባል ፡ አላት ። በዚያ ፡ በጋጣዋ ፡ ውስጥ ፡ ደግሞ ፡ ድርቆሽና ፡ ጥራጥሬ ፡ የሆነ ፡ ነገር ፡ ምግቧ፡ የሚዘጋ ጅበት ፡ አለ ፤ እንግዲህ ፡ እንደዚች ፡ ያሉችው ፡ እንስሳ ፡ በልታ ፡ የማትጠግብ ፡ ከሆነ ፡ ክፍሏ ፡ ጋማ ፡ ካላቸው ፡ እንስሳት ፡ ጋራ ፡ ነው ።

ይህች ፡ እንስሳ ፡ ለመውለድ ፡ የማትችል ፡ ማሕፀኗ ፡ የደረቀ ፡ ነው ። ወንዱም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ ሴቷ ፡ በቅሎ ፡ አባለ ፡ ዘር ፡ አላቸው ። ብቻውን ፡ ያረረ ፡ ፍሬ ፡ የማያ ፈራ ፡ ነው ። እንደዚህ ፡ ተጽፎ ፡ ሲገኝ ፡ ግንኙነት ፡ የላቸውም ፡ መባሉ ፡ አይደለም ። ለመዋለድ ፡ አለመቻላቸውን ፡ ለማስረዳት ፡ ነው፡ እንጂ ፤ እንደዚች ፡ ያለችው ፡ እንስሳ፡ ወልዳና ፡ አጥብታ ፡ ካላሳደገች ፡ ጎዶሏ ፡ የማይቀነስ፡ እንስሳ ፡ ናት ።

### ንብ ፡

የንብ ፡ አካላት ፡ አሠራር ፡ ዕፁብ ፡ ድንቅ ፡ ነው ። አካላቷ ፡ በሦስት ፡ ክፍል ፡ ይከ ፈላል ፤ ባንደኛው ፡ ክፍል ፡ የምታሸትበትና ፡ የምትዳስስበት ፡ የምትሰማበትም ፡ በግ ንባሯ ፡ በስተቀኝና ፡ በስተግራ ፡ ሁለት ፡ ቀጫጭን ፡ ነገሮች ፡ እንደ ፡ ቀንድ ፡ የሆኑ፡ አሏት ። ዳግም ፡ በዚህ ፡ በገጿ ፡ ላይ ፡ ሁለት ፡ ትልልቅ ፡ ጠፍጣፋ ፡ ዐይኖች ፡ በግራና ፡ በቀኝ ፡ ሆነው፡ ለማየት ፡ የሚያስችሏት፡ በሌሎች፡ ትንንሽ ፡ ዐይኖች፡ የተመሉ ፡ አሏት።

በሁለተኛው ፡ ያካላት ፡ ክፍሏ ፡ ጸጉራሞች ፡ የሆኑ ፡ ባበባ ፤ ውስጥ ፡ ያለውን ፡ ኔክታር ፡ (ፈሳሽ ፡ ነገር ) ፡ ስትመጥ ፡ ያበባ ፡ ዱቄት ፡ የምታመጣባቸው ፡ ስድስት ፡ እግ ሮች ፡ ሁለት ፡ ወፈር ፡ ያሉ ፡ ክንፎችና ፡ ሌሎች ፡ ሁለት ፡ ሣሣ ፡ ያሉ ፡ ክንፎች ፡ በጠን ካሮች ፡ ሥር ፡ የሆኑ ፡ አሏት ።

በሦስተኛው ፡ የአካላት ፡ ክፍሏ ፡ እንደ ፡ አንጓ ፡ ክርክር ፡ ያላቸው ፡ መተንፈሻ ዎች ፡ የምትነድፍበትና ፡ የተበላሸውን ፡ የምታስወጣበት ፡ አሏት ።

(ሀ) <u>አሳብ ፡ ሰጭ ፡</u>

መልኩ ፡ ዐይነቱ ፡ ቅርጹና ፡ አሠራሩ ፡ ከተነገረ ፡ በኋላ ፡ ደራሲው ፡ አስተያየ ቱን ፡ የሚሰጥበት ፡ ድርሰት ፡ ነው ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ለብቻው ፡ ይሰጣል ፤ ለምሳሌ፡ የሚከተሉትን ፡ ድርሰቶች ፡ ተመልከት ።

## የበቅሎ ፡ አገልግሎትና ፡ ጠባይ ፡

በቅሎ ፡ ጠንካራና ፡ አደጋ ፡ ቻይ ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ ዋና ፡ ለሰው ፡ አገልግሎት ፡ የምትሆን ፡ የቤት ፡ እንስሳ ፡ ነች ። እግዚአብሔር ፡ ለሰው ፡ ሁሉን ፡ ግዛ ፡ ብሎ ፡ ሥልጣን ፡ ስለ ፡ ሰጠው ፡ ይህችን ፡ ጉልበታም ፡ እንስሳ ፡ በልጓም ፡ ገዝቶና ፡ አለዝቦ ፡ ያኖራታል ። ከባድ ፡ ጭነት፡ ተጭና ፡ ረዥም፡ በረሃ፡ ቆርጣ፡ ስለምትሄድ ፡ በጣም ፡ ብርቱ ፡ ጠቃሚ፡ እንስሳ ፡ ናት ። መኪናም ፡ በሌለበት ፡ ወይም፡ በማይገባው ፡ አገር ፡ ለጭነት ፡ ብቻ፡ ሳይሆን ፡ ሰዎችንም ፡ ወደ ፡ ፈቀዱበት፡ አገር ፡ በዠርባዋ፡ ወድላ ፡ ታዘዋውራቸዋለች ።

ዐመሏ ፡ ከማንም ፡ የማይስማማ ፡ አስቸጋሪ ፡ በመሆኑ ፡ የሚያዝንላትና ፡ የሚራራላት ፡ የለም ። እርሷም ፡ በተመቻት ፡ ጊዜ ፡ ረግጣ ፡ ጥላ ፡ ለማጉላላት ፡ አትመለስም ። ስለዚህ ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ባጠገቧ ፡ ታከው ፡ ለማለፍ ፡ አይፈቅዱም ። በቅሎ ፡ ለጌታዋ ፡ ታማኝ ፡ አይደለችም ፡ እየተባለ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ሲተረክ ፡ ይኖራል ። ፈናጥ ፡ ፈናጥባይ ፡ መሆኗን ፡ የገዛ ፡ ግብሯ ፡ ይመሰክርባታል ።

የበቅሎ ፡ ባሕርይ ፡ ክፉ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሰው ፡ አያዝንላትም ፡ ተብሏል ። ይሁን ፡ እንጂ ፡ በውድም ፡ ሆነ ፡ በግድ ፡ ከተያዘች ፡ በኋላ ፡ (ከተጫኘች ፡ በኋላ) ፡ ከባድ ፡ ጭነት፡ ተሸክማ ፡ አስፈላጊውን ፡ መንገድ ፡ ቆርጣ ፡ እንደምትሄድና ፡ ሰዎችን ፡ እየተሸከመች ፡ እፈቀዱበት ፡ ሥፍራ ፡ እንደምታደርሳቸው ፡ ተነግሯል ። ስለዚህ ፡ በክፋቷ ፡ ከምታመጣው ፡ ጉዳት ፡ ይልቅ ፡ በጉልበቷ ፡ የምትሰጠው ፡ አገልግሎት ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሰዎች ፡ በበለጠ ፡ ዋጋ ፡ እየገዙ ፡ በፈቀዱበት ፡ ቦታ ፡ ያስቀምጧታል ።

እንግዲህ ፡ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ጥቅም ፡ የምትሰጥ ፡ ከሆነ ፡ መልካም ፡ የሚሞቅ ፡ ቤት ፡ እየሠሩና ፡ ጉልበት ፡ የሚሰጣትን ፡ ምግብ ፡ እየሰጡ ፡ ውኃም ፡ በደንበኛው ፡ ሰዓት ፡ እያቀረቡላትና ፡ ቤቷንም ፡ እየጠረጉ ፡ ሊጠነቀቁላት ፡ ያስፈልጋል ።

## የንብ ፡ ጥቅምና ፡ ጥንቃቄ ፡

ንብ ፡ ለሰው ፡ ጠቃሚ ፡ የሆነች ፡ ትንሽ ፡ ፍጥረት ፡ ናት ። በብዙ ፡ ትግል ፡ ወዲህና ፡ ወዲያ ፡ ብላ ፡ የሚያስፈልጋትን ፡ የማር ፡ አበባ ፡ ሰብስባ ፡ ደንበኛውን ፡ ማር ፡ ሠርታ ፡ ያለውድ ፡ በግድ ፡ ለሰው ፡ ታስረክባለች። የማር ፡ አበባን ፡ ስትቀሥም ፡ ሴቴና ፡ ወንዴ ፡ የሆኑትን ፡ አበቦች ፡ በእግሮቿ ፡ የአበባ ፡ ዱቄትን ፡ እየወሰደች ፡ እንዲያፈሩ ፡ ታገናኛቸዋለች ። እንዲያውም ፡ ከማርም ፡ ይልቅ ፡ የበለጠ ፡ ጥቅም ፡ የምትሰጥበት ፡ መንገድ ፡ ይህ ፡ ነው ።

ንብ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ ማርን ፡ ለሰው ፡ ብላ ፡ ባትሠራ ፡ ሰው ፡ ለራሷ ፡ ብላ ፡ ከሠራችው ፡ በግድም ፡ ሆነ ፡ በውድ ፡ መውሰዱ ፡ ካልቀረ ፡ ለንብ ፡ የሚያስፈልጋትን ፡ ጥንቃቄ ፡ በሙሉ ፡ እንኳ ፡ ባይሆን ፡ ከሞላ ፡ ጎደል ፡ እየፈጸሙ ፡ ሊደክሙበት ፡ ይገባል ። ንብ ፡ ብዙ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ አበቦች ፡ ያሉበትንና ፡ ለመኖሪያዋ ፡ ሞቃት ፡ የሆነውን ፡ ቦታ ፡ ስለምትፈቅድ ፡ በመልካም ፡ አትክልት ፡ ውስጥ ፡ እያስገቡ ፡ መስቀል፡ ( ማስቀመጥ ) ፡ ያስፈልጋል ።

አንድ ፡ ሠራተኛ ፡ የሚሠራበትን ፡ መሣሪያና ፡ የሚሠራውን ፡ ሥራ ፡ አሠሪው፡ ካላዘጋጀለት፡ ለባለቤቱ፡ አጥጋቢ፡ ነገርን፡ ለመሥራት፡ አይችልም። እንደዚሁም፡ ሁሉ ፡ ንብ ፡ የሚያስፈልጋትን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ካላደረጉላት ፡ በቂ ፡ ማርን ፡ አትሠራም ፡ (አትሰጥም) ። ስለዚህ ፡ አናቢ ፡ የንብን ፡ ኑሮ ፡ የሚያሻሽልበትን ፡ ዘዴ ፡ እየፈለገና ፡ እያጠና ፡ ሊሠራ ፡ ግዴታ ፡ ነው ።

## ሥዕላዊ ፡ ድርሰት ፡ ወይም ፡ መስተዋታዊ ፡ ድርሰት ፡

ሥዕላዊ ፡ ድርሰት ፡ ገላጭንና ፡ አሳብ ፡ ሰጪን ፡ ባንድነት ፡ ይይዛል። ስለዚህ ፡ የሚከተሉትን ፡ ድርሰቶች ፡ ተመልከት ።

## ትምህርት ፡

ትምህርት ፡ ሰውነታችንንና ፡ አእምሯችንን ፡ በመልካም ፡ አኳኋን ፡ እየጠበቀ ፡ የሚያሳድግ ፡ ሞግዚታችን ፡ ነው ። ትምህርት ፡ ባራት ፡ ትልልቅ ፡ ክፍሎች ፡ ይከፈላል ። እነርሱም ፡ የሰውነት ፡ ማጠንከሪያ ፡ ትምህርት ፡ መንፈሳዊ ፡ ትምህርት ፡ ያንጎልና ፡ የግብረ ፡ ገብነት ፡ ትምህርቶች ፡ ናቸው ።

የሰውነት ፡ ማጠንከሪያ ፡ ትምህርት ፡ ሰውነታችን ፡ ላልቶና ፡ ተዝለፍልፎ ፡ ሥራን ፡ መሥራት ፡ እንዳያቅተው ፡ ዥማቶቻችንን ፡ ጡንቶቻችንንና ፡ ዐጥንቶቻችንን፡ ደኅና ፡ አድርጎ ፡ እያፍታታና ፡ እያበረታታ ፡ ኀይልን ፡ እንዲያገኙ ፡ የሚያስተምረን ፡ ትምህርት ፡ ነው ። የሰውነት ፡ ማጠንከሪያ ፡ ትምህርት ፡ በእንግሊዝኛ ፡ ጅምናስቲክ ፡ ይባላል፤ ባማርኛም ፡ ያልተለመደ ፡ አይደለም ። የጅምናስቲክ ፡ ትምህርት ፡ ብዙ ፡ ልዩ፡ ልዩ ፡ የሆኑ ፡ ንኡሳን ፡ ክፍሎች ፡ አሉት ። ለጊዜው ፡ ለምሳሌ ፡ የሚሆኑንን ፡ እንጠቅሳለን ፡ እንጂ ፡ ሁሉንም ፡ አንዘረዝራቸውም ። ከእነርሱም ፡ ውስጥ ፡ ዋናዎቹ ፡ የኳስ ፡ ጨዋታ ፡ ዝላይ ፡ ሩጫ ፡ ትግል ፡ ቡጢ ፡ (ቦክስ) ፡ ውኃ ፡ ዋና ፡ አደን ፡ እሽቅድምድም ፡ ገና ፡ ጉግስና ፡ ጊጤን ፡ የመሰሉ ፡ ናቸው ። አንድ ፡ ልጅ፡ እነዚህን ፡ ጫወቶች ፡ እለምድ፡ ሲል ፡ (እማር ፡ ሲል) ፡ ከቀን ፡ ብዛት ፡ ሰውነቱን ፡ እያሻሻለው ፡ ይሄዳል ። ጅምናስቲክን ፡ በትምህርት ፡ ቤት ፡ ከደንበኛ ፡ አስተማሪ ፡ በመቀበልና ፡ ከትምህርት ፡ ቤት ፡ ውጭ ፡ ከባልንጀሮቻችን ፡ ጋራ ፡ በመጫወት ፡ (በመሥራት) ፡ እንማረዋለን ። ጅምናስቲክን ፡ ከመሥራት ፡ ብንቦዝን ፡ ግን ፡ ሰውነታችንን ፡ አፍዝዘን ፡ ለበሽታ ፡ ማረፊያ ፡ የተዘጋጀን ፡ መሆናችንን ፡ ማወቅ ፡ አለብን ።

መንፈሳዊ ፡ ትምህርት ፡ማን ፡ እንደ፡ ፈጠረን፡ ለምን፡ እንደ ፡ ተፈጠርን፡ እንዴት፡ እንደምናምነውና ፡ ካመነውም ፡ በኋላ ፡ ምን ፡ ማድረግ ፡ እንደሚገባን ፡ የሚያስተምረን ፡ ትምህርት ፡ ነው ። በዚህ ፡ ዓለም ፡ ብዙ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ እምነቶች ፡ አሉ ። እነሱም፡ ክርስቲያንነት ፡ መሐመዳዊነት ፡ አይሁዳዊነት ፡ ቡድሃዊነትና፡ ኮንፊሽናዊነት፡ ናቸው። እነዚህም ፡ ደግሞ ፡ በንኡሳን ፡ ክፍሎች ፡ ይከፈላሉ ፡ (ይተነተናሉ) ። አሁን ፡ ከነዚህ ፡ ውስጥ፡ አንዱን፡ ለብቻው፡ነጥለን፡ አንዘረዝረውም፤ በጠቅላላ፡ ስንገምተው፡ እያንዳንዱ፡

ሃይማኖት ፡ ሰውን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ከአምላኩ ፡ ጋራ ፡ የሚያስታርቀው ፡ ትምህርት ፡ መሆኑን ፡ በቅን ፡ ልቦናችን ፡ እንገነዘበዋለን። የኔ፡ የራሴ ፡ ሃይማኖት ፡ ክርስቲያን፡ ስለ፡ ሆነ፡ ከተጠቀሱት ፡ ሃይማኖቶች ፡ ውስጥ ፡ ክርስቲያንነት ፡ ብቻ፡ ከእግዚአብሔር፡ እንደ ሚያስታርቅ ፡ አምናለሁ። መንፈሳዊ፡ ትምህርት ፡ ከወላጆቻችን ፡ ከመንፈሳውያን፡ትም ህርት፡ ቤቶችና፡ ከመመራመር ፡ እንማረዋለን። ስለዚህ ፡ መንፈሳዊ፡ ትምህርት፡ ሰውን፡ ከክፉ ፡ ሥራ ፡ እንዲወገድ ፡ እያደረገ ፡ ወዳምላኩ ፡ እንዲጠጋ ፡ የሚሰበው ፡ መሆኑን ፡ የማያምን ፡ ሰው ፡ የለም ።

ያንጎል ፡ ትምህርት ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ነገሮችን ፡ በአእምሯችን ፡ እያየንና ፡ እያመዛ ዘን ፡ እንድንሠራ ፡ የሚያስተምረን ፡ ነው ። ባንጎል ፡ የምንማራቸው ፡ ትምህርቶች ፡ አስ ቸጋሪዎች ፡ ከመሆናቸው ፡ የተነሣ ፡ በጣም ፡ እየተመራመርን ፡ (እየተራቀቅን)፡ እንድና ስብ ፡ ያስገድዱናል።ከአእምሮ ፡ ትምህርት ፡ ውስጥ ፡ ለምሳሌ ፡ የሚሆኑትን ፡ ሒሳብን ፡ መሐንዲስነትን ፡ ሥዕልን ፡ ቋንቋን ፡ ቍጥርን ፡ ሙዚቃን ፡ መካኒክን ፡ የነገር፡ አመጣጥ ንና ፡ አካሄድን፡ የመሳሰሉትን ፡ ሁሉ ፡ እንጠቀልላለን ። እንግዲህ ፡ የአእምሮን ፡ ትምህ ርት ፡ ከደንበኛ ፡ ትምህርት ፡ ቤት፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሥነ፡ ፍጥረታት፡ ከመመልከትና፡ መጻሕፍትን ፡ ከመመርመር ፡ የተነሣ ፡ እንማረዋለን ። የአእምሮ ፡ ትምህርት ፡ አንድ ፡ ነገርን ፡ ባንጎላችን ፡ ቀርጸን ፡ ሊሠራ ፡ እንደሚገባው ፡ አድርገን ፡ መሥራት ፡ እንዳለ ብን ፡ የሚያስተምረን ፡ ትምህርት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ማወቅ ፡ አለብን ።

ግብረ ፡ ገብነት ፡ ሰው፡ የመባልን ፡ መብት ፡ (ክብር)፡ እንድንጠብቅ ፡ ዐመላች ንን ፡ ከቀን፡ ወደ፡ቀን ፡ እያሻሻልን ፡ መኖርን ፡ የሚያስተምረን፡ ትምህርት ፡ ነው። ግብረ፡ ገብነት ፡ በጠቅላላ ፡ የዓለም ፡ ልጆች ፡ በሐሳብ ፡ እየተግባቡ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ እንዲረ ዳዱ ፡ የሚያስተምራቸው ፡ ትምህርት ፡ ነው ። የግብረ ፡ ገብነት ፡ ትምህርት ፡ የሰውን ፡ ገንዘብ ፡ መፈለግን ፡ የቅናትን ፡ የምቀኝነትንና ፡ የጭካኔን ፡ መንፈስ ፡ አጥብቆ ፡ እየተቃ ወመ ፡ በጎ ፡ አድራጎትን ፡ የሚያስተምር ፡ ነው ። ግብረ ፡ ገብነት ፡ ችግርና ፡ መከራ ፡ በሰው ፡ ልጅ ፡ ላይ ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ በትዕግሥት ፡ ተቀብሎና ፡ አስተናግዶ ፡ መሸኘት፡ እንደሚገባ ፡ ይነግራል ፤ ስለዚህ ፡ ሃይማኖት ፡ ግብረ ፡ ገብነትን ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡ ከመሥ ራት ፡ አያግደውም ።

የሰው ፡ ልጅ ፡ በውነተኛው ፡ ነገር ፡ ተማረ ፡ ተብሎ ፡ ሊገመት ፡ የሚገባው ፡ በሰ ውነቱ ፡ በመንፈሳዊነቱ ፡ በአእምሮውና ፡ በግረ ፡ ገብነቱ ፡ ጎልምሶ ፡ ትክክለኛውን ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት ፡ የቻለ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ነው ። ባሁኑ ፡ ዘመናችን ፡ አብዛኞቹ ፡ ያዳም ፡ ልጆች ፡ በሰውነትና ፡ በአእምሮ፡ ፋፍተው ፡ በመንፈሳዊነትና ፡ በግብረ ፡ ገብነት፡ ጫጭ ተው ፡ ስለ ፡ ቀሩ ፡ ጤና ፡ ከማጣታቸው ፡ የተነሣ ፡ በጣም ፡ ተቆፍሮ ፡ ያልተተከለውን ፡ ማማ ፡ ነፋስ ፡ እንደሚያዋዥቀው ፡ ሁሉ ፡ ዓለምን ፡ ያዋዥቁታል ። እንግዲህ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ በትምህርት ፡ ጕድለት ፡ ሲገኝበት ፡ ጤና ፡ የማያገኝ ፡ ከሆነ ፡ አራቱንም ፡ ትምህ ርቶች ፡ በየአግባባቸው ፡ እየተማረ ፡ እያስማማና ፡ እያዋሐደ ፡ እንዲይዛቸው ፡ የግዴታ ፡ አስፈላጊ ፡ መሆናቸውን ፡ ማወቅ ፡ አለብን ።

## ነፋስ ፡

ነፋስ ፡ ባይን ፡ የማይታይ ፡ በእጅ ፡ የማይዳሰስ ፡ ሲነፍስ ፡ ስሜቱ ፡ ለፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ የሚሰማ ፡ ነው ። በቀሩት ፡ ግብሮቹ ፡ ከሚዳሰሱት ፡ ነገሮች ፡ ምንም ፡ ያህል ፡ አይለያይም። ይህ ፡ በራሪ ፡ አየር ፡ ተለይተው፡ ከታወቁት ፡ አየሮች ፡ ከኩሬና ፡ ከሐይቅ ፡ ከባሕርና ፡ ከፈሳሾች ፡ ለፀሐይ ፡ ኀይል ፡ ተነሥቶ ፡ ባየር ፡ ውስጥ ፡ ከሚዘዋወረው ፡ እንፋሎት ፡ ከትክልት ፡ ርግፍጋፊ ፡ ካቧራ ፡ ባየር ፡ ውስጥ ፡ ከሚገኙት ፡ ከጥቃቅን ፡ ነገ ሮችና ፡ ከትናንስ ፡ ተባዮች ፡ ይመሠረታል ። ነፋስ ፡ ሲነፍስ ፡ ረቂቅ ፡ ነገር ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ ዕፀዋትን ፡ ደመናትን ፡ ጢስንና ፡ ዐቧራን ፡ ወዲህና ፡ ወዲያ ፡ ሲያከለፈልፋቸው ፡ ይታ ያል ። ስለዚህ ፡ የነፋስ ፡ ሥራው ፡ እንጂ ፡ ራሱ ፡ ጎልቶ ፡ ለኛ ፡ አይታይም ።

ነፋስ ፡ መሬት ፡ በመዞሯ ፡ ምክንያትና ፡ ፀሐይ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ሥፍሮችን ፡ በመ ምታቷ ፡ የነዚህም ፡ ሥፍሮች ፡ የሙቀት ፡ አቀባበል ፡ ደረጃቸው ፡ የተለያየ ፡ በመሆኑ ፡ ይነፍሳል ፤ ፀሐይ ፡ በጎድጓዶች ፡ በረባዶችና ፡ በሸለቆች ፡ ሥፍሮች፡ ላይ ፡ የሙቀቷን ፡ ኀይል ፡ ስትጥልባቸው ፡ ሌሊቱን ፡ ቀዝቅዞ ፡ ያደረው ፡ አየር፡ እየሞቀ ፡ ይነሣል። በየደጋ ምቹና ፡ በየተራሮቹ ፡ ያደረው ፡ አየር ፡ ግን ፡ የዚያን ፡ ያህል ፡ ሙቀት ፡ ስለሚያገኝ ፡ የነርሱን ፡ ቦታ ፡ ለመያዝ ፡ ቁልቁል ፡ ይሽቀዳደማል ፡ የተጠቀሱት ፡ ቦታዎች ፡ እኩል ፡ ሙቀት ፡ የማያገኙበት ፡ ምክንያት ፡ ጎድጓዶቹ ፡ ሸለቆቹና ፡ ረባዶቹ ፡ መሬቶች ፡ ግል ብጥ ፡ ሆነው ፡ ስለሚበታትኑት ፡ ነው ። እንደዚሁም ፡ መሬትና ፡ ባሕር ፡ ከፀሐይ ፡ ሙቀ ትን ፡ ባንድ ፡ ፀይነት ፡ ደረጃ ፡ አይቀበሉም ። መሬት ፡ ፈጠን ፡ ብላ ፡ ተቀብላ ፡ ፈጠን ፡ ብላ ፡ ትለቃለች ፤ ባሕር ፡ ግን ፡ ሲቀበልም፡ ሲለቅም ፡ ይዘገያል። በዚሁም ፡ ላይ ፡ ባሕር፡ ከመሬት ፡ ሦስት ፡ እጅ ፡ ስለሚበልጥ ፡ በብዛቱ ፡ ልክ ፡ ሙቀትን ፡ ይቀበላል ። ስለዚህ ፡ የነዚህ ፡ የሁለቱ ፡ ልዩነት ፡ ደግሞ ፡ ነፋስን ፡ ወዲህና ፡ ወዲያ ፡ እንዲል ፡ ያስገድደዋል ።

ነፋስ ፡ የሚመጣበትን ፡ አቅጣጫ ፡ እየወረሰ ፡ በዚያው ፡ ስም ፡ ይጠራል ። የነ ፋስ ፡ ዐይነቶች ፡ ሦስት ፡ ናቸው ። እነርሱም ፡ ሙቅ ፡ መካከለኛና ፡ ቀዝቃዛ ፡ ነፋሳት ፡ ናቸው ። ሙቅ ፡ ነፋስ ፡ ካጋማሽ ፡ መሥመር ፡ ይነሣል ። ሽቅብ ፡ እየነፈሰ ፡ ወደ ፡ መካከ ለኛውና ፡ ወደ ፡ ቀዝቃዛው ፡ መካናተ ፡ ነፋሳት ፡ ይሄዳል ። መካከለኛውም ፡ ነፋስ ፡ ወደ፡ ላይ ፡ ሽቅብ ፡ እየነፈሰ ፡ ወደ ፡ ግራውና ፡ ወደ ፡ ቀኝ ፡ ወይም ፡ ወደ ፡ ደቡብና ፡ ወደ፡ ሰሜን፡ ይነፍሳል። ቀዝቃዛው ፡ ነፋስ ፡ ግን ፡ ከሰሜንና ፡ ከደቡብ ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ወገብ፡ ይነፍሳል ፤ አንዳንዶቹ ፡ በዚያው ፡ በደንበኛው፡ ጊዜያቸው ፡ ይነፍሳሉ ።

ነፋስ ፡ ለሰው ፡ ልጅ ፡ ለእንስሳትና ፡ ላትክልት ፡ ይጠቅማል ። ባንድ ፡ ዐይነት ፡ አስተያየት ፡ እነዚህ፡ የተጠቀሱት ፡ ፍጥረቶች ፡ ያለዝናም ፡ ወይም ፡ ያለውኃ ፡ ለመኖር ፡ አይችሉም ። በእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ ነፋስ ፡ በሙቀት ፡ ኀይል ፡ ካየሩ ፡ ላይ ፡ የሚነ ሣውን ፡ ውኃ ፡ ባየሩ ፡ ላይ ፡ እየነዳና ፡ እየወሰደ ፡ እንዲዘንምላቸው ፡ ያደርገዋል ። በዚህ፡ አኳኋን ፡ ነፋስ ፡ በርጥበት ፡ አብቅለውና ፡ በሙቀት ፡ ኀይል ፡ እንዲያበስሉ ፡ ይደግፋቸ

ዋል ። ለሰው ፡ ልጅ ፡ በተለይ ፡ የሥራ ፡ ረዳቱ ፡ ነው ። አዝርዕት ፡ እንዲያድጉለትና ፡ በደረሱም ፡ ጊዜ ፡ በውቂያ ፡ ላይ ፡ ምርቱ ፡ ከገለባው ፡ እንዲለይለት ፡ ያደርግለታል ። ያላንዳች ፡ ሥጋትም ፡ አይሮፕላን ፡ ባየር ፡ ውስጥ ፡ እንዲበር ፡ ይረዳል ። ላትክልትም ፡ አንደኛ ፡ ሴቴንና ፡ ወንዴን ፡ አበቦች ፡ እያጋባ ፡ እንዲራቡ ፡ ያደርጋቸዋል ። ሁለተኛ ፡ ጥቅጥቅ ፡ ባለ ፡ ጫካ ፡ ውስጥ ፡ የፀሐይን ፡ ብርሃን ፡ ለማግኘት ፡ የማይችሉትን ፡ አትክልት ፡ ባጠገባቸው ፡ የሚገኙትን ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ እያላጋ ፡ የፀሐይን ፡ ሙቀት ፡ ከነጨረሯ ፡ እንዲያገኙ ፡ ያግዛቸዋል ። በዚያውም ፡ ላይ ፡ ይህን ፡ በሚያደርግበት ፡ ጊዜ ፡ በጠቅላላ ፡ ለዕፀዋት ፡ ብርታትን ፡ ይሰጣቸዋል ። ለደማውያን ፡ እንስሶች ፡ ሽማ ፡ በየፈርጁ ፡ ይለበሳል ፡ እንደሚባለው ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ስልት ፡ ይጠቅማቸዋል ። አንዳንዶቹ ፡ እንስሶች ፡ በተለይ ፡ የማሽተት ፡ ስጦታ ፡ ስላላቸው ፡ ከሩቅ ፡ ምን ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ መጣባቸው ፡ ወይም ፡ ምን ፡ እንደ ፡ መጣላቸው ፡ ይነግራቸዋል ።

ነፋስ ፡ የሚሰጠው ፡ ጥቅም ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ ስንል ፡ የሚያመጣውን ፡ ጉዳትና ፡ ዋዬታ ፡ ሳናነሣው ፡ አናልፍም ። በመሬት ፡ ላይ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ድኃ ፡ ሆነ ፡ ወይም ፡ ሀብታም ፡ በብዙ ፡ ዓመታት ፡ ውስጥ ፡ አጠራቅሞ ፡ ለፍቶ ፡ የሠራውን ፡ ቤት ፡ በጥቂት ፡ ደቂቆች ፡ ውስጥ ፡ ነቅሎ ፡ ወስዶ ፡ ወዳንድ ፡ ቦታ ፡ ላይ ፡ ይጥለዋል ፤ ወይም ፡ ብትንትኑን ፡ ያወጣዋል ።

በአየር ፡ ውስጥ ፡ ቀኑን ፡ ጉም ፡ በሸፈነው ፡ ጊዜ ፡ በተራራ ፡ አጠገብ ፡ የሚወጣውና ፡ የሚወርደው ፡ ነፋስ ፡ አይሮፕላንን ፡ ቁልቁል ፡ በሚወርድበት ፡ ጊዜ ፡ ስቦ ፡ ከተራራ ፡ ጋራ ፡ ወይም ፡ ከመሬት ፡ ጋራ ፡ ያጋጨዋል ። በባሕር ፡ ላይ ፡ ቢሆንም ፡ ጉም ፡ በለገተበት ፡ ቀን ፡ መርከቦች ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ እንዲጋጩ ፡ ወይም ፡ ከተራራ ፡ ጋራ ፡ እንዲጋጩ ፡ ዋና ፡ ምክንያት ፡ ይሆንባቸዋል ። የባሕሩንም ፡ ውኃ ፡ ሽቅብ ፡ እየወረወረ ፡ ባነሣው ፡ ጊዜ ፡ ተመልሶ ፡ ማዕበሉ ፡ በመርከቦቹ ፡ ላይ ፡ ያርፍና ፡ ያሰጥማቸዋል ።

ቸሩ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሕያዋን ፡ ፍጥረታት ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ለሰው ፡ አስቦ ፡ እንዲያድር ፡ አእምሮ ፡ ሰጥቶታል ። እርሱ ፡ ካወቀበት ፡ አደጋ ፡ ከሚያመጡበት ፡ ነገሮች ፡ ሁሉ ፡ ለመራቅ ፡ ወይም ፡ መከላከያ ፡ ለማድረግ ፡ ይችላል ። ስለዚህ ፡ ሰው ፡ በነፋስ ፡ ግብር ፡ ካወቀበት ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ለመጠቀም ፡ ስለሚችል ፡ ከጉዳቱ ፡ ይልቅ ፡ ጥቅሙ ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ነው ።

## ፱ ፡ ተራኪ ፡ ድርሰት ፡ ወይም ፡ ዜናን ፡ አጎላማሽ ፡ ድርሰት ፡

### መግለጫ ፡

አንድ ፡ ነገር ፡ ወይም ፡ ድንገተኛ ፡ አደጋ ፡ የሆነበትን ፡ ጊዜ ፡ የተደረገበትን ፡ ቦታ ፡ ያመጣውን ፡ ጉዳትና ፡ ጥቅም ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ድረስ ፡ ያለውን ፡ ሐተታ ፡ እንደ ፡ ቀደምትነቱ ፡ ከመነሻው ፡ እያከታተለ ፡ (እያደራጀ) ፡ የሚሰጥ ፡ ነው ።

### ክፍል ፡ ፩ ፡ የባላገር ፡ ወጣቶች ፡ ኑሮና ፡ የእሳት ፡ አደጋ ፡

ለገሥና ፡ ከልክል ፡ የተወለዱባት ፡ አገር ፡ በሸዋ ፡ ጠቅላይ ፡ ግዛት ፡ በሰላሌ ፡ አውራጃ ፡ በሚዳ ፡ ወረዳ ፡ ውስጥ ፡ ዐመልሳ ፡ የምትባል ፡ ቀበሌ ፡ ናት ። ይህች ፡ ቀበሌ ፡ ቆላ ፡

ቀመስ ፡ ከመሆኗ ፡ በላይ ፡ ገደል ፡ ሸንተረር ፡ ሸለቆና ፡ ወንዛወንዝ ፡ የሞላባት ፡ ናት ።
ስለዚህ ፡ ያብዛኞቹ ፡ ገበሬዎች ፡ እርሻዎች ፡ በየገደሉ ፡ ጥግ ፡ በአንገች ፡ በደበደብና ፡
በፋልማ ፡ ስለ ፡ ነበሩ ፡ የለገሠና ፡ የከልክል ፡ ቤቶች ፡ እርሻዎችም ፡ ከተጠቀሱት ፡ ባን
ደኛው ፡ ወይም ፡ በሦስቱም ፡ ክፍል ፡ ውስጥ ፡ በመገኘታቸው ፡ በተወለዱ ፡ በሰባት ፡
ዓመታቸው ፡ ዐቀብ ፡ ቁልቁል ፡ ማለት ፡ ዠመሩ ። ምንም ፡ እንኳን ፡ የባላገር ፡ ኑሮ ፡ ብዙ
ውን ፡ ጊዜ ፡ አስደሳች ፡ መስሎ ፡ ባይታይ ፡ የባላገር ፡ ወጣቶች ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ለመሄድ ፡
አይፈቅዱም ፡ ነበር ። እንዲያውም ፡ አንዳንዶቹ ፡ በከተማው ፡ ኑሮ ፡ አላውቅበት ፡ እያሉ ፡
ሲመለሱ ፡ እያዩ ፡ ብዙዎቹ ፡ አይመኙትም ፡ ነበር ። ለገሠና ፡ ከልክል ፡ ግን ፡ የትምህርት ፡
ፍላጎት ፡ ስለ ፡ አደረባቸው ፡ በሕልማቸውም ፡ በውናቸውም ፡ የሚያስቡት ፡ ውጭ ፡ ውጭ
ውን ፡ ነበር ። ከሁሉም ፡ ነገር ፡ በጣም ፡ አድርጎ ፡ የሚያስደንቀው ፡ በዚያች ፡ ቀበሌ ፡
በትምህርታቸው ፡ ምክንያት ፡ የሚጠቀሙትን ፡ ሰዎች ፡ ሳያዩ ፡ እነዚህ ፡ ሁለት ፡ ወጣ
ቶች ፡ ለትምህርት ፡ መጓጓታቸው ፡ ነው ። እንዴት ፡ ከባልንጀሮቻቸው ፡ ጋራ ፡ ሆነው ፡
የሚጫወቷቸው ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ ዋና ፡ እንደ ፡ አደን ፡ ገና ፡ እንደ ፡ ጊጤ ፡ እንደ ፡ ምክክ
ቶሽ ፡ እንደ ፡ ትግልና ፡ እንደ ፡ ግርፊያ ፡ ያሉት ፡ ጫወቶች ፡ አላታለሏቸውም ፡ (ልባቸ
ውን ፡ አልማረኩም) ! ከነዚህ ፡ ጫወቶች ፡ በቀር ፡ ወጣቶቹ ፡ ዐቀብና ፡ ቁልቁል ፡ ሲሉ ፡
(ወደ ፡ ቆላ ፡ ሲወርዱና ፡ ወደ ፡ ደጋ ፡ ሲወጡ) ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ቀረርቶችን ፡ ያቅራሩና ፡ ልዩ ፡
ልዩ ፡ ዘፈኖችን ፡ ይዘፍኑ ፡ ነበር ፤ እነዚህስ ፡ እንዴት ፡ የሁለት ፡ ወጣቶችን ፡ አንጎል ፡ መለ
ወጥ ፡ (መሳብ) ፡ አቃታቸው !

በዚች ፡ ቀበሌ ፡ አዋሳኝ ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ ወንዝ ፡ ወንጭት ፡ የሚሉት ፡ አለ ።
ይህ ፡ ወንዝ ፡ ከፍ ፡ ከማለቱም ፡ የተነሣ ፡ አልፎ ፡ አልፎ ፡ በሠራቸው ፡ ባሕሮች ፡ ውስጥ ፡
ብዙ ፡ ትልልቅ ፡ ዓሦች ፡ ይገኛሉ ። ስለዚህ ፡ ያገሩ ፡ ተወላጆች ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ብር
ብራ ፡ እየጣሉ ፡ ይይዟቸዋል ። አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ደግሞ ፡ ብርብራ ፡ በተወደደበት ፡ ወራት ፡
ወደ ፡ ቆላ ፡ ወርደው ፡ የበደኖን ፡ (የጀሞን) ፡ ቅርፊት ፡ እየቀጠቀጡና ፡ በማር ፡ እያሠሩ ፡
ወስደው ፡ በወንዙ ፡ ላይ ፡ በእግራቸው ፡ ያሹታል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ዓሦች ፡ ሁሉ ፡ የበደ
ኖን ፡ ብርዝ ፡ እየጠጡ ፡ (እየሰመጠጡ) ፡ በውኃ ፡ ላይ ፡ ይንከፈረራሉ ፤ ዓሣ ፡ አጥማጆ
ችም ፡ የተንሳፈፉትን ፡ በመረብና ፡ በከረጢት ፡ ይለቅማሉ ። አንዳንዶቹም ፡ በውኃው ፡
መንደርደሪያ ፡ ላይ ፡ በቀኝና ፡ በግራ ፡ ድንጋዮችን ፡ እየካቡ ፡ የመረባቸውን ፡ ዋግንቦ ፡
በመካከል ፡ እያደረጉ ፡ ያጠምዷቸዋል ።

ከዕለታት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ለገሠና ፡ ከልክል ፡ ከዓሣ ፡ አጥማጆች ፡ ጋራ ፡ ዓሣ ፡ ሲያ
ጠምዱ ፡ ውለው ፡ መሸቶባቸው ፡ ዳቦት ፡ (ችቦ) ፡ አብርተው ፡ ወደ ፡ ቤታቸው ፡ ሲወጡ ፡
ወራቱ ፡ በጋ ፡ ነበርና ፡ የዳቦቱ ፡ እሳት ፡ ፍንጣሪ ፡ በመንገዱ ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ያሉትን ፡ ጫካ
ዎች ፡ አያያዛቸው ፡ (አቀጣጠላቸው) ። አዬ ፡ ጉድ ፡ (እንግዴህ ፡ እነዚህ ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡
ኋላ ፡ ይሂዱ ፡ ወይስ ፡ ወደ ፡ ፊት) ! ፡ በታላቅ ፡ ድንጋጤ ፡ ልባቸው ፡ ትር ፡ ትር ፡ ካለ ፡ በኋላ ፡
ልብ ፡ ገዝተው ፡ ቢመለከቱ ፡ ነፋሱ ፡ ወደ ፡ ታች ፡ መንፈሱን ፡ ትቶ ፡ ወደ ፡ ቀኝና ፡ ወደ ፡
ግራ ፡ ወደ ፡ ዳገቱም ፡ አሻቅቦ ፡ ስለ ፡ ነፈሰ ፡ ቁልቁል ፡ ቢሮጡ ፡ ወላፈኑ ፡ የማይጎዳቸው ፡

መሆኑን ፡ ተረዱት። ስለዚህ ፡ ወዲያው ፡ ዐይናቸውን ፡ ጨፍነው ፡ ቍልቍል ፡ ሮጡ። እንዚህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ አብረዋቸው ፡ ከነበሩት ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ በስንት ፡ ድካም ፡ (በብዙ ፡ ድካም) ፡ ከዚህ ፡ ከክፉ ፡ አደጋ ፡ አመለጡ ፤ (ዳኑ) ።

## ክፍል ፡ ፪ ፡ እረኛና ፡ የነብር ፡ አደጋ ፡

ቆላ ፡ ቀመስ ፡ አገሮች ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ለፍየሎች ፡ የተስማሙ ፡ ናቸው ። ዐመልሳ ፡ የምትባለዋም ፡ ቀበሌ ፡ ለፍየል ፡ ርቢ ፡ የተስማማች ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ በእርሻቸው ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተጨማሪ ፡ ሥራ ፡ እያደረጉ፡ ፍየሎችን፡ ያረቡ ፡ ነበር ።

እረኞች ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ መሚገጣቸው ፡ አይቀርምና ፡ አንድ ፡ እረኛ ፡ ፍየሎቹን ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ቆላ ፡ ተሠምርቶ ፡ ሳለ ፡ ፍየሎቹን ፡ ትቶ ፡ ከሌሎች ፡ እረኞች ፡ ጋራ ፡ እንኮይንና ፡ ገባን ፡ (ቁርቁራን) ፡ ሲያሳድድ ፡ ሦስቱን ፡ ፍየሎች ፡ ነብር ፡ ጠቅቶ ፡ ጥሏቸው ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ሲመለስ ፡ ሦስቱን ፡ ከጉመሮ ፡ ሥር ፡ ተዘርግተው ፡ አገኛቸው ። የጠቃቸውንም ፡ ነብር ፡ በጉመሮው፡ አጠገብ ፡ ባለው ፡ ዛፍ ፡ ላይ ፡ መኖሩን፡ ባወቀ ፡ ጊዜ ፡ ለጌታው ፡ ለመንገር ፡ ወደ ፡ መንደር ፡ (አንባ) ፡ ወጣ ። እንደ ፡ ደረሰም ፡ ለጌታው ፡ ነገረውና ፡ እርሱም ፡ በንዴት ፡ ጦሩን ፡ አንሥቶ ፡ ባላጋራው ፡ ወዳለበት ፡ ባሽከሩ ፡ እየተመራ ፡ መጣ ።

አያ ፡ ነብሮና ፡ ጌትዮው ፡ ዐይን ፡ ላይን ፡ ግጭት ፡ ሲሉ ፡ ከንዴቱ ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ጌትዮው ፡ ቸኩሎ ፡ ነበርና ፡ ጦሩን ፡ ሰብቆ ፡ ቢወረውርበት ፡ መቼም ፡ ፍጥነት ፡ የአያ ፡ ነብሮ ፡ የባሕርይ ፡ ገንዘብ ፡ ናትና ፡ በፍጥነት ፡ ጦሩን ፡ ቀልቶ ፡ ጥሎ ፡ ወደ ፡ ጌትዮው ፡ ገሠገሠ ። እንዲሁም ፡ የሚቾቹ ፡ ጌታ ፡ ደፋር ፡ ስለ፡ ነበረ ፡ ወደ ፡ ነብሩ ፡ ሲገሠግሥ ፡ እመንገድ ፡ ተገናኙና ፡ ታላቅ ፡ ትግል ፡ ተዠመረ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አሽከርዮው ፡ ጌታውን ፡ በመርዳት ፡ ፈንታ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ሰው ፡ ለመጥራት ፡ ወደ ፡ አንባ ፡ ወጣ ።

ሁለቱ ፡ ጀግኖች ፡ ገጥመው ፡ ሲባባሉ ፡ ላየ ፡ ሰው ፡ በጣም ፡ አስደናቂ ፡ ነበር ፡ ይባላል ። አንድ ፡ ጊዜ ፡ አንደኛው ፡ በላይ ፡ ሁለተኛው ፡ በታች ፡ እየሆኑ ፡ ሁለቱም ፡ በየበኩላቸው ፡ አንዱ ፡ ሁለተኛውን ፡ በመጥፎ ፡ አኳኋን ፡ ጕረሮውን ፡ ይዞት ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ በጣም ፡ ተዳከሙ ። ስለዚህ ፡ ሁለቱም ፡ ሰዎች ፡ ከመንደር፡ መጥተው ፡ እስኪገላግሏቸው፡ ድረስ ፡ እንዲሁ ፡ እንደ ፡ ተያያዙ ፡ ተፋጠው ፡ ከመታየታቸው ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ ለማድረግ ፡ አልቻሉም ፡ ነበር ።

አሽከርዮውም ፡ ወደ ፡ መንደር ፡ ወጥቶ ፡ እንደ ፡ ፈተኛው ፡ በለሆሳስ ፡ ሳይሆን ፡ ጩኸቱን ፡ ስላቀለጠው ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ተሰብስበው ፡ ጋሻና ፡ ጦራቸውን ፡ ይዘው ፡ ወደ፡ ጀግኖቹ ፡ ዘንድ ፡ በፍጥነት ፡ ወረዱ ። ለገሠና ፡ ከልክልም ፡ እንደዚሁ ፡ ሰምተው ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ እየተሯሯጡ፡ ደርሰውባቸው ፡ አብረው ፡ ቍልቍለቱን ፡ ተንደረደሩ። በደረሱም ፡ ጊዜ ፡ በቀላሉ ፡ ጀግኖቹን ፡ ለመገላገል ፡ የማይቻል ፡ በመሆኑ ፡ ታላቅ ፡ ምጥ ፡ ያዛቸው። ከነዚያም ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ አንድ ፡ ጀግና ፡ አይታጣም ፡ ነበርና ፡ ለገሠ

የሚባለው ፡ ወጣት ፡ ጩቤዉን ፡ መዞ ፡ እየሮከረ ፡ ሄደና ፡ የነብሩን፡ ሆድ ፡ ዕቃ፡ ዘርግፎ፡ ጣለው ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ነምሩ ፡ ተዝለፈለፈና ፡ የጠላቱን ፡ አንገት ፡ ለቀቀ ፤ ወዲያ ውም ፡ ነፍሱን ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠ ። የሚቾቹ፡ ጌታ ፡ የማታ፡ ማታ ፡ ድሉ ፡ የርሱ፡ በመሆኑ፡ ታላቅ ፡ ደስታ ፡ ስለ ፡ ተሰማው ፡ ሥቃዩንና ፡ መከራውን ፡ አላስታወሰውም ። እንደዚህ ፡ ያለው ፡ የጀግንነት ፡ እስፖርት ፡ የለገሥንና ፡ የከልክልን ፡ ምኞት ፡ እየገነነ ፡ ከመሄድ ፡ አላገደውም ።

## ክፍል፡፫፡ ለገሥና ፡ ከልክል ፡ ወደ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ኮበለሉ ፡

ለገሥና ፡ ከልክል ፡ ከሕፃንነታቸው ፡ ዠምሮ ፡ የትምህርት ፡ ፍላጎት፡ ነበራቸውና፤ ዕድሜያቸው ፡ ዐሥራ ፡ አራት ፡ ዓመት ፡ ከሆነ ፡ በኋላ ፡ መቼም ፡ በቀድሞ ፡ ዘመናት ፡ ወጣቶች ፡ ከቤታቸው ፡ እየጠፉ ፡ ነበርና ፡ የሚማሩት ፡ ጠፍተው ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ አውራጃ ፡ ሄዱ ። ሲሄዱም ፡ ካንዳንድ ፡ የውኃ ፡ ቅልና ፡ ካንዳንድ ፡ ኮረጆ ፡ በስተቀር ፡ ምንም ፡ አል ያዙም ፡ ነበር ።

የለገሠ ፡ ወላጆች ፡ ሰባት ፡ ልጆች ፡ ከወለዱ ፡ በኋላ ፡ በጥቂት ፡ ምክንያት ፡ ተለያ ይተው ፡ አባቱ ፡ ባገር ፡ አገዛዝ ፡ ምክንያት ፡ እነርሱ ፡ ወደ ፡ ሄዱበት ፡ ወረዳ ፡ ሄደው ፡ አንድ ፡ ቀበሌ ፡ እያስተዳደሩ ፡ ይቀመጡ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ልጃቸውንና ፡ የልጃቸውን ፡ ባል ንጀራ ፡ በመልካም ፡ ተቀብለው ፡ አስቀምጠው ፡ ደጓና ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ መፈለግ ፡ ዠመሩ ። ወጣቶቹም ፡ በዚህ ፡ ነገር፡ ተደስተው ፡ በጋለ ፡ ተስፋ ፡ ሲጠባበቁ ፡ በጥባጭ፡ ሳለ ፡ ማን ፡ ጥሩ ፡ ይጠጣል ፡ እንደሚባለው ፡ ሁሉ ፡ ያባቱ፡ አሽከር ፡ ለገሠን ፡ በምክር ፡ እያሽበለበለ ፡ ከዚያ ፡ ወረዳ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ቢሄዱ ፡ የበለጠ ፡ ትምህርት ፡ እንደሚገኝ ፡ አሳምሮ ፡ ልቡን ፡ አሸፈተው ።

እነዚህ ፡ ሁለት፡ አዲስ ፡ ባልንጀሮች፡ የሚከዱበትን ፡ ምቹ ፡ ጊዜ ፡ ፈለጉና ፡ በሌ ሊት ፡ ኮብልለው ፡ ሄዱ።አዬ፣ ጉድ! እንግዲህ ፡ ከልክልን ፡ ምን ፡ ይዋጠው! እርሱም፡ እንደ ፡ ለገሠ ፡ ሌሊት ፡ ከድቶ ፡ ይጥፋ ! አይደለም ፤ ለለገሠ ፡ አባት ፡ ታማኝ፡ ሆኖ ፡ እር ሳቸው ፡ ባዘዙት ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ ገብቶ ፡ መማር ፡ ይሻለዋል ። ግሩም ፡ ነው ፡ እኮ! በጣም ፡ ይደንቃል ! እንዴት ፡ ሰው ፡ አብሮ ፡ መክሮና ፡ ዘክሮ ፡ ከቤቱ ፡ ከወጣ ፡ በኋላ ፡ ይከዳል ! እንደዚህ ፡ ያለው ፡ ነገር ፡ ራስን ፡ ወዳድ ፡ ከመሆን ፡ የተነሣ ፡ የሚደረግ ፡ ይመስላል ። ደግሞ ፡ እንደዚህ ፡ ተብሎ ፡ እንዳይገመት ፡ ልጁ ፡ ገና ፡ ያሥራ ፡ አራት ፡ ዓመት ፡ ወጣት ፡ ነው ፤ ቢሆንም !! ብቻውን ፡ ከመሆኑ ፡ የተነሣ ፡ ከልክልን ፡ ያሳብ ፡ ትግል ፡ በጎሊናው ፡ እየወጣና ፡ እየወረደ ፡ አስቸገረው ። እርሱም ፡ እንደነዚያ ፡ አንድ፡ ቀን ፡ ከድቶ ፡ እንደሚሄድ ፡ ቁርጥ ፡ አሳብ ፡ አደረገ ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ ብቻውን ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ልቡ ፡ ትርግ ፡ ትርግ ፡ እያለ ፡ መባባቱ ፡ አልቀረም ። እንደ ፡ እነርሱ ፡ ሌሊት ፡ ኮብልሎ ፡ ለመሄድ ፡ ስለ ፡ ፈራ ፡ በማለዳ ፡ ከዳና ፡ ዱር ፡ ለዱር ፡ እየተሹለከለከ ፡ ጓደ ኛው ፡ ሄደ ፡ ወደ ፡ ተባለበት ፡ አገር ፡ እየጠየቀ ፡ ነጎደ ። አምስት ፡ ሰዓት ፡ ከሄደ፡ በኋላ፡ ታላቅ ፡ ፍርሀት ፡ ያዘውና ፡ ጎሊናው ፡ ተጨነቀበት ፡ ብቻውን ፡ በመንገድ ፡ ዳር ፡ ቁጭ፡

ብሎ ፡ ያለቅስና ፡ ይተክዝ ፡ ዝምር ። አዬ ፡ ሕፃን ፡ ሆኖ ፡ በማያውቁት ፡ አገር ፡ መንከራተት ፡ ያለበት ፡ አበሳ ! እንዲያው ፡ ይቀመጥ ! ኧረ ፡ አይነሣ ! መቼም ፡ ልጅ ፡ በአሳብ ፡ መድከም ፡ አይቀርምና ፡ ምድር ፡ ሰማዩ ፡ ስለ ፡ ዞረበት ፡ ልቡ ፡ በጣም ፡ ተሸ በረበት ፤ በዙሪያውም ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ ዘሎ ፡ አንቆ ፡ የሚበላው ፡ መሰለው ። ከእንግ ዲህ ፡ ወዲያ ፡ መንገድ ፡ መቀጠል ፡ ጭንቀት ፡ ባለበት ፡ ሐሳባዊ ፡ ባሕር ፡ ውስጥ ፡ እንደ፡ መግባት ፡ ያለ ፡ ስለ ፡ ሆነበት ፡ ወደ ፡ ኋላው ፡ አውጪኝ ፡ እግሬ ፡ እያለ ፡ ይኳትን ፡ ዝመር። ማለክለክንና ፡ ሲቃን ፡ ማን ፡ ከቁም ፡ ነገር ፡ ቢቈጥራቸው ፡ እንደ ፡ ንፋስ ፡ እየበነነ ፡ አምስት ፡ ሰዓት ፡ ያህል ፡ የፈጀበትን ፡ መንገድ ፡ በጥቂት ፡ ጊዜያት ፡ ውስጥ ፡ አቋራርጦ ፡ ብቅ ፡ አለ ።

የለገሠ ፡ አባት ፡ ቤት ፡ ባንድ ፡ ትንሽ ፡ ጋራ ፡ ሥር ፡ ባለው ፡ ረባዳ ፡ ሥፍራ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ልጆች ፡ ከልክልን ፡ ባለባበሱና ፡ ባካሄዱ ፡ ያውቁት ፡ ነበርና ፡ ቁልቁል ፡ ሲንደረደር ፡ አይተው ፡ የሦስት ፡ ልጆች ፡ መጥፋት ፡ ላበሳጫቸው ፡ አባት ፡ ነገሯቸው ፡ እርሳቸውም ፡ ብቅ ፡ ብለው ፡ ቢመለከቱ ፡ በእውነቱ ፡ ከልክል ፡ በቁልቁለቱ ፡ ላይ ፡ ይጣደፋል ። ከደስታቸውም ፡ የተነሣ ፡ በእልልታ ፡ መንደሩን ፡ ሊያሸብሩት ፡ ምንም ፡ ያህል ፡ አልቀራቸውም ። እንደ ፡ ደረሰም ፡ እቅፍ ፡ አድረገው ፡ ስመው ፡ «ምነው ፡ ልጄ ፡ ምን ፡ በደልሁ » ? ብለው ፡ ጠየቁት ፤ ልጁ ፡ ግን ፡ በልቅሶ ፡ ከሙንፈቅፈቅ ፡ (መንሰቅ ሰቅ) ፡ በስተቀር ፡ ምንም ፡ ሊመልስላቸው ፡ አልቻለም ። ወዲያውም ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ይዘ ውት ፡ ገብተው ፡ እንዲታጠብ ፡ ካደረጉ ፡ በኋላ ፡ ምግብ ፡ እንዲዘጋጅለት ፡ አዘዙ ። ረኃብ ፡ ቆንድዶት ፡ ነበርና ፡ ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ ታጥቦ ፡ ጨረሰና ፡ ከመታጠቢያ ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ወጣ ፡ ምግብ ፡ ቀረበለት ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ቀድሞው ፡ ነፃ ፡ መሆኑ ፡ ቀርቶ ፡ በዐ ይነ ፡ ቁራኛ ፡ ያስጠብቁት ፡ ዝምር ።

የኮበለሉት ፡ ጉብሎች ፡ በሄዱበት ፡ አገር ፡ ላንድ ፡ ሳምንት ፡ ያህል ፡ በችጋር ፡ አለንጋ ፡ ስለ ፡ ተገረፉ ፡ ቍስለ ፡ ረኃቡ ፡ እየነዘነዘ ፡ (እየወዘወዘ) ፡ ወይም ፡ እየነዘረ ፡ ስላ ስቸገራቸው ፡ ከቍስለ ፡ ረኃቡ ፡ የሚፈወሱበትን ፡ መንገድ ፡ መፈለግ ፡ ግዴታ ፡ ሆነባቸው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ቢዘሉ ፡ ቢፈርጡ ፡ በማያቁት ፡ አገር ፡ እንዴት ፡ አድርገው ፡ መድኀኒት ፡ ለማግኘት ፡ ይቻሉ ! እንግዲህ ፡ ከልክላቸውን ፡ በመንገድ ፡ ድል ፡ አድርጋ ፡ የመ ለሰች ፡ ፈተና ፡ ልትቀርባቸው ፡ ነው ፡ መሰለኝ ፤ ይህን ፡ ጊዜ ፡ በቤታችን ፡ እነአባባ ፡ ለኛ ፡ ሲሉ ፡ ይጨነቃሉ ። እኛ ፡ ግን ፡ ሳያዋጣን ፡ እዚህ ፡ ድረስ ፡ ከድተን ፡ መጥተን ፡ በችጋር ፡ እንቆራመዳለን ፡ እያሉ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ መወያየት ፡ ዝመሩ ። ከዚህ በኋላ ፡ የመመለሳቸው ፡ ነገር ፡ በማያወላውል ፡ አሳብ ፡ ተቆረጠና ፡ የመልስ ፡ ጉዞ ፡ ተጀ መረ ። ሲመለሱ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ ለለገሠ ፡ ደስታ ፡ ቢሰማው ፡ አሽከሩ ፡ ቷወቅሶ ፡ ቅጣት ፡ እንደሚያገኘው ፡ ያምን ፡ ነበረና ፤ ማዘንና ፡ መተከዝ ፡ ዝመረ ። ስርቆ ፡ ከማሰብ ፡ እጅን ፡ መሰብሰብ ፡ እንደሚባለው ፡ ያለሙን ፡ አስቀድሞ ፡ መርምሮ ፡ ተረድቶት ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ መቼ ፡ አሁን ፡ ይተክዝ ፡ ነበር ! አዬ ፡ አርቆ ፡ አለማሰብና ፡ አለመገመት ፡ ኧረ ፡ እንዴት ፡ ያለውን ፡ ጣጣ ፡ ታመጣላችሁ !

ሞት ፡ ካልቀደመ ፡ በቀር ፡ ወይም ፡ ባንድ ፡ ምክንያት ፡ ካልተሰናከለ ፡ በቀር ፡ የተዝመረ ፡ ጉዞ ፡ መዘለቁ ፡ አይቀርምና ፤ ወዳባታቸው ፡ ቤት ፡ ደረሱ ። አባታቸውም ፡

በደስታ ፡ ተቀበሏቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ ለከልክላቸው ፡ የተደረገለት ፡ አቀባበል ፡ አል ታሰበላቸውም ። አሽከርዮውም ፡ የፈራው ፡ ቅጣትና ፡ ወቀሣ ፡ አልቀረለትም ፤ ለለገ ሠም ፡ ጥቂት ፡ ግልምጫ ፡ ተደርጎለታል ።

ለገሠና ፡ ከልክል ፡ እንደ ፡ ገና ፡ አዲስ ፡ ብልኀት ፡ ፈጥረው ፡ ይጣፉሉ ፡ በማለት፡ ስለ ፡ ሠጉ ፡ በበለጠ ፡ አኳኋን ፡ በዐይን ፡ ቁራኛ ፡ ያስጠብቋቸው ፡ ዠመር ። እንዳጋ ጣሚ ፡ በዐመልሳ ፡ ቀበሌ ፡ ውስጥ ፡ ከሚኖሩት ፡ ከለገሠ ፡ አባት ፡ ዘመዶች ፡ አንዱ ፡ ስለ፡ ሞተ ፡ ለልቅሶ ፡ ሲመጡ ፡ ወጣቶቹን ፡ አምጥተው ፡ አንደኛውን፡ ለናቱ፡ ሌላውን፡ ላባቱ፡ አስረከቡ ። ስለዚህ ፡ የለገሠና ፡ የከልክላቸው ፡ አሳብ ፡ በዚያ ፡ በጠማማ ፡ አሽከር ፡ ምክ ንያት ፡ ስለ ፡ ተሰናከለ ፡ እንደ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ ተይዘው ፡ መጥተው ፡ ለየቤቶቻቸው ፡ ተሰጡ ።

## ፫ ፡ አመዛዛኝ ፡ ድርሰት ፡ (የጎሊናን ፡ አሳብ ፡ መመዘኛ ፡ ድርሰት)፡

መግለጫ ፡

ከአእምሮ ፡ እየፈለቀ ፡ የሚወጣው ፡ ጉልሕ ፡ አሳብ ፡ ተመዛዝኖ ፡ ጉዳቱና ፡ ጥቅሙ ፡ በመልካም ፡ ድርጅት ፡ የሚቀርብበት ፡ መንገድ ፡ ነው ፡ ማወዳደርም ፡ በዚሁ፡ ይጠቀለላል ።

### ሥልጣኔና ፡ ድንቁርና ፡

ሥልጣኔ ፡ በኑሮ ፡ ረገድ ፡ ጥንት ፡ ያልተሻሻለውን ፡ ነገር ፡ በቀላል ፡ ዘዴ ፡ (መን ገድ) እያሻሻሉ ፡ ምቾት ፡ የሚገኝበትን፡ ብልኀት ፡ እየፈለጉ፡ መሥሪያና ፡ ባዲሱ ፡ ሥል ጣኔ ፡ ሕዝብ ፡ በጭካኔ ፡ እንዳይጉላላ ፡ በመልካም ፡ ትምህርት ፡ እያሳደገ ፡ ወደ ፡ ከፍ ተኛው ፡ የኑሮ ፡ ዘዴ ፡ መምሪያ ፡ ነው ።

ድንቁርና ፡ ያንድ ፡ አገር ፡ ሕዝብ ፡ የኑሮውን ፡ ዘዴና ፡ የሀብቱን ፡ ደረጃ ፡ እንዳ ያሻሽል ፡ በጨለማዊ ፡ ድንቁርና ፡ ሰንሰለት ፡ እየጎተተ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ወጥሮ ፡ የሚስብ፡ ታላቅ ፡ ኃይል ፡ ነው ። ያንድ ፡ አገር ፡ ሀብት ፡ የሚስፋፋው ፡ ሕዝቡ ፡ እንደ ፡ ልቡ ፡ መንገድ ፡ ተከፍቶለት ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ በማለቱ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የመሠልጠን ፡ መንፈስ ፡ የመንግሥቱንና ፡ የሕዝቡን ፡ መንፈስ ፡ የገዛው ፡ (የሳበው) ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የመኪናን ፡ መንገድ ፡ በመቀጥቀጥና ፡ የባቡር ፡ መንገድን ፡ በመዘርጋት ፡ ውደቅ ፡ ተነሣ ፡ እንዲል ፡ ያደርገዋል ።

ማናቸውም ፡ ሥራ ፡ ጠንክር ፡ ብለው ፡ ካልደከሙበት ፡ ጥቅም ፡ አይሰጥም ፤ ይል ቁንም ፡ ዝቅተኛን ፡ ሥራ ፡ በመሥራት ፡ ላይ ፡ ያለው ፡ ድካም ፡ ከልክ ፡ ያለፈ ፡ ነው ። አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ ተው ፡ እባክህ ፡ ኩራት ፡ ራት ፡ ነው ፡ እያሉ ፡ በስንፍና ፡ ምክንያት ፡ መሥራት ፡ አቅቷቸው ፡ በችጋር ፡ አለንጋ ፡ በገዛ ፡ ራሳቸው ፡ ይገረፋሉ ። ኩራት ፡ ራት፡ ነው ፡ የሚባለው ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ጉልበት ፡ እያለኝ ፡ ማንንም ፡ አላስቸግርም ፡ ብሎ ፡ ጠንክሮ ፡ እየሠራ ፡ ራሱን ፡ ቢችል ፡ ነው፡ እንጂ ፤ ሥራን ፡ ንቆ ፡ በመንገላወድ ፡ አይደ ለም።እንግዲህ፡ መንገላወድን፡ የፈጠረው፡ ታላቁ፡ ድንቁርና፡ መሆኑ፡ የተረጋገጠ፡ ነው። አንድ፡ ሰው፡ ለጊዜው፡ ከፍተኛ፡ ሥራን፡ አጥቶ፡ ዝቅተኛን፡ ሥራ፡ ቢያገኝ፡ ለጊዜው፡ ዝቅ

ተኛውን፡ ሥራ፡ ይዞ ፡ ከፍተኛ፡ ሥራን ፡ ለማግኘት፡ መጣጣር ፡ ይገባዋል ? ወይስ፡ ከፍ
ተኛ ፡ ሥራን፡ እስኪያገኝ፡ በችግር ፡ እየተቆራመደ፡ ቦዝኖ፡ መቀመጥ ? እንደኔ፡ ሐሳብ፡
ቢሆን ፡ የጊዜው ፡ ሁናቴ ፡ እንደ ፡ ፈቀደለት ፡ ከትንሹ ፡ ደረጃ ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡
ቀስ ፡ እያለ ፡ ቢያዘግም ፡ ይሻለዋል ።

ሥልጣኔ፡ እንኳ፡ በከተማ፡ይቅርና፡ በባላገርም፡ ቢሆን፡ ሕዝቡ፡ የእርሻውን፡ ዘዴ፡
እያሻሻለ ፡ እንዲሄድ ፡ ያደርገዋል ። ሥልጣኔ ፡ አንድ ፡ ገበሬ ፡ መሬቴ ፡ አርጅቷል ።
ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ሌላ ፡ ፈልጌ ፡ አርሳለሁ ፡ እንዲል ፡ አይፈቀድለትም። ምክንያቱም፡
መሬቱ ፡ ፍግና ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ማዕድናትን ፡ በመመገብ ፡ እንደሚታደስ ፡ ስለሚያስተም
ረው ፡ ነው ፤ ሥልጣኔ ፡ ለርቢና ፡ ለፍሪዳ ፡ የሚሆኑትን ፡ እየለየ ፡ በያገባባቸው ፡ እንዲ
ሻሻሉ ፡ ያስተምራል ።

ድንቁርና ፡ ግን ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ከተበላሸ ፡ በኋላ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ዘዴ ፡ ተመልሶ፡
መሠራቱን ፡ ወይም ፡ መተካቱን ፡ አያስተምርም ፤ ድንቁርና ፡ የቁጠባ ፡ ጠላት ፡ ስለ፡
ሆነ ፡ ማናቸውም ፡ ነገር ፡ ያለበዓቱ ፡ ደፋ፡ ደፋ ፡ ብሎ ፡ እንዲያልቅ ፡ ይገፋፋና ፡ ከታላቅ፡
ችግር ፡ ላይ ፡ ይጥላል ። የድቁርና ፡ አዟሪት ፡ ባሕር ፡ ያስጠማቸው ፡ ሰዎች፡ ቢቈጠሩ ፡
እስከመቼም ፡ ድረስ፡ አያልቁም ። ድንቁርና ፡ የምቀኝነት፡ መማሪያ ፡ ስለ፡ ሆነ ፡ ሰዎች፡
በሰላም ፡ እንዲተዳደሩ ፡ አይፈቅድላቸውም ፤ ቢቻለውስ ፡ አንዱ ፡ አንዱን ፡ እንዲሰርቅ፡
አንዱ ፡ አንዱን ፡ እንዲቀማና ፡ አንዱ ፡ ደግሞ ፡ አንዱን ፡ እንዲገድል፡ ያደርገዋል ።

የከተማን ፡ ውበትና ፡ የሕዝብን ፡ ጤና ፡ የሚጠብቅ ፡ አቶ ፡ ሥልጣኔ ፡ የሕዝቡን፡
ዝቅተኛ ፡ አኗኗር ፡ ከፍ ፡ ለማድረግ ፡ ሌት ፡ ከቀን ፡ ተግቶ ፡ ይሠራል ። ሰዎች ፡ በከተማ፡
ውስጥ ፡ ሲቀመጡ ፡ ቆሻሻውን ፡ (ጥራጊውን) ፡ እንዳፈተታቸው ፡ እየጣሉ ፡ በገዛ ፡ ራሳ
ቸው ፡ በመጥፎ ፡ ሽታና ፡ በጥቃቅን ፡ በራሪዎች ፡ ምክንያት ፡ በሽታን ፡ እንዳያመጡ ፡
በትምህርት ፡ ይከለክላቸዋል ። ልብሳቸውንም ፡ ባደፈ ፡ ቊጥር ፡ እንዲያጥቡና ፡ እንዲለ
ውጡ ፡ ያስጠነቅቃቸዋል ። ሥልጣኔ ፡ በነገሠበት ፡ አገር ፡ የሕዝቡ ፡ ጤናና ፡ ሀብት ፡
በጣም ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ነው ።

ድንቁርና ፡ ያለመተማመንን ፡ መንፈስ ፡ በሕዝብ ፡ ላይ ፡ እየዘረጋ ፡ እርስ ፡ በርሳ
ቸው ፡ እንዳይረዳዱ ፡ እያደረገ ፡ በመንፈስ ፡ ይበትናቸዋል ። ስለዚህ ፡ አንዱ ፡ እንደዚህ ፡
ይደረግ ፡ ሲል ፡ አንደኛው ፡ ደግሞ ፡ ለምን ፡ እንደዚህ ፡ ይሆናል ፡ በማለት ፡ እንዲነሣ
በት ፡ ያደርገዋል ። አንዱ ፡ ባንዱ ፡ ሲሥቅ ፡ ጀንበር ፡ ጥልቅ ፡ እንደሚባለው ፡ አንዱ ፡
የቤቱን ፡ ጥራጊ ፡ በደንበኛው ፡ የቆሻሻ ፡ መጣያ ፡ ሲያስጥል ፡ ሌላው ፡ ደግሞ ፡ በደ
ጃፉ ፡ አጠገብ ፡ እንዲጥለው ፡ ያደርጋል ። በዚህ ፡ ምክንያት ፡ የከተማው ፡ ውበት ፡ ተበ
ላሽቶ ፡ ሕዝቡ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ በሽቶች ፡ ይመረዛል ፤ ድንቁርና ፡ የሚያስገኘው ፡ ፍሬ ፡
እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ነው ።

ሥልጣኔ ፡ ጊዜ ፡ ወርቅ ፡ መሆኑን ፡ ለሕዝብ ፡ ያስገነዝባል ። አንድ ፡ ሰኮንድ ፡
ወይም ፡ አንዲት ፡ ደቂቃ፡ ስታልፍ ፡ ከዕድሜያቸው፡ ላይ ፡ መቀነሱንና ፡ ያች ፡ የሚያሳል
ፉት ፡ ደቂቃ ፡ ወይም ፡ ሰኮንድ ፡ ላንድ ፡ ነገር ፡ መሥሪያ ፡ እንደ ፡ ተሰጠቻቸው ፡ ያስተ

ምራቸዋል ። የጊዜ ፡ ገንዘብነት ፡ በጣም ፡ ላቅ ፡ ያለ ፡ ነው ። ምክንያቱም ፡ አንድ ፡ ሰው፡ በተሰጠው ፡ ጊዜ ፡ ካልሠራበት ፡ ዋጋ ፡ ለማግኘት ፡ ስለማይችል ፡ ነው ።

ድንቁርና ፡ ሰውን ፡ ከፈሪሀ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያርቅና ፡ ውርደት ፡ የሚያመጣበትን ፡ ነገር ፡ ያሠራዋል ። ሰውን ፡ የሚያዋርዱ ፡ ነገሮች ፡ ምንድር ፡ ናቸው ? ተንኮል ፡ ልክስክስነት ፡ እምነትን፡ ማጉደል፡ እኔ ፡ ልባስ ፡ እኔ፡ ልባስ፡ ማለትና ፡ ሥሥት ፡ ናቸው ። የሰው ፡ ልጅ ፡ ከእምነት ፡ ከተራቀተ ፡ ማንን ፡ ፈርቶ ፡ በጎ ፡ ነገርን ፡ ለመሥራት ፡ ይሞክራል ? እንሆ ፡ ድንቁርና ፡ ሰውን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ለይቶ ፡ ወደ ፡ ጥፋት ፡ ገደል ፡ የሚሰድ ፡ ነው ።

ሥልጣኔ ፡ ማለት ፡ ሰውን ፡ ካለማወቅ ፡ ወደ ፡ ማወቅ ፡ የሚመራ ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ ሥልጣኔ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ወደ ፡ ማወቅ ፡ ይመራናል ። አንዱ ፡ ላንዱ ፡ በፍቅር ፡ መታዘዝ ፡ እንደሚገባው ፡ ያስተምራል ። የሥልጣኔ ፡ ዋና ፡ ጋሾቹ ፡ እምነትና ፡ ትሕትና ፡ ናቸው ። እምነትና ፡ ትሕትና ፡ በሚገኙበት ፡ አገር ፡ የሕዝቡ ፡ አስተዳደር ፡ የተመሰገነ ፡ እንደሚሆን ፡ የተረጋገጠ ፡ ነው ።

ያሁኑ ፡ ዘመናችን ፡ እንዲያው ፡ በከንቱ ፡ የሥልጣኔ ፡ ዘመን ፡ ይባላል ፡ እንጂ ፡ የድንቁርና ፡ ዘመን ፡ ነው ። አንዱ ፡ አንዱን ፡ ለመግዛት ፡ አንዱ ፡ አንዱን ፡ ለመንጠቅ ፡ አንዱ ፡ አንዱን ፡ ጨቁኖ ፡ ለማስለቀስ ፡ የሚጣጣርበት ፡ ዘመን ፡ እንዴት ፡ ተደርጎ ፡ የሥልጣኔ ፡ ዘመን ፡ ተብሎ ፡ ይጠራል ? እንሆ ፡ ባንዳንድ ፡ አገሮች ፡ ሴቶች ፡ ሽማግሌዎችና ፡ ሕፃናት ፡ ቤታቸው ፡ በቦንብ ፡ ስለ ፡ ፈረሰ ፡ መግቢያ ፡ አጥተው ፡ ይንከራተታሉ ። እንሆ ፡ በስንትና ፡ በስንት ፡ ዘመን ፡ በሚሊዮን ፡ የሚቈጠር ፡ ብር ፡ ወጥቶባቸው ፡ የተሠሩ ፡ ከተሞች ፡ በትንሽ ፡ ሰዓቶች ፡ ውስጥ ፡ ድምጥማጣቸው ፡ ይጠፋል ። ስለዚህ ፡ ያሁኑ ፡ ዘመን ፡ በጠቅላላው ፡ የድንቁርና ፡ ዘመን ፡ መሆኑ ፡ የተረጋገጠ ፡ ነው ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ ሥልጣኔን ፡ ለማላቅ ፡ መጣር ፡ ይገባናል ።

## ደራሲና ፡ ቀማሚ ፡

አንድ ፡ ደራሲ ፡ ባንድ ፡ መድኀኒት ፡ ቀማሚ ፡ ይመሰላል ። አንድ ፡ መድኀኒት ፡ ቀማሚ ፡ ሳይማርና ፡ ልምድ ፡ ሳያደርግ ፡ እንዲያው ፡ ከመሬት ፡ ተነሥቶ ፡ መድኀኒት ፡ ቀማሚ ፡ እሆናለሁ ፡ ቢል ፡ ማንም ፡ አይቀበለውም ። አስቀድሞ ፡ አንድ ፡ ነገርን ፡ ከመቀመሙ ፡ በፊት ፡ የሚቀመሙትን ፡ ነገሮች ፡ በያይነታቸው ፡ እየሰበሰበ ፡ በሚያሰናዳበት ፡ ሥፍራ ፡ ማስቀመጥ ፡ አለበት ። ተፈላጊዎች ፡ ነገሮች ፡ በያይነታቸው ፡ ከቀረቡ ፡ በኋላ ፡ ባንድነት ፡ እየተዋሐዱ ፡ (እየተገጣጠሙ) ፡ አንድ ፡ ፀይነት ፡ በሽታ ፡ የሚፈውሱትን ፡ ይቀምማል ። ይህንንም ፡ የቀመመውን ፡ መድኀኒት ፡ ለሕዝብ ፡ ከመስጠቱ ፡ በፊት ፡ በትናንሾችና ፡ በትልልቆች ፡ እንስሳት ፡ ላይ ፡ ይፈትነዋል ፤ ደኅና ፡ አድርጎ ፡ ግብሩን ፡ አጣርቶና ፡ መጠኑን ፡ ለክቶ ፡ ካወቀ ፡ በኋላ ፡ ለሕዝብ ፡ ይሰጣል ።

እንደዚሁም ፡ ጽሑፉን ፡ ከማዘጋጀት ፡ በፊት ፡ የጽሑፉን ፡ ሥነ ፡ ሥርዐት ፡ ጠንቅቆ ፡ ማጥናት ፡ ላንድ ፡ ደራሲ ፡ ዋና ፡ ተግባሩ ፡ ነው ። ከዚህ ፡ በኋላ፡ የሚጽፈውን፡

ነገር ፡ በየፈርጁ፡ እያጠና ፡ ይሰበስብና ፡ ባንድነት፡ እየተቀነባበሩ፡ ስሜት፡ የሚሰጡትን፡ ነገሮች ፡ በየወገናቸው፡ ጠቅልሎ፡ ይጽፋቸዋል። ደራሲው ፡ የሚጽፈውን ፡ ነገር፡ ባሳቡ፡ እንደ ፡ መጣለት ፡ ጽፎ ፡ ሳያሳትም ፡ የጽሑፉን ፡ ቅደም ፡ ተከተልና ፡ ጠቃሚነት ፡ እየመ ላለሰ ፡ ያርመዋል ። በመጨረሻም ው ፡ ጠቃሚነቱ ፡ ተረጋግጦ ፡ ታትሞ ፡ ይወጣና ፡ ለሕዝብ ፡ ይሰጣል ።

መድኀኒት ፡ ቀማሚና ፡ ደራሲ ፡ የሚለያዩበት ፡ ቀማሚ ፡ በዐይን ፡ የሚታዩትንና፡ በጅ ፡ የሚዳሰሱትን ፡ ነገሮች ፡ እየሰበሰበና ፡ በእጁ ፡ እያገላበጠ ፡ ስለሚቀምማቸው ፡ ነው ። ደራሲ ፡ ግን ፡ በአእምሮ፡ እየሰበሰበና፡ እየቀረጸ፡ ይጽፋል ፡ እንጂ፡ እንደ ፡ ቀማሚ፡ በእጁ ፡ አይዳስሳቸውም ፤ ባይኑም ፡ አያያቸውም ። ከተጠቀሱት ፡ ምክንያቶች ፡ በስተ ቀር ፡ እየሰበሰቡ ፡ ቀምሞና ፡ አዘጋጅቶ ፡ ለሕዝብ ፡ በመስጠት ፡ ግን ፡ ሁለቱም ፡ አንድ ፡ ናቸው ። (በሥራቸው ፡ ይመሳሰላሉ) ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ፡ ንግግር ፡

### ክፍል ፡ ፩ ፡ የንግግር ፡ መግለጫ ፡

ንግግር ፡ አንዱ ፡ ካንዱ ፡ ጋራ ፡ ሐሳቡን ፡ የሚለዋወጥበት ፡ መገናኛ ፡ ነው ። ሰው፡ አንድ ፡ ነገርን ፡ ሲገዛ ፡ ወይም ፡ ሲሸጥ ፡ አንድ ፡ ነገርን ፡ ሲዋስ ፡ ወይም ፡ ሲሞክር ፡ ወይም ፡ ሲመከር ፡ ሲያዝ ፡ ወይም ፡ ሲታዘዝ፡ ሐሳቡን ፡ የሚቀበልበትና ፡ የሚሰጥበትም፡ መገናኛ ፡ ነው ። ሰው ፡ በንግግር ፡ ካልሆነ ፡ በስተቀር ፡ በምልክት ፡ ሐሳቡን ፡ እንደ ፡ ልቡ ፡ ለመግለጽ ፡ አይችልም ። ሐሳቡንም ፡ የሚገልጽበት ፡ ቋንቋ ፡ ከሌለው ፡ ለመስጠ ትና፡ ለመቀበል፡ ለማግባባትም ፡ ስለማይችል፡ ትልቅ፡ ድካም ፡ ይሆንበታል። ነገር፡ ግን፡ አሁን ፡ እኔ ፡ ንግግር ፡ ስለ ፡ ተባለው ፡ አርእስት ፡ ስጽፍ ፡ ዋናው ፡ አሳቤ ፡ ቋንቋችንን ፡ እንዴት ፡ እንደምናሰፋው ፡ ሳይሆን ፡ የምናውቀውን ፡ ቋንቋ ፡ ሥራ ፡ የምናሲዝበትን ፡ ዘዴ ፡ ለማወቅ ፡ እንዴት ፡ እንደምንችል ፡ ነው ። ንግግር ፡ በሚከተሉት ፡ አንቀጾች ፡ ይሠራበታል ።

አንድ ፡ ሰው ፡ ካንድ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ ሲነጋገር ፡ የሚፈልገውን ፡ ነገር ፡ እንደሚ ገባው ፡ አድርጎ ፡ ይናገርበታል ። ለምሳሌ ፡ መጽሐፍ ፡ ለመዋስ ፡ ሂዶ ፡ ሳለ ፡ በቤትህ ፡ ብዙ ፡ መጻሕፍት ፡ አሉህ ፡ እያንዳንዳቸውንስ ፡ በስንት ፡ በስንት ፡ ብር ፡ ገዛሃቸው ? ሳይል ፡ የፈለገውን ፡ መጽሐፍ ፡ ስም ፡ ጠርቶ ፡ ይህን ፡ አውሰኝ ፡ ብሎ ፡ ይጠይቀዋል ፡ ማለት ፡ ነው ።

ሰው ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፡ ስሕተት ፡ ከማድረግ ፡ አይታገሥም ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ደግሞ ፡ አንድ ፡ ነገርን ፡ ለመሥራት ፡ ችሎታ ፡ አያገኝም ፡ ወይም ፡ ያገኝ ፡ ይሆ ናል ። ስለዚህ ፡ ንግግር ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ምክሮችን ፡ በምሳሌ ፡ እያደረገ ፡ ሆነ ፡ ወይም ፡ በቀ ጥታ ፡ ሆነ ፡ መስጫ ፡ ይሆናል ።

ማንኛውም ፡ አስተማሪ ፡ ለተማሪዎቹ ፡ የሚሰጠውን ፡ ትምህርት ፡ በቅደም ፡ ተከተልነት ፡ በአእምሮው ፡ ይዞ ፡ በቆንጆ ፡ አማርኛ ፡ እያገጣጠመና ፡ እንደሚገባቸው ፡

አኳኋን ፡ እያደረገ ፡ ይሠራበታል ። ነገር ፡ ግን ፡ ያገጣጠሙ ፡ አኳኋን ፡ በመልካም ፡ ሆኖ ፡ ያልተሰናዳ ፡ እንደሆን ፡ በእርሱና ፡ በተማሪዎቹ ፡ መካከል ፡ ጠብ ፡ ይነሣል ፤ ስለዚህ ፡ ንግግር ፡ ይህ ፡ እንዳይደረግ ፡ ያስጠነቅቃል ።

በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሰው ፡ የበላይና ፡ የበታች ፡ ሆኖ ፡ እንዲሠራ ፡ መደረጉን ፡ ቅዱሳት ፡ መጻሕፍት ፡ ይነግሩናል ። የበላይ ፡ ለበታች ፡ ትክክለኛውን ፡ ትእዛዝ ፡ ሲያስተላልፍ ፡ የንግግርን ፡ አሰጣጥ ፡ ዐቅድ ፡ ያወቀ ፡ እንደሆን ፡ ትእዛዙ ፡ የማያዳግም ፡ ሆኖ ፡ ይሠራበታል ። እንደዚህ ፡ የሆነ ፡ እንደሆን ፡ ታዛዦች ፡ ያዛዦቻቸውን ፡ አንጎል ፡ ደኅና፡ አድርገው ፡ ያነቡበታል ።

ሰዎች ፡ ላንድ ፡ ጉዳይ ፡ በጉባኤ ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡ እያንዳንዳቸው ፡ ሐሳባቸውን ፡ ደረጃ ፡ በደረጃ ፡ እያቀነባበሩ ፡ እንዲህ ፡ ቢሆን ፡ እንዲህ፡ መሆን ፡ አለበት ፡ ወይም፡ የነገሩ ፡ አመጣጥና ፡ አካሄድ ፡ እንዲህ ፡ ከሆነ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ መፍረስ ፡ ይገባዋል ፡ እያሉ፡ ይገልጹበታል ፤ በዚህም ፡ ጊዜ ፡ ፍርድ ፡ መስጠትን ፡ ያስተምራል ።

አንድ ፡ ነገር ፡ በምን ፡ ምክንያት ፡ እንደ ፡ ተነሣና ፡ ምን ፡ ዐይነት ፡ ውጤት ፡ እንደ፡ሰጠ ፡ ይገለጽበታል ፤ ውጤቱ ፡ መልካም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ መልካምነቱ ፡ መጥፎም ፡ እንደሆን ፡ መጥፎነቱ ፡ ይገለጽበታል ።

## ክፍል ፡ ፪ ፡ ንግግርን ፡ የማወቅ ፡ ጥቅም ፡

ሰው ፡ የሚያስፈልገውን ፡ ነገር ፡ ብቻ ፡ በቀላሉና ፡ ባጭሩ ፡ ለመናገር ፡ እንዲችል ፡ የሚያደርግ ፡ ትምህርት ፡ ነው ። ለምሳሌ ፡ አንድ ፡ ገበሬ ፡ ስንዴን ፡ ይዘራና ፡ እየተለባኘ ፡ እልክ ፡ ሲደርስለት ፡ ዐጭዶ ፡ ይወቃል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ምርቱን ፡ ለብቻው ፡ ግርዱንም ፡ ለብቻው ፡ እንችፉንም ፡ ለብቻው ፡ እያደረገ ፡ በያይነቱ ፡ በጎተራው ፡ ይከታል ። የደቀቀውን ፡ ገለባም ፡ ለየብቻው ፡ ያስቀምጠዋል ፤ ወይም ፡ ይቀላቅለዋል ፤ የገለባው ፡ አሠራር ፡ እንደ ፡ እህሉ ፡ አይደለምና ፡ በሰውዬው ፡ ሐሳብ ፡ የሚወሰን ፡ ነገር ፡ ነው ። እንደዚሁም ፡ ንግግር ፡ የሚሰጥ ፡ ሰው፡ ገበሬው ፡ ምርቱን ፡ ግርዱንና ፡ እንችፉን ፡ እየለየ ፡ በደንበኛው ፡ ሥፍራ ፡ እንደሚያስቀምጠው ፡ በንግግሩ ፡ ውስጥ ፡ ዋናውን ፡ ሐሳብ ፡ ካነስተኛው ፡ አነስተኛውንም ፡ በጣም ፡ ዝቅ ፡ ካለው ፡ እየለየ ፡ በያገባባቸው ፡ ይሰጣል ። በተሰጠው ፡ ማስረጃ ፡ የምናገኘው ፡ ጥቅም ፡ ብስልና ፡ ጥሬ ፡ ነገርን ፡ እየለየን ፡ በየቦታቸው ፡ ለማስገባት ፡ ችሎታን ፡ ማግኘት ፡ ነው ።

የንግግር፡ ቅደም፡ ተከተል ፡ የተፋለሰ ፡ እንደ፡ሆነ፡ መግመሪያውና፡ መጨረሻው፡ ይጠፋና ፡ ነገሩ ፡ ውስብስብ ፡ ይሆናል ። ስለዚህ ፡ እንደዚህ ፡ ያለው ፡ አደጋ ፡ እንዳይደርስ ፡ በደንብ ፡ ተዘጋጅቶ ፡ መምጣትን ፡ ያስተምራል ። ቃላት ፡ ባቀነባባሪያቸው ፡ ብርታት ፡ በማጋነን ፡ ሁኔታ ፡ ማሞገስን ፡ ወይም ፡ ማኮሰስን ፡ ይገልጻሉ ። እነዚህን ፡ የመሰሉትን ፡ ስሜቶች ፡ ለመግለጽ ፡ የሚቻለው ፡ የቃላትን ፡ ቅደም ፡ ተከተልነት ፡ በማወቅ ፡ መሆኑን ፡ አጥብቆ ፡ መመልከት ፡ አስፈላጊ ፡ ነው ።

ከማንኛውም ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ በተነጋገሩ ፡ ጊዜ ፡ ለሰውዬው ፡ ተገቢውን ፡ መልስ፡ እየጠበቁ ፡ እንዲናገሩ ፡ ያስተምራል ። ሰው ፡ የሰውን ፡ ደረጃ ፡ እየተረዳ ፡ በያመጣጡ ፡ የሚመለከትበትን ፡ ዘዴ ፡ ከማወቅ ፡ በላይ ፡ ምን ፡ ይፈልጋል ? ዋናው ፡ ሐሳብ ፡ የመጣ ባባትን ፡ ብልኀት ፡ ይህ ፡ ያወጣል ፡ ይህ ፡ ያወርዳል ፡ ብሎ፡ መረዳት ፡ መሆኑን ፡ ማወቅ፡ ይገባል ።

ትልቁንም ፡ እንደ ፡ ትልቅነቱ ፡ አክብሮ ፡ ማነጋገርንና ፡ ትንሹንም ፡ እንደ ፡ ትን ሽነቱ ፡ ሳይንቁ ፡ በሚገባ ፡ ክብር ፡ ተቀብሎ ፡ ማስተናገድን ፡ ስለሚያስተምር ፡ የትል ቅም ፡ የትንሽም ፡ ወዳጅ ፡ ያደርጋል ። ሰው ፡ በመልካም ፡ አንደበቱ ፡ ወዳጅ ፡ የሚገዛ ፡ ከሆነ፡ ስለ ፡ ምን፡ እየተሽቀዳደመ፡ ወዳጅ፡ የሚገዛበትን፡ ብልኀት ፡ አይማርም? ነገር ፡ግን፡ ማንኛውም ፡ የምላስ ፡ ልዝብነት ፡ ከእውነት ፡ ውጭ ፡ የሆነ ፡ እንደሆነ ፡ ከውር ደት ፡ በስተቀር ፡ የሚያተርፈው ፡ ነገር ፡ የለም ፤ ስለዚህ ፡ እንደዚህ ፡ ያለው ፡ አደጋ ፡ ደርሶ ፡ ሥራን ፡ እንዳያሰናክል ፡ እያሰቡ ፡ መሥራት ፡ ታላቅ ፡ ጉዳይ ፡ መሆኑን ፡ ካልተ ገነዘቡ ፡ በመጥፎ ፡ ችግር ፡ ላይ ፡ መውደቅን ፡ ያመጣል ።

## ክፍል ፡ ፫ ፡ የንግግር ፡ አሰጣጥ ፡

አንድ ፡ ሰው ፡ ስለሚናገረው ፡ አርእስት ፡ ደኅና ፡ አድርጎ ፡ ማጥናት ፡ ይገባዋል ። ስለ ፡ አርእስቱ ፡ የሚናገሩትን ፡ መጻሕፍት ፡ እየፈለገ ፡ በተቻለው ፡ መጠን ፡ ማንበብና ፡ ያነበበውን ፡ ፍሬ ፡ ፍሬ ፡ ነገር ፡ በማስታወሻ ፡ መጻፍ ፡ አለበት ። ይህንንም ፡ ከራሱ ፡ ሐሳብ ፡ ጋራ ፡ እያስማማና ፡ እያዋሐደ ፡ የቆነዠ ፡ አስተዋፅኦ ፡ አውጥቶ ፡ በተፈለገው ፡ ሥፍራ ፡ ሄዶ ፡ መናገር ፡ አለበት ፡ እንጂ ፤ ደንበኛውን ፡ ድርሰት ፡ ጽፎ ፡ በቃል ፡ አጥንቶ ፡ መናገር ፡ የለበትም ። ንግግር ፡ በወረቀት ፡ ተጽፎ ፡ የማይነገርበት ፡ ምክንያት ፡ በሰው ነት ፡ ሊገለጹ ፡ የሚገባቸው ፡ ኀይለ ፡ ቃላት ፡ ተሰውረው ፡ እንዳይቀሩ ፡ ነው ። ማንኛ ውም ፡ ንግግር ፡ በራዲዮ ፡ ወይም ፡ በድምፅ ፡ ማጉሊያ ፡ የሚሰጥ፡ የሆነ ፡ እንደሆነ ፡ ግን ፡ ንግግሩ ፡ ተጽፎ ፡ መነበብ ፡ አለበት ።

ደፋር ፡ መሆን ፡ ማለት ፡ ሰውን ፡ መዘርጠጥ ፡ ማለት ፡ አይደለም ። አንድ ፡ ሰው ፡ ንግግርን ፡ ሲያደርግ ፡ በከንቱ ፡ ቢንቀጠቀጥ ፡ ያሰበውን ፡ ንግግር ፡ ከማጥፋት ፡ በስተ ቀር ፡ የሚጨምረው ፡ ነገር ፡ የለምና ፤ በተቻለው ፡ መጠን ፡ ራሱን ፡ መግዛትና ፡ በገዛ ፡ ራሱ ፡ መጽናናት ፡ ያስፈልገዋል ፡ ማለት ፡ ነው ።

ሐሳብ ፡ አካፋይ ፡ ሰው ፡ ንግግርን ፡ ሲሰጥ ፡ ዐዋቂ ፡ ነው ፡ እንዲሉት ፡ ከባድ ፡ የሆኑትን ፡ ቃላት ፡ ባረፍቱ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ አስገብቶ ፡ ምን ፡ ማለቱ ፡ ነው ፡ ከሚሉት ፡ ይልቅ ፡ በመጠነኞች ፡ ቃላት ፡ አሳቡን ፡ ቢገልጥና ፡ ለሁሉም ፡ ጉልሕ ፡ ቢሆንላቸው ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ የተሻለ ፡ ነው ። የሰው፡ ዕውቀት ፡ የሚገመተው ፡ አርእስቱን ፡ በቀላል፡ አማርኛ ፡ አሳክቶ ፡ በመግለጹ ፡ መጠን ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ በንግግሩ ፡ ውስጥ ፡ ከባድ ፡ የሆ ኑትን ፡ (ያልተለመዱትን) ፡ ቋንቋዎች ፡ (ቃላት) ፡ በማስገባቱ ፡ አይደለም ። ዲስኩርን ፡ አዘጋጅቶ ፡ ብቻ ፡ መምጣት ፡ በቂ ፡ ነገር ፡ አይደለም ፤ ባዳማጮቹ ፡ ፊት ፡ በቆመ ፡ ጊዜ ፡

ከሁሉ ፡ አስቀድሞ ፡ አቋቋምን ፡ ማሳመር ፡ ያስፈልገዋል ። ንግግር ፡ የሚሰጠው ፡ ልጅ ፡ ወይም ፡ ወጣት ፡ ወይም ፡ ሙሉ ፡ ሰው ፡ ላዳማጮቹ ፡ መልካም ፡ አቋቋምን ሳያሳይ ፡ በወንበር ፡ ወይም ፡ በጠረጴዛ ፡ ላይ ፡ እየተደገፈ ፡ ወይም ፡ እግሩን ፡ እያጣመረና ፡ ሰውነቱን ፡ እያወጫመደ ፡ ንግግሩን ፡ የሰጠ ፡ እንደሆን ፡ አዳማጮች ፡ ንግግሩን ፡ በመስማት፡ ፈንታ ፡ ሁኔታውን ፡ እያዩ ፡ መሰልቸት ፡ ይገሮምሩና ፡ ገሮራቸውን ፡ ለርሱ ፡ ከመስጠት ፡ ይታገዳሉ ።

በሰውነት ፡ መሥራት ፡ አንድ ፡ ጠቃሚ ፡ ነገር ፡ ነው ። አንድ ፡ ሰው ፡ ንግግር ፡ ሲሰጥ ፡ እጆቹን ፡ እንደ ፡ ሐውልት ፡ አቁሞ ፡ በሰውነቱ ፡ ሊገለጹ ፡ የሚገባቸውን ፡ ነገሮች ፡ ያላገባብ ፡ እያድበሰበሳቸው ፡ ቢያልፍ ፡ የንግግሩ ፡ ዋና ፡ ስሜት ፡ ባዳማጮቹ ፡ ልብ ፡ ሊቀረጽ ፡ አይችልም ፡ ነገር ፡ ግን ፡ እጆቹ ፡ በውኑ ፡ ዋና ፡ ጊዜ ፡ እንደሚሠሩት ፡ እየነዙ ፡ እግሮቹም ፡ እየተንቀሳቀሱ ፡ በኃለ ፡ ምኞት ፡ ተቀስቅሰው ፡ እውነተኛውን ፡ አሳብ ፡ ለመስጠት ፡ የሞከሩ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያዳማጮቹ ፡ ልብ ፡ በቅናት፡ ተሞልቶ ፡ የፈገግታ ፡ ምልክት ፡ በጉልሕ ፡ ይታይባቸዋል ።

አሳብ ፡ ሰጭ ፡ ንግግር ፡ ሲያደርግ ፡ ድምፁን ፡ አንድ ፡ ዐይነት ፡ ማድረግ ፡ የለበትም ። ድምፁ ፡ እንደ ፡ ንግግሩ ፡ ኀይለ ፡ ቃል ፡ ከፍና ፡ ዝቅ ፡ ማለት ፡ አለበት። በንግግር፡ ውስጥ ፡ አንዳንድ ፡ አሳብ ፡ በዝግታ ፡ ተገሮምሮ ፡ እየኃለ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ይወጣና ፡ ዝግ ፡ ብሎ ፡ ይወርዳል ፤ በመካከለኛ ፡ መንፈስ ፡ ይጨረሳል ። እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ንግግር ፡ ለማድረግ ፡ የሚቻልበት ፡ ዘዴ ፡ ቃላትን ፡ ከዝቅተኛ ፡ ሥፍራቸው ፡ ደረጃ ፡ በደረጃ ፡ ቀስ ፡ እያሉ ፡ በማውረድ ፡ ነው። በዚህ ፡ ጊዜ ፡ የቃላት ፡ አሰካክ ፡ ድምፅን ፡ ከፍና ፡ ዝቅ፡ እንዲል ፡ ይረዳዋል ። ምን ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፡ ድምፅ ፡ ከገነነ ፡ ዘንድ ፡ ሰውነት ፡ መሥራት ፡ አይቀርም ።

አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ በብዙ ፡ ቃላት ፡ የሚገለጸውን ፡ ነገር ፡ ምሳሌና ፡ ተረት ፡ እያስገቡ ፡ ባጭሩ ፡ ለማስረዳት ፡ ይቻላል ። ማንኛውም ፡ ንግግር ፡ ከመገሮመሪያው ፡ እስከ ፡ መጨረሻው ፡ በቁም ፡ ነገር ፡ የተመላ ፡ ነው ። ይሁን ፡ እንጂ ፡ የሰሚዎቹ ፡ መንፈስ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ እንዲታደስና ፡ የሚሰጠውን ፡ አሳብ ፡ ባረፈ ፡ አእምሮ ፡ እንዲቀበል ፡ ለማድረግ ፡ የሚያሥቁ ፡ ነገሮችን ፡ በምቹ ፡ ሰዓት ፡ ማስገባት ፡ ያስፈልጋል ። አንዳንድ፡ ጊዜም ፡ ጥያቄ ፡ ቢያቀርቡላቸው ፡ እኔ ፡ እመልስ ፡ እኔ ፡ እመልስ ፡ በማለት ፡ በጣም ፡ ይነቃሉ ፤ ለዚህም ፡ ምቹ ፡ ጊዜ ፡ ያስፈልገዋል ፤ የሚጠየቀውም ፡ ጥያቄ ፡ በጣም ፡ ከባድ፡ ሳይሆን ፡ ዋጋ ፡ ያለው ፡ እንዲሆን ፡ አስፈላጊ ፡ መሆኑን ፡ አለመሳት ፡ ነው ።

ዲስኩር ፡ አድራጊ ፡ ለመሆን ፡ የሚማር ፡ ሰው ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ከመጽሐፍ ፡ ላይ ፡ በማጥናት ፡ ሳይሆን ፡ በመሥራት ፡ ልማድ ፡ እንዲያደርግበት ፡ መጣጣር ፡ ይገባዋል ። አንድ ፡ ሕፃን ፡ ልጅ ፡ ገና ፡ ለመቆምና ፡ ለመሄድ ፡ ሲገሮምር ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ መፍረጥና ፡ መነሣት አንዳንድ ጊዜም መከስከስ ፡ አለበት ። ነገር ፡ ግን ፡ ርሱ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ሳይሰለችና ፡ ሳይሰቀቅ ፡ ይቀጥላል ። ከቀን ፡ ብዛት ፡ ሙከራ ፡ በማድረግ ፡ ቀጥ ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ ልቡ ፡ ለመቆምና ፡ እንደ ፡ ልቡ ፡ ለመሄድ ፡ ይችላል ። እንደዚሁም ፡ አንድ ፡

ተማሪ ፡ ሳይሰለችና ፡ ሳይበሳጭ ፡ ሥራውን ፡ ባለማቋረጥ ፡ የቀጠለ ፡ እንደሆነ፡በመጨረሻው ፡ በሥራው ፡ ላይ ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ የሠለጠነ ፡ ይሆናል ፤ ስለዚህ ፡ አንድ ፡ የዲስኩር ፡ ተማሪ ፡ ሥራውን ፡ በዚህ ፡ መንገድ ፡ መቀጠል ፡ አለበት ።

## ክፍል ፡ ፩ ፡ ንግግርና ፡ ድርሰት ፡

መዠመሪያ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ድርሰትን ፡ ከመጻፉ ፡ በፊት ፡ የሚያውቀውንና ፡ የሚወደውን ፡ አርእስት ፡ ይመርጣል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ፍሬ ፡ ፍሬ ፡ ነገሮችን ፡ ባሳቡ ፡ እንደ ፡ መጣለት ፡ ይጽፍና ፡ ሲያበቃ ፡ በቅደም ፡ ተከተልነት ፡ አዘጋጅቶ ፡ ዋናውን ፡ ድርሰት ፡ መጻፍ ፡ ይዠምራል ። ቀጥሎም ፡ እስከ ፡ መጨረሻው ፡ ድረስ ፡ የቃላቱን ፡ አሰካክና ፡ ያሳቡን ፡ስምምነት ፡ እየተመለከተ ፡ በተቻለው ፡ መጠን ፡ በጥንቃቄ ፡ ይሠራል ። ስለዚህ ፡ የድርሰቱ ፡ አሳብ ፡ በጽሑፍ ፡ እንጂ ፤ በሌላ ፡ ዘዴ ፡ ለሰው ፡ ሊሰጥ፡ አይቻልም።

መካሪ ፡ ሰው ፡ ንግግር ፡ ለማድረግ ፡ ሲያስብ ፡ ወይም ፡ ንግግርን ፡ እንዲሰጥ ፡ ቢጠየቅ ፡ ላሰበው ፡ ጉዳይ ፡ ወይም ፡ ለታዘዘበት ፡ ጉዳይ ፡ ተስማሚውን ፡ አርእስት ፡ መርጦ ፡ ስለ ፡ ርሱ ፡ ብዙ ፡ ነገሮችን ፡ ለማወቅ ፡ እየጠየቀም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ መጻሕፍትን ፡ እያነበበ ፡ ወሬን ፡ ይሰበስባል ። በነገሩም ፡ ርግጠኛ ፡ ከሆነ ፡ በኋላ ፡ አስተዋፅኦ፡ ይነድፍና፡ የቃላትን፡ አገባብ ፡ በደንብ ፡ አደራጅቶ፡ ወደሚናገርበት፡ ሥፍራ ፡ ይመጣል ።

ንግግሩን ፡ ሲሰጥ ፡ ካልተሳተው ፡ በስተቀር ፡ አስተዋፅኦን ፡ መመልከት ፡ የለበትም ። ድርሰትም ፡ ሆነ ፡ ወይም ፡ ንግግር ፡ የሚዘጋጀው ፡ ባይን ፡ ከታየው ፡ በዦሮ ፡ ከተሰማው ፡ አንብቦ ፡ ከመጽሐፍ ፡ ከተገኘውና ፡ ብዙ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ነገሮችን ፡ ሰብስቦ ፡ አሳብ ፡ አመዛዝኖ ፡ ካያዘው ፡ ነው ። በዚህ ፡ ረገድ ፡ ሁለቱም ፡ አንድ ፡ ናቸው ፤ ማንኛውም ፡ ነገር ፡ ቅርጽና ፡ መልክ ፡ ካለው ፡ ባይን ፡ ብቻ ፡ ታይቶ ፡ በሚሠራው ፡ ግብሩ ፡ ጉልሕ ፡ ሆኖ ፡ ስለሚታይ ፡ ሊገለጽ ፡ ይቻላል ።

በዦሮ ፡ ከተሰማው ፡ ማለት ፡ እናት ፡ አባት ፡ ወይም ፡ እኅቶችና ፡ ወንድሞች ፡ ወይም ፡ ጎረቤቶችና ፡ ባልንጀሮች ፡ ከተናገሩት ፡ ማለት ፡ ነው ።

እንደዚህ ፡ ያለው ፡ ነገር ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ ሁለት ፡ ነገር ፡ ይነገራል ። አንደኛው ፡ ከተረት ፡ ሌላው ፡ ደግሞ ፡ ባይን ፡ ከታየው ፡ ነው ። ሁለቱም ፡ ባንድ ፡ ሊነገሩ ፡ የሚቻልበትም ፡ ጊዜ ፡ ይገኛል ። የሕይወት ፡ ታሪኩ ፡ ሲነገር ፡ መጠኑና ፡ ግብሩ ፡ የሠራቸው ፡ ሥራዎች ፡ የሠራባቸው ፡ ጊዚያት ፡ እንደዚሁም ፡ ስለምን ፡ እንደ ፡ ሠራቸው ፡ ስለሚጠቀሱ ፡ ነው ።

ከመጽሐፍ ፡ ከተገኘውና ፡ አእምሮ ፡ አመዛዝኖ ፡ ካፈለቀው ፡ ማለት ፡ በሕይወት ፡ ከገፉ ፡ ዘንድ ፡ በመስማት ፡ በማየትና ፡ በመሥራት ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ልማድ ፡ ስለሚገኝ ፡ የሚጠቅመውንና ፡ የሚጎዳውን ፡ በማወቅ ፡ መጻሕፍትም ፡ በውስጣቸው ፡ ብዙ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ነገሮችን ፡ ስለሚይዙ ፡ እነርሱን ፡ አንብቦ ፡ አእምሮን ፡ በወሬ ፡ በመሙላት፡ ነው።ስለዚህ፡ ስለ ፡ ድርሰትና ፡ ስለ ፡ ንግግር ፡ ወሬን ፡ በመሰብሰብ ፡ ልዩ ፡ ነገር ፡ የለም።

በንግግር ፡ ውስጥ ፡ ታላቁ ፡ ጥቅም ፡ ድምፅን ፡ ከፍና ፡ ዝቅ ፡ በማድረግ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ኀይለ ፡ ቃላት ፡ መግለጻቸው ፡ ነው ። አወዳደቅና ፡ አነሣሥ ፡ ያዳማጮቹን ፡ መንፈስ ፡ ይማርካሉ ። እንደዚሁም ፡ በሰውነት ፡ ተፈላጊ ፡ ነገር ፡ ሊገለጽ ፡ ይቻላል ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ በሰውነት ፡ የሚገለጸው ፡ ነገር ፡ ያዳማጮቹን ፡ ስሜት ፡ የሚገልጽና ፡ የሚያነቃቃ ፡ አለበት ። ስለዚህ ፡ ንግግር ፡ የሚሰጥ ፡ ሰው ፡ ልብ ፡ የሚሞትበትን ፡ ጉድለት ፡ ተጠንቅቆ ፡ እያረመ ፡ በጋለ ፡ መንፈስ ፡ የሚያነቃቃ ፡ የሰውነት ፡ አገላለጽ ፡ ትምህርትን ፡ በጣም ፡ ተግቶ ፡ ማጥናት ፡ አለበት ።

ምንም ፡ እንኳ ፡ አርእስት ፡ አሳብን ፡ ለሰው ፡ ሲያቀርቡባቸው ፡ በጥቂት ፡ ነገሮች ፡ ቢለያዩ ፡ ሁለቱም ፡ የሚፈለገውን ፡ ሐሳብ ፡ ይገልጻሉ ። ስለዚህ ፡ የድርሰትን ፡ አጸጻፍ ፡ ትምህርት ፡ እየፈለፈሉና ፡ እያደቀቁ ፡ ያጠኑት ፡ እንደሆን ፡ ለንግግር፡ አሰጣጥ፡ በጣም ፡ ይረዳል ። ማንኛውም ፡ ትምህርት ፡ ከሌላው ፡ ትምህርት ፡ ጋራ ፡ የተደጋገፈ ፡ በመሆኑ ፡ አንደኛው ፡ ተጠንቶ ፡ ለሌላው ፡ ደጋፊ ፡ ሆኖ ፡ ሲገኝ ፡ ታላቅ ፡ ደስታን ፡ ይሰጣል ። ለምሳሌ ፡ የጂኦግራፊ ፡ ትምህርት ፡ ከሳይንስና ፡ ከታሪክ ፡ ጋራ፡ የተያያዘ ፡ ነገር፡ ስላለበት ፡ ጠቅላላ ፡ ዕውቀት ፡ የሚሰጠውን ፡ የሳይንስንና ፡ የታሪክን ፡ ትምህርት ፡ ደኅና ፡ አድርገው ፡ ከተማሩ ፡ የጂኦግራፊ ፡ ትምህርት ፡ በቀላሉ ፡ ይጠናል ። ስለዚህ ፡ ልዩ፡ ልዩ፡ አርእስትን፡ በማወዳደር ፡ ወይም ፡ በማመሳሰል ፡ ወይም፡ በማማረጥ ፡ በኩል፡ ቢመለከቷቸው ፡ በብዙ ፡ ሳይደከምባቸው ፡ በቀላሉ ፡ ይጠናሉ ። እንግዲህ ፡ ዋናው ፡ ትምህርት ፡ ያለፈው ፡ ነገር ፡ ካሁኑ ፡ ጋራ ፡ የሚዛመድበትንና ፡ የሚለያይበትን ፡ መለየት ፡ መሆኑን ፡ አጥብቆ ፡ መረዳት ፡ ነው ።

## የንግግርን ፡ አሰጣጥ ፡ ለማረም ፡ የሚረዱ ፡ ነገሮች ፡

በክፍል ፡ ውስጥ ፡ ሆነ ፡ ወይም ፡ በውጭ ፡ ዲስኩር ፡ በሚደረግበት ፡ ሥፍራ ፡ መሄድና ፡ መስማት ፡ ታላቅ ፡ ጠቃሚ ፡ ነገር ፡ ነው ። ሰዎች ፡ በተፈጥሮ ፡ ጠባያቸው ፡ የተለያዩ ፡ ናቸው ፤ ከዚህም ፡ የተነሣ ፡ ንግግር ፡ የሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ባቋቋማቸውና ፡ በዲስኩር ፡ አሰጣጣቸው ፡ አንድ ፡ አይደሉም ። ስለዚህ ፡ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ እነርሱን ፡ እያማረጠ ፡ የተሻለውን ፡ ለመያዝ ፡ ይችላል ።

ራዲዮንም ፡ መስማት ፡ የዕለት ፡ ወሬን ፡ ከማግኘት ፡ በላይ ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ የትልልቆችን ፡ ንግግር ፡ ለመካፈል ፡ ያስችላል ።

ዲስኩር ፡ የሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ መንገዳቸው ፡ አንድ ፡ አይደለም ። እያንዳንዳቸው ፡ ያዳማጮቻቸውን ፡ መንፈስ ፡ የሚስቡባቸው ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ዘዴዎች ፡ አሏቸው ። እንግዲህ፡ ይህን ፡ ትምህርት ፡ ለማጥናት ፡ ፍላጎት ፡ ያለው፡ ሰው ፡ ዲስኩረኞችን፡ እየለየ ፡ ያጠናቸውና ፡ ባንደኛው ፡ ዲስኩረኛ ፡ ጊዜ ፡ መንፈሱን ፡ (አሳቡን) ፡ ለማሠራት፡ ይቀርጣል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በሚያገኘው ፡ አሳብ ፡ የራሱን ፡ ጉድለት ፡ እያረመ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ልማድ ፡ ያደረገበት ፡ እንደሆን ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ በዚህ ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ ታጥቆ ፡ ተነሥቷልና ፡ ጥሩ ፡ ዲስኩረኛ ፡ ወይም ፡ ተናጋሪ ፡ ይወጣዋል ።

ዲስኩር ፡ በሚነገርበት ፡ ክፍል ፡ ወይም ፡ አዳራሽ ፡ ገብቶ ፡ ዲስኩረኛውን ፡ ብቻ ፡ መመልከት ፡ በቂ ፡ አይደለም ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ አዳማጮች ፡ በሚሰጠው ፡ ንግግር ፡ መደሰትና ፡ አለመደሰታቸውን ፡ ለማወቅ ፡ ገጻቸውን ፡ ማንበብ ፡ ያስፈልጋል። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ በእውነተኛው ፡ ነገር ፡ ዲስኩረኛው ፡ ያዳማጮችን ፡ መንፈስ ፡ መማረኩንና ፡ አለመማረኩን ፡ ለማወቅ ፡ ይችላል ። ስለዚህ፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ ዲስኩሮችን ፡ ወይም፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ ተማሪዎችንና ፡ አስተማሪዎችን ፡ ዲስኩር ፡ በማዳመጥ ፡ ብዙ ፡ ነገሮችን ፡ ለማረምና ፡ ለማሻሻል ፡ የሚቻልበት ፡ ዘዴ ፡ ይገኛል ።

## የንግግር ፡ አሰጣጥ ፡ ዓላማ ፡ አስተዋፅኦ ፡

፩ ፡ አሳብን ፡ ሰብስቦና ፡ አሳክቶ ፡ ማሰማት ፡ ያዳማጮቹን ፡ መንፈስ ፡ የሚማርከውን ፡ አርእስት ፡ መምረጥ ፡

፪ ፡ የመዠመሪያው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ አዳማጮቹን ፡ ከአርእስቱ ፡ ጋራ ፡ ደኅና ፡ አድርጎ ፡ እንዲያስተዋውቃቸው ፡ ማድረግ

፫ ፡ አርእስቱን ፡ እንደ ፡ ሕፃን ፡ ልጅ ፡ ደረጃ ፡ በደረጃ ፡ እያደረጉ ፡ እስከ ፡ መጨረሻው ፡ ድረስ ፡ ማሳደግ ፡

፬ ፡ ላሳደጉት ፡ ሐሳብ ፡ በመንፈስ ፡ የሚቀረጽ ፡ ማሰሪያ ፡ (መዝጊያ) ፡ ማበጀት ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ፡ አስተዋፅኦ ።

አስተዋፅኦ ፡ አንድ ፡ የተጻፈ ፡ ነገርን ፡ ወይም ፡ በአእምሮ ፡ ውስጥ ፡ የተያዘ ፡ ነገር ፡ ፍሬ ፡ ፍሬ ፡ ነገርን ፡ በቅደም ፡ ተከተልነት ፡ ለቅሞ ፡ መጻፍ ፡ ነው ።

ከዚህ ፡ በፊት ፡ እንዳስረዳነው፡ ድርሰትና ፡ ንግግር፡ ባሰጣጥ ፡ ላይ፡ ነው ፡ እንጂ፡ በማሰናዳት ፡ ረገድ ፡ አንድ ፡ ናቸው ፡ ብለናል ። ድርሰትና ፡ ንግግር ፡ ሲዘጋጁም ፡ በሦስት ፡ ላይ ፡ መመደብ ፡ አለባቸው ። እነርሱም ፡ መግቢያ ፡ ሐተታና ፡ መዝጊያ ፡ ናቸው ።

መግቢያ ፡ የሚባለው ፡ ክፍል ፡ አርእስቱን ፡ ካንባቢው ፡ ወይም ፡ ካዳማጮቹ ፡ ጋራ ፡ የምናስተዋውቅበት ፡ ነው ። ይህ ፡ ክፍል ፡ ስለ ፡ አርእስቱ ፡ ደኅና ፡ መግለጫ ፡ የያዘ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አንባቢው ፡ ወይም ፡ አዳማጮቹ ፡ የሚቀጥለውን ፡ ሐተታ ፡ በናፍቆት ፡ ይጠባበቃሉ ።

ሐተታ ፡ የምንለው ፡ አርእስቱን ፡ በሥዕላዊ ፡ ድርሰት ፡ አጻጻፍ ፡ ደንብ ፡ የምንገልጽበት ፡ ክፍል ፡ ነው ። በዚህ ፡ ክፍል ፡ አርእስቱን ፡ በማወዳደር ፡ ወይም ፡ በማመሳሰል ፡ ወይም ፡ ባይነቱ ፡ በመኖሪያው ፡ በሚሰጠው ፡ ጥቅምና ፡ ጉዳት ፡ እናትትበታለን ።

መዝጊያ ፡ የጻፍነውን ፡ ድርሰት ፡ ወይም ፡ የሰጠነውን ፡ ንግግር ፡ አመዛዝነን፡ ሐሳባችንን ፡ የምንሰጥበት ፡ ክፍል ፡ ነው ።

ከዚህ ፡ በላይ ፡ ስለ ፡ ተገለጸው ፡ የሚከተሉትን ፡ አስተዋፅኦ ፡ ተመልከት ።

## ድርሰት ፡ ስለ ፡ እንስሳት ፡

ስለ ፡ እንስሳት ፡ ድርሰት ፡ ሲጻፍ ፡ በአእምሮ ፡ ሊታወሱ ፡ የሚገባቸው ፡ ነገሮች ፡ እንደሚከተሉት ፡ በአስተዋፅኦ ፡ ደንብ ፡ ተጽፈዋል ፤ ድርሰቱንም ፡ በሦስት ፡ ታላላቅ ፡ ክፍል ፡ ከፍለነዋል ።

(ሀ) ጠቅላላ ፡ ድርሰት ፡
(ለ) ነጠላ ፡ ድርሰት ፡
(ሐ) ልዩ ፡ ድርሰት ፡

### ስለ ፡ እንስሳት ፡ ጠቅላላ ፡ ድርሰት ፡

### አስተዋፅኦ ፡

፩ ፤ መግቢያ ፡

(ሀ) አምስቱ ፡ ሕዋሳት ፡
አንዳንዶቹ ፡ ባምስቱ ፡ ትክክል ፡ አይሠሩባቸውም ።

(ለ) የቤትና ፡ የዱር ፡ እንስሳት ፡

(ሐ) ማስተዋል ፡- አንዳንዶቹ ፡ ከሌሎቹ ፡ የተለየ ፡ ብልጠት ፡ አላቸው ።

(መ) አገልግሎት ፡

፪ ፤ ሐተታ ፡

(ሀ) ዐይነታቸው ፡

1 መልክ ፡- ጥቍር ፡ ቀይ ፡ ዳለቻ ፡ ሌጉማ ፡
2 ቁመት ፡- ረዥም ፡ አጭር ፡
3 ግዝፈት ፡- ወፍራም ፡ ቀጭን ፡
4 ግብር ፡- ገር ፡ ክፉ ፡ ጠንካራ ፡

(ለ) መኖሪያቸው ፡

1 ደጋ ፡ አንዳንዶቹ ፡ ጸጉር ፡ አላቸው ፤ ብርድን ፡ ይቃወማሉ ።
2 ወይና ፡ ደጋ ፡ የሚፈልጉትን ፡ ምግብና ፡ አየር ፡ ንብረት ፡ ያገኛሉ ።
3 ቆላ ፡ የሚፈልጉትን ፡ ምግብና ፡ አየር ፡ ንብረት ፡ ያገኛሉ ።
4 በውኃ ፡ ውስጥ ፡ በየዋሻው ፡
5 ልዩ ፡ ስፍራ ፡
(ሀ) ዋሻ ፡
(ለ) ደን ፡ (ጫካ) ፡
(ሐ) ገደል ፡ (ጥግ) ፡
(መ) ዛፍ ፡

(ሐ) ኑሯቸው ፡

1 ለብቻ ፡ (እየተነጠሉ) ፡
2 በማኅበር ፡
እንደዚህ፡ የሚባለው፡ላም፡ ፍየል፡ በግና፡የጋማ፡ከብት፡አብረው፡ሲውሉ፡ነው።
3 በቤት ፡ ሰብ ፡
(እንደዚህ፡ የሚባለው፡ የበግ፡መንጋ፡ ብቻ ፡ አብሮ ፡ ሲውል ፡ ነው ) ።
(ሀ) ሙክት ፡
(ለ) ወጠጤ ፡
(ሐ) ጠቦት ፡
(መ) ቄብ ፡
(ሠ) እናት ፡
በዚሁ፡ ዐይነት፡ለሁሉም፡ ይሠራል።

(መ) ምግባቸው ፡

1 ሣርና ፡ ቅጠል ፡ ርጥብ ፡ ደረቅ ፡
2 ሥጋና ፡ ሣር ፡
3 አፈርና ፡ ሥጋ ፡
4 ሥጋ ፡ ብቻ ፡

(ሠ) ጥቅማቸው ፡

1 በጉልበት ፡ ለዕቃ ፡ ለኮርቻ ፡
2 በሥጋ ፡ ምግብ ፡
3 በቆዳ፡ ለጫማ ፡ ለጠፍር፡ ለስልቻ፡
4 በቅባት ፡
5 በጸጉራቸው ፡
6 በቀንዳቸውና ፡ በሰኮናቸው ፡

(ረ) የሚያመጡት ፡ ጉዳት ፡

1 አዝርዕትን ፡ ማጥፋት ፡
በውስጡ ፡ እየሄዱ ፡

2 ሰውን ፣ መጣላት ፣
3 እርስ ፣ በርስ ፣ መባላት ፣
4 ቆዳና ፣ ሥጋቸው ፣ መጣሉ ፣
(በጣም ፣ አስፈላጊ ፣ አይደለም)።

(ሰ) አረባባቸው ፣
1 ኮርማ ፣ (አውራ) ፣
2 እንስት ፣
(ሀ) ባምስት ፣ ወር ፣
(ለ) በዘጠኝ ፣ ወር ፣
(ሐ) አጥብቶ ፣ ማሳደግ ፣

፫ ፣ መዝጊያ ፣

(ሀ) ማድረግ ፣ የሚገባን ፣
1 አንዳንዶቹን ፣ ማጥፋት ፣
2 የቤት ፣ የሆኑትን ፣ እየመረጡ ፣ ማዋለድ ፣
3 ለመኖሪያቸውና፣ለምግባቸው፣መጠንቀቅ፣

(ለ) አስተያየት ፣

ነጠላ ፣ ድርሰት ፣ ስላንድ ፣ እንስሳ ፣

፩ ፤ መግቢያ ፣

(ሀ) አምስቱን ፣ ሕዋሳት ፣
1 መስማት ፣
2 ማሽተት ፣
3 ማየት ፣
4 መቅመስ ፣
5 መዳሰስ ፣
} በያይነቶቹና ፣ በጣም ፣ እንደሚ ሠራባቸው ፣ መጣ ለጽ ፣

(ለ) የቤት ፣ ወይም ፣ የዱር ፣

(ሐ) ማስተዋል ፣ ከሌሎቹ ፣ ይሻላል ፣ ወይስ ፣ አይሻልም ።

(መ) አገልግሎቱ ፣ በምን ፣ ነው ?

፪ ፤ ሐተታ ፣

(ሀ) ዐይነት፣-ነጭ፣ ብጫ ፣ በቃ ፣ ዶግማ ፣
መልክ ፣ -
ቁመት ፣ አጭር ፣ ረዥም ፣ ትንሽ ፣
ግዝፈት ፣ (መጠን) ፣
ጠባይ ፣ (ግብር) ፣

(ለ) መኖሪያው ፣
ቆላ ፣
ደጋ ፣
ወይና ፣ ደጋ ፣
ልዩ ፣ ሥፍራ ፣
ዋሻ ፣
ደን ፣
ገደል ፣
ዛፍ ፣

(ሐ) ኑሮው ፣
ለብቻው ፣
በማኅበር ፣
ቤተ ፣ ሰቡ ፣

(መ) ምግቡ ፣
1 ሣርና ፣ ቅጠል ፣
2 ሥጋ ፣ ብቻ ፣
3 ሥጋና ፣ ሣር ፣
4 አፈርና ፣ አመድ ፣
5 ቆሻሻና ፣ ሥጋ ፣

(ሠ) ጥቅሙ ፣
1 በጕልበት ፣
2 ምግብ ፣ በመሆን ፣
3 በቆዳው ፣
4 በቅባቱ ፣
5 በጸጕሩ ፣
6 በቀንዱና ፣ በስኮናው ፣

(ረ) ጉዳቱ ፣
1 አዝርዕትን ፣ ማጥፋት ፣
2 ሰውን ፣ መጣላት ፣
3 ሌላውን ፣ መብላት ፣
4 ሥጋውና፣ ቆዳው፣ መጣሉ፣

(ሰ) ባረባቡ ፣
1 ኮርማ ፣ (አውራ) ፣
2 እንስት ፣

3 አምስት ፡ ወር ፡
4 ዘጠኝ ፡ ወር ፡
5 አጥብቶ ፡ ማሳደግ ፡

፫ኛ ፡ መዝጊያ ፡

(ሀ) ማድረግ ፡ የሚገባን ፡

1 አመዛዝኖ ፡ ጉዳቱ፡ ከሚሰጠው፡ ጥቅም ፡ ከበለጠ ፡ ማጥፋት ፡
2 እየመረጡ ፡ ማራባት ፡
3 ለምግቡ ፡ መጠንቀቅ ፡
4 ለመኖሪያው ፡ ቤትን፡ መሥራት፡

(ለ) አስተያየት ፡

ልዩ ፡ ድርሰት ፡

ሦስተኛው ፡ ከነጠላው፡ ወይም ፡ ከጠቅላላው፡ ድርሰት ፡ ውስጥ ፡ አንዱን፡ ክፍል፡ ወስደን ፡ ከሌላ ፡ ወይም ፡ ከሌሎቹ ፡ ጋራ ፡ እያወዳደርን ፡ ወይም ፡ እያመሳሰልን፡ የምንጽፈው፡ ድርሰት ፡ ነው። አጻጻፉም ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ በተሰጡት ፡ ዐቅድ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከመዘርዘር ፡ ታግሠናል ።

ከብረት ፡ ለተሠራ ፡ ዕቃ ፡ አስተዋፅኦ ፡

፩ ፡ ዕቃው ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ መግለጽ፡

1 ቅርጹን ፡ ለይቶ ፡ መግለጽ ፡
2 ጠንካራነቱን ፡ ወይም ፡ ልልነቱን ፡ ማስረዳት ፡

፪ ፡ ሥር ፡ መሠረቱ ፡ ከምን ፡ ተገኘ ፡

1 ከመሬት ፡ ውስጥ ፡
2 መሐንዲስ፡ መርምሮ፡ማግኘቱን፡
3 ሠራተኞች ፡ ቆፍረው ፡ ማውጣታቸውን ፡ ማወቅ ፡

፫ ፡ ያስቆፈረው ፡

1 በማመላለሻ ፡ እንደ ፡ ላከው ፡ ማወቅ ፡
2 ዕቃው ፡ ሲወርድና ፡ ሲወጣ ፡ ብዙ ፡ ድካም ፡ እንዳለበት ፡ መረዳት ፡

፬ ፡ ፕላን ፡ አንሺው ፡(ነዳፊው) ፡

1 አስቦ ፡ በአእምሮ፡ ውስጥ ፡ መገምሪያ ፡ የሚሠራውን ፡ ነገር ፡ መቅረጹን ፡ መገንዘብ ፡
2 በወረቀት ፡ ላይ ፡ መንደፉን ፡
3 ቀጥሎ ፡ ዕቃው ፡ መሠራቱንና ፡ በመገምሪያ ፡ የተሠራው ፡ ተስማሚ፡ መሆኑን፡ ማሰብ፡ ቢበላሽ፡ እንኳ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ተሻሽሎ ፡ እንዲሠራ ፡ መደረጉን ፡
4 በፕላኑ፡ መሠረት፡ ተሠርቶ፡ጠቃሚነቱ ፡ ሲታወቅ ፡ በብዙ ፡ መሸጡን ፡

፭ ፡ታሪኩ ፡

1 ለምን ፡ እንደ ፡ ተሠራ ፡
2 ማን ፡ እንደ ፡ ሠራው ፡
3 መቼ ፡ እንደ ፡ ሠራው ፡
4 እንዴት፡አድርጎ፡ እንደ፡ ሠራው፡
(ሀ) ባንድ ፡ ቦታ ፡ መቅለጡን ፡
(ለ) ለማቅለጫ ፡ ያስፈለጉ ፡ ነገሮች ፡
(ሐ) እንደ ፡ ገና ፡ ከምን፡ ጋራ፡ ተደባልቆ፡ እንደ ፡ ተሠራ ፡

፮ ፡ አምጪው ፡

1 ነጋዴ ፡
2 በምን ፡ እንዳመጣው ፡

፯ ፡ ምን፡ዐይነት፡ ጥንቃቄ፡እንዳስፈለገው፡

ስለ ፡ እንስሳት ፡ በወጣው ፡ አስተዋፅኦ ፡ በድርሰት ፡ ክፍል ፡ ስለ ፡ በቅሎና ፡ ስለ፡ ንብ ፡ የተጻፉትን ፡ ድርሰቶች ፡ ተመልከት ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

### ክፍል ፡ ፩ ፡ አኅጽሮተ ፡ ጽሑፍ ፡

አኅጽሮተ ፡ ጽሑፍ ፡-በረዥሙ ፡ የተጻፈውን ፡ ጽሑፍ ፡ ፍሬ ፡ ፍሬ ፡ ነገር፡ ለቅሞ፡ አስካኩን ፡ በተዋበ ፡ አማርኛ ፡ መጻፍ ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ በብዙ ፡ ቃላት ፡ የተዘጋጀውን ፡ (የተቀነባበረውን) ፡ ጽሑፍ ፡ በተቻለ ፡ መጠን ፡ አሳጥሮ ፡ አሳቡን ፡ ሳያስቀሩ ፡ በሙሉ ፡ መግለጽ ፡ አስፈላጊ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፤ ያጠረውን ፡ ጽሑፍ ፡ ፍሬ ፡ ፍሬ ፡ ነገሮች ፡ ተራ ፡ ሰው፡ አንብቦ ፡ ለመረዳት ፡ እንዲችል ፡ ቅዱ ፡ አጭር ፡ ግልጽና ፡ ትክክለኛውን ፡ መሠረታዊ ፡ አሳብ ፡ እንዲሰጥ ፡ ማድረግ ፡ ይገባል ።

አኅጽሮተ ፡ ጽሑፍ ፡ ከዚህ ፡ ቀደም ፡ ባገራችን ፡ በጣም ፡ የተለመደ ፡ አይደለም ። ከዚህም ፡ የተነሣ ፡ ስለ ፡ አኅጽሮተ ፡ ጽሑፍ ፡ የሚናገር ፡ መጽሐፍ ፡ አይገኝም ፤ በእንግሊዘኛ ፡ መጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡ ተመለከትሁት ፡ የቅዱ ፡ (ያጠረው) ፡ ቃላት ፡ ከዋናው ፡ ከእናቱ ፡ ጽሑፍ ፡ ቃላት ፡ በአንድ ፡ ሦስተኛ ፡ ያህል ፡ ማጠር ፡ ይገባቸዋል ፡ ይላል ። እንዲህ ፡ ከሆነ ፡ አንድም ፡ እያሰኙ ፡ ትርጓሜ ፡ በሚያራቅቁትና ፡ ወይም ፡ በሚያሰኙት ፡ ቃላት ፡ ከመሥራት ፡ መታገሥ ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ ነገር ፡ ነው ።

### ክፍል ፡ ፪ ፡ የአኅጽሮተ ፡ ጽሑፍ ፡ ጥቅም ፡

አንድ ፡ ሠራተኛ ፡ የተሰጠውን ፡ ነገር ፡ አሳጥረህ ፡ ጻፍ ፡ በተባለ ፡ ጊዜ ፡ ጽሑፉን ፡ በማስተዋል ፡ እያነበበ ፡ ሲጽፍ ፡ አእምሮውን ፡ ሰብስቦ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ይጥልና ፡ የሚያነበውን ፡ ነገር ፡ ባይኑ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ በአእምሮው ፡ እያስተዋለ ፡ እንዲይዘው ፡ አስገድዶ ፡ ያስተምረዋል ።

ማሳጠር ፡ በተንዛዛ ፡ አማርኛ ፡ ቅደም ፡ ተከተሉን ፡ እያበላሸን ፡ እንዳንጽፍ ፡ ያስጠነቅቀናል ። እንደዚሁም ፡ አንድ ፡ ቅጥ ፡ የለሽ ፡ ንግግር ፡ ሰጭ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ የሚፈጅበትን ፡ ዲስኩር ፡ (ንግግር) ፡ አንድ ፡ ጥንቁቅ ፡ ሰው ፡ በጥቂት ፡ ደቂቆች ፡ ውስጥ ፡ አቀላጥፎ ፡ እንደሚሰጥ ፡ ያስተምራል ፤ በዚህም ፡ ጊዜ ፡ ሰውዬው ፡ ይህን ፡ ችሎታ ፡ ያገኘው ፡ ተፈላጊዎቹን ፡ ቃላት ፡ እየመረጠ ፡ በደንበኛ ፡ ሥፍራቸው ፡ በማስገባት ፡ መሆኑን ፡ አጉልቶ ፡ ያሳያል ።

ስለዚህ ፡ ባሁኑ ፡ ዘመናችን ፡ የአኅጽሮተ ፡ ጽሑፍን ፡ አጻጻፍ ፡ ልማድ ፡ ማድረግ፡ ለልዩ ፡ ልዩ ፡ ሥራዎች ፡ ዋና ፡ ዐይነታቸው ፡ ነው ። በዚህም ፡ ዘዴ ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ የሚጠቀሙበት ፡ የመንግሥት ፡ ሠራተኞች ፡ ነጋዴዎች ፡ ጠበቆችና ፡ ቴሌግራም ፡ ላኪዎች ፡ ናቸው ።

ማስገንዘቢያ ፡

አንድም ፡ ይቅር ፡ የተባለው ፡ እንዲያጥሩ ፡ በሚፈልጉት ፡ ጽሑፎች ፡ ውስጥ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በቅዱሳት ፡ መጻሕፍት ፡ አይደለም ።

## ክፍል ፡ ፫ ፡ የአኅጽሮተ ፡ ጽሑፍ ፡ አጻጻፍ ፡ ዘዴ ፡

አንድ ፡ የወርቅ ፡ አንጥረኛ ፡ ወርቅን ፡ በከውር ፡ (አጎዶ) ፡ አንጥሮ ፡ እንደሚሠራው ፡ ሁሉ ፡ ያንድ ፡ አኅጽሮተ ፡ ጽሑፍን ፡ እንብርት ፡ አፍርጦ ፡ ማሳየት ፡ አስፈላጊ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አሳብን ፡ ሰብስቦ ፡ ደኅና ፡ አድርጎ ፡ ማሠራት ፡ ግዴታዊ ፡ ነገር ፡ ነው ።

መዠመሪያ ፡ ጠቅላላውን ፡ አሳብ ፡ ለማግኘት ፡ በመካከለኛ ፡ ፍጥነት ፡ አንብብ፤ ያልገባህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ግን ፡ እየመላለስህ ፡ እስኪገባህ ፡ ድረስ ፡ አንብበው ። አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ለአኅጽሮተ ፡ ጽሑፍ ፡ አርእስት ፡ አይሰጥምና ፡ እየደጋገምህ ፡ ስታነብ ፡ አርእስቱ ፡ የቱ ፡ ነው ? ስለ ፡ አርእስቱ ፡ የተናገሩት ፡ ፍሬ ፡ ነገሮች ፡ የትኞቹ ፡ ናቸው ? የደራሲውስ ፡ አሳብ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ብለህ ፡ ራስህን ፡ በራስህ ፡ መጠየቅ ፡ በጣም ፡ ያስፈልግሃል ። በዚህ ፡ መንገድ ፡ እየተመራመርህ ፡ አጣርተህ ፡ ፍሬ ፡ ፍሬ ፡ ነገሩን ፡ ቀርጸህና ፡ አርእስት ፡ ሰጥተህ ፡ አስተዋፅኦን ፡ ንደፍ ።

እንደ ፡ ገናም ፡ እያንዳንዱን ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ እየደጋገምህ ፡ መርምረህ ፡ እስከ፡ መጨረሻው ፡ ድረስ ፡ በተቻለህ ፡ መጠን ፡ ጠንቅቀህ ፡ ከተረዳህ ፡ በኋላ ፡ መዠመሪያ ፡ ያወጣኸውን ፡ አስተዋፅኦ ፡ አርም ።

ማሳጠር ፡ ማለት ፡ በጣም ፡ ጠቃሚ ፡ የሆኑትን ፡ ነገሮች ፡ ቢቀሩ ፡ ከማያጎድሉት ፡ ለመለየት ፡ ነውና ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ መጠንቀቅ ፡ ያስፈልጋል ።

ስለዚህ ፡ የጽሑፉን ፡ አሳብ ፡ ተከታትለህ ፡ ከሁሉ ፡ አስቀድመህ ፡ አርእስቱን ፡ ማግኘት ፡ ለቅድህ ፡ ዋና ፡ ጠቃሚ ፡ ነገር ፡ ይሆንልሃል ።

እንግዲህ ፡ ማናቸውንም ፡ ነገር ፡ በአእምሮህ ፡ ከቀረጽህ ፡ ረቂቅ ፡ አውጣ ። ረቂቁ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ አይጣራምና ፡ በትዕግሥት ፡ እየመላለሱ ፡ በመሥራት ፡ መለመዱን ፡ ደኅና ፡ አድርጎ ፡ መረዳት ፡ ይጠቅማል ።

አኅጽሮተ ፡ ጽሑፍ ፡ ሲሰጥህ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ የተወሰነ ፡ ቍጥር ፡ ይሰጥሃል፤ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ቅድሕ ፡ ከዋናው ፡ ጽሑፍ ፡ አንድ ፡ ሦስተኛ ፡ እንዳይበልጥ ፡ ትባላለህ ፤ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ የተሰጠህን ፡ ጽሑፍ ፡ ቃላት ፡ ቈጥረህ ፡ በሦስት ፡ ትከፍለዋለህ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የቅድሕ ፡ ቃላት ፡ ከውጤቱ ፡ እንዳይበልጡ ፡ መሞከር ፡ አለብህ ።

### ስትሠራ ፡ የሚከተሉትን ፡ በአእምሮህ ፡ ያዛቸው ።

1 የተሰጠህን ፡ ጽሑፍ ፡ አሳብ ፡ ወስደህ ፡ እንደ ፡ ራስህ ፡ ያህል ፡ አድርገህ ፡ ጻፍ።

2 ምናልባት ፡ የምታሳጥራቸው ፡ አንቀጾች ፡ ሦስት ፡ አራት ፡ ቢሆኑ ፡ ፍሬ ፡ ፍሬ ፡ ነገራቸውን ፡ ልቀምና ፡ ባንድነት ፡ ጽፈህ ፡ በቀጥታ ፡ ተነቦ ፡ ስሜት ፡ እንዲሰጥህ፡ አድርግ ።

3 ጽሑፉ ፡ በሚያጥርበት ፡ ጊዜ ፡ ያሳቡን ፡ ቅደም ፡ ተከተልነት ፡ እንደሚስማማህ ፡ ለመለወጥ ፡ ትችላለህ ።

4 ለአኅጽሮተ ፡ ጽሑፍ ፡ ዋናው ፡ ቍልፍ ፡ በብዙ ፡ ቃላት ፡ የሚገለጸውን ፡ ነገር ፡ በጥቂት ፡ ቃላት ፡ ለመግለጽ ፡ መቻል ፡ ነው ።

12*

5 አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ በእንግሊዝኛ ፡ እንደ ፡ ተማርነው ፡ አኃጽሮተ ፡ ጽሑፍ ፡ በሦስተኛ ፡ መደብ ፡ ሰው ፡ ቢጻፍ ፡ በጣም ፡ የተሻለ ፡ ነው ።

6 ሰዋስው ፡ መማር ፡ የሚጠቅመው ፡ የቃላትን ፡ አሰካክ ፡ አሳምሮ ፡ ለሰው ፡ ዋጋ ፡ ያለውን ፡ አዘጋጅቶ ፡ ማቅረቢያ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በተቻለ ፡ መጠን ፡ ቃላት ፡ በደንበኛ ፡ ሥፍራቸው ፡ እንዲውሉ ፡ ማድረግ ፡ አለብህ ።

7 ረቂቁን ፡ ደኅና ፡ አድርገህ ፡ አርምና ፡ ከተወሰነልህ ፡ ቃላት ፡ ወይም ፡ ርዝመት ፡ ሳታስበልጥ ፡ ጽዳት ፡ ጠብቀህ ፡ ጻፍ ።

ለማስረጃ ፡ የሚከተለውን ፡ ጽሑፍ ፡ አሳጥሬ ፡ አስረዳለሁ ።

## አንድ ፡ ብልኅ ፡ ዐይነ ፡ ስውር ፡

ዐይነ ፡ ስውር ፡ የነበረ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ገንዘብ ፡ አጠራቅሞ ፡ የሚያስቀምጥበት ፡ ቦታ ፡ ቸገረው ። አደራም ፡ እንዳያስቀምጥ ፡ የሚያምነው ፡ ሰው ፡ አጣ ። አንድ ፡ ቀን ፡ እኩለ ፡ ሌሊት ፡ ሲሆን ፡ ከመኝታው ፡ ተነሥቶ ፡ በሩን ፡ ከፍቶ ፡ ካትክልቱ ፡ ውስጥ ፡ ገባና ፡ ጕድጓድ ፡ ቆፍሮ ፡ ወርቁን ፡ በከረጢት ፡ ቋጥሮ ፡ ቀበረው ። ጎረቤቱ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ በር ፡ ሲከፍት ፡ ሰምቶ ፡ ቀስ ፡ ብሎ ፡ ተነሥቶ ፡ ከደጅ ፡ ወጥቶ ፡ ጨረቃ ፡ ስለ ፡ ነበረች ፡ ተመልክቶ ፡ ኖሮ ፡ ዐይነ ፡ ስውሩ ፡ ተመልሶ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሲገባ ፡ ጠብቆ ፡ የቀበረውን ፡ ወርቅ ፡ ወሰደበት ።

ጥቂት ፡ ቀን ፡ ከዋለ ፡ ካደረ ፡ በኋላ ፡ ዐይነ ፡ ስውሩ ፡ ወርቁ ፡ መኖሩንና ፡ አለመኖሩን ፡ ለማወቅ ፡ ሄዶ ፡ ከቀበረበት ፡ ቦታ ፡ ቢፈልግ ፡ አጣው ። ነገሩን ፡ ባሳቡ ፡ እየመረመረ ፡ የወሰደበትን ፡ ሰው ፡ ለማወቅ ፡ በብዙ ፡ ዐይነት ፡ መንገድ ፡ አመዛዝኖ ፡ ካየው ፡ በኋላ ፡ ይህን ፡ የሠራኝ ፡ ጎረቤቴ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ አይደለም ፡ ብሎ ፡ ጠረጠረው ። ከጎረቤቱ ፡ ዘንድ ፡ ሄደና ፡ ከዚህ ፡ ቀደም ፡ አንድ ፡ ምሥጢር ፡ አካፍልሃለሁ ፡ ብዬ ፡ ረስቼው ፡ ሳልነግርህ ፡ ቆየሁ ፤ መቼም ፡ ያላንተ ፡ ሌላ ፡ ዘመድ ፡ የለኝምና ፡ ልንገርህ ።

ጥቂት ፡ ወርቅ ፡ በእጄ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ በቀደም ፡ ዕለት ፡ የማስቀምጥበት ፡ ቦታ ፡ ቢቸግረኝ ፡ አትክልት ፡ ውስጥ ፡ ወስጄ ፡ ቀበርሁት ። አሁንም ፡ ደግሞ ፡ ከሰው ፡ ዘንድ ፡ ወርቅ ፡ አስቀምጬ ፡ ስኖር ፡ ሰውዬው ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አገር ፡ ሊሄድ ፡ ስለ ፡ ተነሣ ፡ ገንዘብህን ፡ ተረከበኝ ፡ ብሎ ፡ ዛሬ ፡ እቤቴ ፡ ድረስ ፡ አምጥቶ ፡ ሰጥቶኝ ፡ ሄደ ፤ ስለዚህ ፡ ይህን ፡ አሁን ፡ ከርሱ ፡ የተቀበልሁትን ፡ ፊት ፡ ቀብሬው ፡ ከነበረው ፡ ጋራ ፡ አንድነት ፡ አድርጌ ፡ ልቅበረው ፡ ወይስ ፡ ለብቻው ፡ አድርጌ ፡ ከሌላ ፡ ሥፍራ ፡ ልቅበረው ? እንዴት ፡ ማድረግ ፡ ይሻል ፡ ይመስልሃል ? ብሎ ፡ ጠየቀው ።

ጎረቤቱም ፡ ዝም ፡ ብሎ ፡ ሲያስብ ፡ ጥቂት ፡ ቆየና ፡ ለየብቻ ፡ ማድረግ ፡ ይሻል ፡ አይመስለኝም ፤ አንድነት ፡ ብትቀብረው ፡ የተሻለ ፡ መስሎ ፡ ይታየኛል ፡ አለው ። ይህን ፡ ተነጋግረው ፡ ዐይነ ፡ ስውሩ ፡ ከቤቱ ፡ ወጥቶ ፡ ሲሄድ ፡ ጎረቤቱ ፡ ብቻውን ፡ ሲሆን ፡ በፊት ፡ የቀበረውን ፡ ወርቅ ፡ ከቦታው ፡ ሲያጣው ፡ ይህን ፡ አሁን ፡ ሊቀብረው ፡ ያሰበውን ፡ አይቀብርም ፡ ብሎ ፡ አሰበና ፡ ሁሉንም ፡ አንድነት ፡ ለመውሰድ ፡ ሲል ፡ የሰረቀውን ፡ ወርቅ ፡ ከነከረጢቱ ፡ ወስዶ ፡ መልሶ ፡ እዚያው ፡ እነበረበት ፡ ቦታ ፡ አስቀመጠው ።

ሌሊት ፡ ሲሆን ፡ ዐይነ ፡ ስውሩ ፡ ሰው ፡ በሩን ፡ ከፍቶ ፡ ትልቅ ፡ ከረጢት ፡ ተሸክሞ ፡ ከቤቱ ፡ ወጣና ፡ አትክልቱ ፡ ውስጥ ፡ ገብቶ ፡ ቀድሞ ፡ የቀበረበትን ፡ ቦታ ፡ ቆፍሮ ፡ ከቤቱ ፡ ይዞት ፡ የመጣውን ፡ ከጕድጓድ ፡ ውስጥ ፡ ቀብሮ ፡ አፈር ፡ አለበሰና ፡ በፊት ፡ የቀበረውን ፡ ግን ፡ አውጥቶ ፡ ተሸክሞ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ገባ ። ጎረቤቱ ፡ ገና ፡ ቀኑ ፡ ሳይጨልም ፡ በጊዜው ፡ ዠምሮ ፡ አትክልቱ ፡ ውስጥ ፡ ተደብቆ ፡ ይጠብቀው ፡ ኖሮ ፡ ዐይነ ፡ ስውሩ ፡ ያደረገውን ፡ ነገር ፡ ከተመለከተ ፡ በኋላ ፡ ለኔ ፡ የነገረኝ፡ ሁለቱንም ፡ አንድነት ፡ እቀብረዋለሁ ፡ ብሎ ፡ ነበር ። አሁን ፡ ግን ፡ የፊተኛውን ፡ አውጥቶ ፡ መውሰዱ ፡ ለምንድር ፡ ነው ? እያለ ፡ ነገሩን ፡ በልቡ ፡ ሲያወጣና ፡ ሲያወርድ፡ ቆይቶ ፡ ዐይነ ፡ ስውሩ፡ እስኪገባ ፡ ድረስ ፡ አላስችልህ ፡ ብሎት ፡ በመጣደፍ ፡ ከጠበቀ ፡ በኋላ ፡ ወዲያው ፡ ገብቶ፡ በሩን ፡ እንደ ፡ ዘጋ ፡ ሄደና ፡ ወርቁ ፡ የተቀበረበትን ፡ ሥፍራ ፡ ቆፍሮ ፡ ከረጢቱን ፡ ጎትቶ፡ በችኮላ ፡ ማሠሪያውን ፡ ፈቶ ፡ እጁን ፡ አግብቶ ፡ በውስጡ ፡ ያለውን ፡ ዘግኖ ፡ አውጥቶ ፡ በጨረቃ ፡ ብርሃን ፡ ቢመለከተው ፡ ወርቅ ፡ መሆኑ ፡ ቀርቶ ፡ ጠጠር ፡ ደንጊያ ፡ ሆኖ ፡ አገኘው ። እንዲህ ፡ አድርጎ ፡ ብልኁ፡ ዐይነ ፡ ስውር፡ በብልኅነት ፡ ገንዘቡን ፡ አስመለሰ ።

ከበደ ፡ ሚካኤል ።

## ያጠረው ፡ ጽሑፍ ፡

## አንድ ፡ ብልኅ ፡ ዐይነ ፡ ስውር ፡

አንድ ፡ ዐይነ ፡ ስውር ፡ ገንዘብ ፡ አጠራቅሞ ፡ ማስቀመጫ ፡ ስላጣ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ በሌሊት ፡ ተነሣና ፡ በከረጢት ፡ አድርጎ ፡ ባትክልቱ ፡ ውስጥ ፡ቀበረው ። ይሁን፡ እንጂ ፡ ጎረቤቱ ፡ ሲቀብረው ፡ ዐይቶ ፡ ነበርና ፡ ወሰደበት ። ከዕለታት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ዐይነ ፡ ስውሩ ፡ ገንዘቡን ፡ ለማየት ፡ ቢሄድ ፡ ስላጣው ፡ ጎረቤቱን ፡ ጠረጠረውና ፡ በታማኝነት ፡ አስመስሎ ፡ «ከዚህ ፡ በፊት ፡ ባትክልቴ ፡ ውስጥ ፡ ወርቅ ፡ ቀብሬ ፡ ነበር ፡ አሁንም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ የተበደረኝን ፡ ወርቅ ፡ መለሰልኝ ፡ ስለዚህ ፡ የት ፡ ባደርገው ፡ ይሻል ፡ ይመስልሃል» ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ። ጎረቤቱም ፡ ሁሉንም ፡ ለመውሰድ ፡ ስለ ፡ ፈለገ፡ «ባንድነት ፡ ቅበረው ?» አለው ። ወዲያው፡ ዐይነ ፡ ስውሩ፡ በሌሊት ፡ መጥቶ ፡ የፊተኛውን ፡ አውጥቶ ፡ ምትኩን ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ ከረጢት ፡ ቀበረና ፡ ሄደ ፤ ጎረቤቱም ፡ ተጣባብቆ ፡ ቢያወጣው ፡ ጠጠር ፡ ሆኖ ፡ አገኘው ።

የሚከተሉትን ፡ ጽሑፎች ፡ ባንድ ፡ ሦስተኛ ፡ ያህል ፡ አሳጥራቸው ፤ አርእስትም ፡ አንተ ፡ ስጣቸው ።

## ከግርማዊነታቸው ፡ የተነገረ ፡ ቃል ፡

፩ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቸርነትና ፡ ረዳትነት ፡ የኢትዮጵያን ፡ ሕዝብ ፡ ለማስተዳደር ፡ ሥልጣን ፡ ከያዝንበት ፡ ጊዜ ፡ ዠምሮ ፡ አሳባችን ፡ ሁሉ ፡ በቤተ ፡ ክህነት፡ ማለት፡ በሃይማኖት ፡ ከሚሆነው ፡ ትምህርት ፡ በቀር ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ፡ የዘር፡ የሃይማኖት ፡ የጎሣ ፡ የወገን ፡ ልዩነት ፡ ሳይኖርበት ፡ ሁሉም ፡ በሕግ ፡ ፊት ፡ ትክክል ፡ ሆኖ፡

እየተማረ ፡ እንዲያድግና ፡ ካደገም ፡ በኋላ ፡ ይገባዋል ፡ በማለት ፡ ሳይሆን ፡ የዕውቀ ትና ፡ ያገልግሎቱ ፡ መጠን ፡ እየታየ ፡ ሁሉም ፡ የሥራውን ፡ የተገባ ፡ ዋጋ ፡ እንዲ ያገኝ ፡ አስበን ፡ የወታደርና ፡ የሌላም ፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ ጥበብ ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ ስናቆም ፡ የእስላሞችም ፡ የክርስቲያኖችም ፡ ልጆች ፡ የያባታቸውን ፡ እንደ ፡ ያዙ ፡ አገ ራቸውን ፡ የሚጠቀሙበትንና ፡ መንግሥታቸውን ፡ የሚያገለግሉበትን ፡ ራሳቸው ንም ፡ የሚረዱበትን ፡ ዕውቀት ፡ እንዲማሩ ፡ አደረግን ፡ እንጂ ፡ እንዲለያዩ ፡ አላደረግ ንም ። ሃይማኖት ፡ የግል ፡ ጉዳይ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ «ሰው ፡ የፈለገውን ፡ ሃይማኖት ፡ እንዲ ይዝ ፡ ነፃነት ፡ የሚያስፈልገው ፡ ነው» ፡ ሲሉ ፡ የአውሮጳ ፡ ሊቃውንት ፡ ተስማምተው በታል ። እኛም ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ ልናስረዳችሁ ፡ የምንፈልገው ፡ ነገር፡ አለ ። እርሱም፡ ለሰው ፡ ልጅ ፡ ሃይማኖት ፡ የግል ፡ ጉዳዩ ፡ ሲሆን ፡ ዳግም ፡ ጠቅላላውን ፡ ጉዳይ ፡ የሚጠብቅለት ፡ ሁለተኛው ፡ ሃይማኖቱ ፡ የግሉ ፡ ነፃነት ፡ ነው ። ይህም ፡ ሁለተኛው ፡ ሃይማኖት ፡ እንደ ፡ ጉዳይ ፡ ሆኖ ፡ የሚቈጠርና ፡ የተቀደሰ ፡ ጉዳይ ፡ ነው ። ነፃነት ፡ ስትጠፋ ፡ በክርስቲያኑም ፡ በእስላሙም ፡ ላይ ፡ ቀንበር ፡ ማስከተሏ ፡ የታወቀ ፡ ነው ።

ስለዚህ ፡ ክርስቲያኑም ፡ እስላሙም ፡ አማራውም ፡ ጋላውም ፡ ሌላውም ፡ ምንም ፡ በወረዳ ፡ ስም ፡ ቢለያይ ፡ ባንድ ፡ በኢትዮጵያ ፡ ሰንደቅ ፡ ዓላማ ፡ ሥር ፡ የሚኖር ፡ ያንዲት ፡ ኢትዮጵያ ፡ ቤተ ፡ ሰብ ፡ ስለ ፡ ሆነና ፡ ጉዳቱንም ፡ ጥቅሙንም ፡ የሚካ ፈል ፡ እኩል ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ይህ ፡ ያንድነትና ፡ የትክክልነት ፡ ሥራ ፡ እየጠበቀ ፡ እንዲ ሄድ ፡ ማድረግ ፡ ከዚህ ፡ በፊት ፡ ስንሠራው ፡ የነበረና ፡ ይልቁንም ፡ አሁን ፡ ባዲሱ ፡ ሥልጣኔ ፡ በበለጠ ፡ አኳኋን ፡ ልንሠራው ፡ የተዘጋጀንበት ፡ ሥራችን ፡ ነው ።

ጠላትም ፡ በግፈኛነት ፡ ሐሳቡ ፡ አገራችንን ፡ በወረረበት፡ ጊዜ ፡ እንዲጎዳውና፡ ድል ፡ እስከ ፡ መሆን ፡ እንዲያደርሰው ፡ ስላወቀ ፡ ክርስቲያንና ፡ እስላም ፡ ለሀገራቸው፡ ነፃነት ፡ ያላቸውን ፡ የጥቅም ፡ አንድነት ፡ አፍርሶ ፡ በመካከላቸው ፡ ያለውን ፡ ወደ ፡ ተቀደሰ ፡ ተግባራቸው ፡ የሚመራቸውን ፡ የተከበረ ፡ ሐሳባቸውን ፡ አጥፍቶ ፡ በመካከ ላቸው ፡ መለያየትን ፡ ለመዝራት ፡ በሚሰብከው ፡ ስበከቱ ፡ ከክርስቲያን ፡ ይልቅ ፡ እስላምን ፡ የሚያከብርና ፡ የሚደግፍ ፡ እስላምም ፡ ከክርስቲያን ፡ ይልቅ ፡ ለርሱ ፡ የሚታመንለት ፡ ያስመስል ፡ ነበር ። እንዲያውም ፡ ባለፈው ፡ ጊዜ ፡ የኢትዮጵያ ፡ መን ግሥት ፡ የእስላምን ፡ ሕዝብ ፡ በጭቆናና ፡ በሥቃይ ፡ ያኖራችሁ ፡ ነበር ፤ እኔ ፡ ግን ፡ አመጣጤ ፡ ለውነት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሙሉ ፡ ነፃነት ፡ ሰጥቻችኋለሁ ፡ እያለ ፡ ዐዋቂው ንና ፡ ተመልካቹን ፡ የእስላምን ፡ ሕዝብ ፡ በዚህ ፡ ቀላል ፡ በሆነ ፡ ስብከቱ ፡ ለመደ ለል ፡ ይጣጣር ፡ ነበር ፤ ዐዋቂው ፡ የእስላም ፡ ሕዝብ ፡ ግን ፡ ሙሐመድ ፡ እንደተና ገረው ፡ የእስላም ፡ ሕዝብ ፡ መጠጊያና ፡ መሸሸጊያ ፡ ባጣ ፡ ጊዜ ፡ በሃይማኖት ፡ ምክን ያት ፡ እስላሞች ፡ በብዙ ፡ ተቸግረው ፡ ሳለ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ ተቀብሎ፡ በመልካም፡ ማኖሩን ፡ ያውቃሉና ፡ የጠላትን ፡ ተንኮል ፡ ከመታዘብ ፡ በቀር ፡ ከወንድሞቻቸው ፡ ከክ ርስቲያኖች ፡ ጋራ ፡ ያላቸው ፡ ከብዙ ፡ ዘመን ፡ ዠምሮ ፡ የሚኖረው ፡ በጋራ ፡ ጥቅም ፡ ላይ ፡ የተመሠረተው ፡ ያንድነትና ፡ የፍቅር ፡ ማሰሪያ ፡ እየጠበቀ ፡ እንዲሄድ ፡ ከማድ ረግ ፡ አላቋረጡም ።

፪ ፡ ትዕግሥት ፡ ከጥበብ ፡ ይበልጣል ። ትዕግሥቴ ፡ ዋጋ ፡ በቅሌ ፡ አንድ ፡ ቁና ፡ ትዕግሥት ፡ ቢገመት ፡ ካንድ ፡ ዳውላ ፡ ጥበብ ፡ ይበልጣል ። ሰው ፡ ሁሉ ፡ ትዕግሥትን ፡ ይወዳል ፤ መታገሥ ፡ ግን ፡ ያስቸግራል ። ትዕግሥት ፡ ለደዌ ፡ ሁሉ ፡ የሚጠቅም ፡ መድኀኒት ፡ ነው ። ማናቸዋም ፡ ባልቴት ፡ ጥቅምን ፡ ዐውቃ ፡ ልትናገር ፡ ትችላለች ። ዳሩ ፡ ግን ፡ ትዕግሥት ፡ መቼም ፡ ባትክልት ፡ ሁሉ ፡ አይገኝም ። ፈረስ ፡ ዝንቦች ፡ ሲያፍነዘንዙት ፡ ራሱን ፡ እንደሚነቀንቅ ፡ መዘውር ፡ ሲላላ ፡ እንደሚንቃቃ ፡ እንዲሁም ፡ በሥጋችንና ፡ ባጥንታችን ፡ ያደረብን ፡ በሽታና ፡ ደዌ ፡ ቢዘበዝበን ፡ በሥቃይ ፡ እየዋለልንና ፡ እየተንሰፈሰፍን ፡ እንጉነፈነፋለን ። መጽሐፍ፡ ከተማረው፡ መከራ፡ የመከረው ፤ በመከራ ፡ ትዕግሥትን ፡ እንማርበታለንና ።

ማጉረምረም ፡ መቼም ፡ ከጥፉ ፡ ጠማማ፡ ዐመላችን ፡ የሚወጣ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ፡ የተስማማ ፡ ነው ። ዳሩ ፡ ግን ፡ ክርስቲያን ፡ ብንሆን ፡ ክፉ ፡ ዐመላችንን ፡ ልንገራና ፡ ልናሸንፍ ፡ እንጂ ፤ ትዕግሥት ፡ ጠቦን ፡ በማንም ፡ ነገር ፡ ልንግማማ ፡ አይገባም ። ሾተልህን ፡ ወደ ፡ አፎት ፡ ቊጣህን ፡ ወደ ፡ ትዕግሥት ፡ ይባላል ። ክፉ ፡ ዐመላችን ፡ ቢገዝመን ፡ ቀምጣሎችና ፡ ሞሽላቆች ፡ ሁነን ፡ በሚደርስብን ፡ ባንታገሥ ፡ በጥቂት ፡ ምክንያት ፡ ከባልንጀራችን ፡ ጋራ ፡ ብንጉነፈነፍና ፡ ብንገፋገፍ ፡ አምላክ ፡ በሰጠን ፡ ሥራ፡ ባንጠነክር ፡ የክርስትና ፡ ሃይማኖታችን ፡ ለምን ፡ ይጠቅመናል ? ያልተቀጣ ፡ ልጅ ፡ ያልታጠበ ፡ እጅ ፡ ኀይልንና ፡ ብቃትን ፡ የምናገኝበት ፡ በሃይማኖት ፡ አይደለምን?ገና፡ የጌታችንን ፡ ትምህርት ፡ ያጎረቡና ፡ የሚያሽጎበቡ ፡ ልጆች ፡ መሆናችን ፡ ነው ።

አሊ ፡ ኢርክሰን ፡

፫ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ አንድ ፡ ዓሣ ፡ አጥማጅ ፡ ሰው ፡ መረቡን ፡ ይዞ ፡ በጀልባ፡ ላይ፡ ተቀምጦ ፡ ከባሕር ፡ ዳር ፡ ሆኖ ፡ ዓሣን ፡ ሲያጠምድ ፡ ከባሕሩ ፡ ሥር ፡ አንዲት ፡ ዛጎል ፡ ስታብለጨልጭ ፡ አይቶ ፡ ዋጋዋ ፡ የከበረ ፡ አልማዝ ፡ ስለ ፡ መሰለችው ፡ እንደ ፡ ወፍ ፡ በራ ፡ የምታመልጠው ፡ መስሎት ፡ ይሆን ? ወይም ፡ ደግሞ ፡ አልማዝ ፡ ካገኘሁ ፡ የቀረው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ምን ፡ ያደርግልኛል ፡ ብሎ ፡ በማሰብ ፡ ይሆን ? ወይስ ፡ ከደስታ ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ነገር ፡ ዓለሙን ፡ ረስቶት ፡ ይሆን ? በምን ፡ ምክንያት ፡ እንደሆን ፡ እንጃ ፡ ከባሕሩ ፡ ውስጥ ፡ ይጎትተው ፡ የነበረውን ፡ ዓሣ ፡ የመላበትን ፡ መረቡን ፡ ከባሕሩ ፡ ውስጥ ፡ ወርውሮ ፡ ገሥግሦ ፡ ሄዶ ፡ ቢያነሣት ፡ ያች ፡ የምታብለጨልጨው ፡ ነገር ፡ ቅርፊቷ ፡ የሚያምር ፡ ውስጧ ፡ ግን ፡ ባዶ ፡ የሆነ ፡ ዛጎል ፡ ነበረች ፡ እንጂ ፡ አልማዝ ፡ አልነበረችም ። እንዲህ ፡ አድርጎ ፡ ምስኪኑ ፡ ሰውዬ ፡ የዕለት ፡ እንጀራውን ፡ የሚያገኝበትን ፡ መረቡን ፡ አጥቶ ፡ አልማዝ ፡ በመሰለችው ፡ ነገር ፡ ተሳቆ ፡ ከሁለቱም ፡ ሳይሆን ፡ እያዘነ ፡ ባዶ፡ እጁን ፡ ተመልሶ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ገባ።

በዚያ ፡ ዕለት ፡ ቀኑን ፡ ሙሉ ፡ ምኞትና ፡ ተስፋ ፡ የሰውን ፡ ልብ ፡ እያታለሉ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ እንደሚቀልዱበትና ፡ እንደሚጫወቱበት ፡ እያሰበ ፡ ሲተክዝ ፡ ዋለ ። ደስታም ፡ ሆነ ፡ ኀዘንም ፡ ሆነ ፡ ማለፉ ፡ አይቀርምና ፡ በማግሥቱ ፡ ሌላ ፡ መረብ ፡ ፈልጎ ፡ ዓሣ፡ ሊያጠምድ ፡ ወደ፡ባሕር፡ ዳር፡ ሄደ። ጸጸቱን ፡ እንዳይቀሰቀስበት፡ ቀድሞ፡ ያጠምድበት፡ የነበረውን፡ መረቡን፡ የወረወረበትን፡ ቦታ፡ ትቶ፡ ወደ፡ ሌላ፡ ስፍራ፡ ሄዶ፡ መረቡን፡

ወደ ፡ ባሕር ፡ ጥሎ ፡ ይጠባበቅ ፡ ገመር ። ወደ፡ ባሕር፡ ውስጥ ፡ ጎንበስ ፡ ብሎ ፡ ቢመለከት ፡ ከውኃው ፡ ሥር፡ እንደ ፡ ጨለማ ፡ ኮከብ፡ ሆና ፡ የምታብረቀርቅ ፡ አንዲት ፡ ነገር፡ አየ ። ትናንትና ፡ የተሞኘሁት ፡ ይበቃኛል ፡ ዛሬስ ፡ አልታለልም ፡ ብሎ ፡ መረቡን፡ ጎተተና ፡ የተያዙለትን ፡ ጥቂት ፡ ዓሣች ፡ ይዞ ፡ ያችን ፡ የምታበራ ፡ ነገር ፡ ትቶ፡ ወደ፡ ቤቱ፡ ሄደ ። እንዲሁ ፡ እንደ ፡ ርሱ፡ ዓሣ ፡ ሊያጠምድ፡ ሄዶ ፡ የነበር ፡ ጓደኛው ፡ ያችን፡ የምታብረቀርቀውን ፡ ነገር ፡ አይቶ ፡ ቢያነሣት ፡ ዋጋዋ ፡ የከበረ ፡ የምታምር ፡ አልማዝ ፡ ሆና፡ አገኛትና ፡ አለመጠን ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ ከኋላው ፡ እየሮጠ ፡ መጥቶ ፡ ደረሰበትና ፡ ደስታውን ፡ አካፈለው ። የመጀመሪያውም ፡ ሰው ፡ ይህችን ፡ አልማዝ ፡ በፊት ፡ ያየኋት ፡ እኔ፡ ነበርሁ ፡ ግን፡ ትናንትና ፡ እንደዚሁ ፡ የምታብለጨልጭ ፡ ነገር ፡ አይቼ ፡ ባነሣት፡ዛጎል፡ ሆና፡ አገኘኋት። አልማዝ፡ መስላኝ ፡ መረቤን፡ ከነዓሣው ፡ ወርውሬው፡ ስለ፡ ነበረ፡ ነው፡ ሄጄ ፡ ያላነሣኋት ። በዚህ ፡ ተጸጽቼ ፡ ሳለሁ ፡ ዛሬ፡ ደግሞ ፡ ይህችን ፡ ባይ፡ እንደ ፡ ትናንትናው ፡ የምሳቀቅ፡ መስሎኝ፡ አልፊያት ፡ መጣሁ ። አሁንም፡ ቢሆን ፡ ለምን ሳላነሣት፡ ቀረሁ ፡ ብዬ፡ አይቆጨኝም ። ትናንትና ፡ ለርሷ ፡ ብዬ ፡ ገንዘቤን ፡ አጥቻለሁና ፡ ምናልባት ፡ ዛሬ ፡ ደግሞ ፡ በሕይወቴ ፡ ሳትቀጣኝ ፡ አትቀርም ፡ ነበር ፤ ስለ ፡ ምን ፡ እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ዕድል ፡ ለኔ ፡ አላለውምና ፡ ብሎ ፡ ለጓደኛው ፡ አጫወተው ።

ሰው ፡ ዕድሉ ፡ ያልሰጠውን ፡ ነገር ፡ አመለጠኝ ፡ ብሎ ፡ መጸጸቱን ፡ ትቶ ፡ ትንሽም ፡ ቢሆን ፡ በዚያው ፡ በተሰጠው ፡ ዕድል ፡ ደስ ፡ እያለውና ፡ ፈጣሪውን ፡ እየመሰገነ ፡ መኖር ፡ ይገባዋል ።

ከበደ ፡ ሚካኤል ፡

## ከፊል ፡ ቃላት ፡

ማሰሪያ ፡አንቀጽ፡=ማ. አ.
ተውሳከ ፡ ግስ ፡=ተ. ግ.
መስተዋድድ ፡=መዋ.
ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡=ጥ.ሐ.
መደበኛ፡ ሐረግ ፡=መ.ሐ.
ንኡስ ፡ ሐረግ ፡=ን.ሐ.
አረፍተ፡ ነገር ፡ =አ. ነ.
የሐረግ፡ዐይነቶች፡=የሐ. ዐ.
የባለቤት፡ገላጭ ፡=የባ. ገ.

## አገባብና ፡ ሙያ ፡

በሰዋስው ፡ ውስጥ ፡ ሙያና ፡ አገባብ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ይወራረሳሉ ፤ በስምና ፡ በተውላጠ ፡ ስም ፡ ብቻ ፡ ይለያያሉ ። ስምና ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ አገባብ ፡ የላቸውም ፤ ለቀሩት ፡ ግን ፡ አላቸው ። ስለዚህ ፡ የመስተዋድድ ፡ ሙያ ፡ ወይም ፡ የመስተዋድድ ፡ አገባብ ፡ ቢል ፡ ትርጕሙ ፡ አንድ ፡ ነው ።

## የቃላት ፡ ዐይነትና ፡ አገባብ ፡

የቃላት ፡ ዐይነት ፡ ስንል ፡ ወገናቸውንና፡ ክፍላቸውን ፡ እንደዚሁም ፡ ከሌሎቹ፡ የሚለዩበትን ፡ ማመልከታችን ፡ ነው ። የቃላት ፡ አገባብ፡ ወይም ፡ ሙያ ፡ ስንል ፡ ግን፡ በአረፍተ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ገቡ ፡ ሥራቸውን ፡ ማመልከታችን ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ ጉዳይ ፡ አጥብቆ ፡ ማሰብ ፡ ይገባል ።

## ልዩ፡ልዩ፡ ያማርኛ ፡ ፈተኖች፡

### ፩ኛ ፡ ያማርኛ ፡ ፈተና ፡

1 የስም ፡ ዐይነቶችን ፡ ጻፍና ፡ ለያንዳንዳቸው ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ ቃላት ፡ ምሳሌ፡ ስጥ ።

2 ከዚህ ፡ በታች ፡ የተጻፉት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ መጠይቅ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ስለጎደላቸው ፡ በተስማሚ ፡ መጠይቃን ፡ ተውላጠ ፡ ስሞች ፡ ሙላቸው ።

(ሀ)----መታህና ፡ ታለቅሳለህ ?

(ለ)---ወደ ፡ ድሬ ፡ ዳዋ ፡ ተላከ ?

(ሐ)---ሰጠህ ?

(መ) ወደ ፡ ድሬ ፡ ዳዋ ፡ ----ተላኩ ?

(ሠ) የከዱት ፡ ልጆች ፡ -----ናቸው ?

(ረ) ቀለም ፡ የሚገኘው ፡ ----ነው ?

3 የሚከተሉትን ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ በተገብሮ ፡ የተነገሩትን ፡ ወደ ፡ ገቢር ፡ በገቢር ፡ የተነገሩትን ፡ ወደ ፡ ተገብሮ ፡ አዙሩቸው ።

(ሀ) ግቢው ፡ ባሰፋ ፡ ብርታት ፡ ጸዳ ።

(ለ) በቀለ ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ የሳይንስ ፡ መጽሐፍን ፡ ተረጐመ ።

(ሐ) እንግዳ ፡ ወርቅ ፡ ቤትን ፡ ሠራ ።

(መ) መጥረቢያው ፡ ባሰፋ ፡ እጅ ፡ ተሰበረ ።

4 (ሀ) ዐምድ ፡ የሚባለውን ፡ ቃል ፡ ግለጸው ።

(ለ) መሰከረ ፡ የሚባለውን ፡ ግስ ፡ በአዕማድ ፡ ደንብ ፡ አርባው ።

ከዚህ ፡ በታች ፡ ከተነገሩት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ ድኩማንና ፡ ጽኑዓን ፡ የሆኑትን ፡ ዐምዶች ፡ እየመረጥህ ፡ ጻፍ ።

(ሐ) ፈለቀ ፡ ወንድሙን ፡ መረቀው ።

(መ) መኩሪያ ፡ ምንም ፡ ቢሠራ ፡ አይደክምም ።

(ሠ) ቀለሙ ፡ ከፎቅ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ ወደቀ ።

(ረ) አበበ ፡ ታላላቆቹን ፡ ያከብራል ።

5 የሚከተሉትን ፡ ቃላት ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ በመሥራት ፡ ብቻ ፡ ግለጻቸው ። በያንዳንዳቸው ፡ አንዳንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራ ፡ ማለት ፡ ነው ።

(ሀ) ውለተኛ ፡ (ለ) ምክንያተኛ ፡ (ሐ) ምኞት ፡ (መ) ጸጸት ።

6 መረጠ ፡ በሚባለው ፡ ግስ ፡ በዝርዝር ፡ ርባታ ፡ ደንብ ፡ እኔ ፡ የሚለው ፡ መራጭ ፡ አንተ ፡ የሚለው ፡ ግን ፡ ተመራጭ ፡ እንደሚሆኑ ፡ አድርገህ ፡ በሚከተሉት ፡ ስልቶች ፡ በሁሉም ፡ ጊዜያት ፡ አርባው ።

(ሀ) በዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡ (ለ) በትእዛዝ ፡ አንቀጽ ፡ (ሐ) ባዋዋይ ፡ አንቀጽ ፡

(መ) በንኡስ ፡ አንቀጽ ።

7 አለ ፡ አራት ፡ ባህሎች ፡ እንዳሉት ፡ ከዚህ ፡ በፊት ፡ ተምረናል ። ስለዚህ ፡ ባራቱም ፡ ባህሎች ፡ አንዳንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሠርተህ ፡ አሳይ ፤ ነበርና ፡ ዠመር ፡ የግስ ፡ ረዳት ፡ እንደሚሆኑ ፡ አድርገህ ፡ አንዳንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራ ።

8 የሚከተሉትን ፡ ቃላት ፡ ግለጻቸው ።

(ሀ) ሰያፍ ፡ ግስ ፡ (ለ) የማያቋርጥ ፡ ግስ ፡ (ሐ) ተውሳከ ፡ ግስ ፡

ከዚህ ፡ በታች ፡ በሚገኙት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ ተውሳካተ ፡ ግሶችን ፡ እየለቀምህ ፡ ጻፍና ፡ ክፍላቸውን ፡ አመልክት ።

(ሀ) ዐመለ ፡ ወርቅ ፡ ቤተ ፡ ሰቦቹን ፡ ለመጠየቅ ፡ ትናንትና ፡ ሄደ ።
(ለ) ቢቻልህ ፡ በዚያው ፡ ትጠይቃቸዋለህ ።
(ሐ) ጠላቶቼን ፡ እነስንፍናን ፡ ዘወትር ፡ እዋጋቸዋለሁ ።
(መ) ወንድሙ ፡ ዘወትር ፡ የመጻሕፍት ፡ ቤቱን ፡ ያጸዳል ።
(ሠ) በቀለ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ በትጋት ፡ ይሠራል ።
(ረ) ደበበው ፡ በዝግታ ፡ ይናገራል ።
(ሰ) አንተ ፡ ልጅ ፡ እንግዲህ ፡ አትዘንጋኝ ።
(ሸ) መቼ ፡ አየኸው ?
(ቀ) መዠመሪያ ፡ አንብና ፡ ኋላ ፡ ትነግረኛለህ ።
(በ) እንደዩ ፡ ብትስት ፡ ሁለተኛ ፡ መሳት ፡ አይገባህም ።
(ተ) እሺ ፡ እጽፍልሃለሁ ።

## ፪ኛ ፡ ያማርኛ ፡ ፈተና ፡

(ሀ) በተውላጠ ፡ ስምና ፡ በስም ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ ልዩነት ፡ አስረዳ ።

1 ከዚህ ፡ በታች ፡ በተጻፉት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ ያሉትን ፡ ስሞች ፡ እየለቀምህ ፡ ከጻፍህ ፡ በኋላ ፡ የየስም ፡ ዐይነታቸውን ፡ አመልክት ።

(ለ) አየለ ፡ ደብዳቤን ፡ ለዘለቀ ፡ ጻፈለት ።

(ሐ) ጠንክሮ ፡ የማይሠራ ፡ ተማሪ ፡ ዝቅተኛ ፡ ቍጥርን ፡ (ማርክን) ፡ ባገኘ ፡ ጊዜ ፡ ይበሳጫል ።

(መ) ሰው ፡ የሚከብረው ፡ ባመሉ ፡ ነው ።

(ሠ) ትዕግሥትና ፡ ዕውቀት ፡ ደግሞም ፡ መጻሕፍትን ፡ መመርመር ፡ የዕውቀት ፡ ቍልፎች ፡ ናቸው ።

2 ከዚህ ፡ በታች ፡ የተጻፉትን ፡ ቃላት ፡ በየቦታቸው ፡ አመልክት ።

ወይፈን ፡ ላም ፡ ጥጃ ፡ አውራ ፡ ብርጭቆ ፡ ፈረስ ፡ አጋዘን ፡ ጊደር ፡ በሬ ፡ ሰው ፡ ባዝራ ፡ ሲካካ ፡ መጽሐፍ ፡ ኮርማ ፡ ዶሮ ፡ ዝንጀሮ ፡

3 ከዚህ ፡ በላይ ፡ በ፪ኛው ፡ ጥያቄ ፡ ውስጥ ፡ የተጻፉትን ፡ ስሞች ፡ በነጠላ ፡ የተጻፉትን ፡ ወደ ፡ ብዙ ፡ በብዙ ፡ የተጻፉትን ፡ ወደ ፡ ነጠላ ፡ አዙራቸው ።

4 (ሀ) ድርብ ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ያለበት ፡ አንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራ ።

(ለ) መዘክር ፡ ተውላጠ ፡ ስም ፡ ያለበት ፡ አንድ ፡ አ. ነ. ሥራ ።

(ሐ) በሦስቱ ፡ መደቦች ፡ ያሉትን ፡ ተውላጠ ፡ ስሞች ፡ ጻፋቸው ።

(መ) ተውላጠ ፡ ስም ፡ የመስተዋድድ ፡ ተገዥ ፡ እንደሚሆን ፡ አድርገህ ፡ አንድ ፡ አ. ነ. ሥራ ።

(ሠ) ተውላጠ ፡ ስም ፡ ተጠቃሽ ፡ ተሳቢ ፡ እንደሚሆን ፡ አድርገህ ፡ አንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራ ።

5 (ሀ) በዘርፍና ፡ በዘርፍ ፡ አስተኔ ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ ልዩነት ፡ አስረዳ ።

(ለ) ተከታይ ፡ ቅጽል ፡ ያለበት ፡ አንድ ፡ አ. ነ. ሥራ ።

(ሐ) በቂ ፡ ቅጽል ፡ ያለበት ፡ አንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራ ።

(መ) በተወሰነ ፡ አኀዝና ፡ ባልተወሰነ ፡ አኀዝ ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ ልዩነት ፡ ግለጽ ።

(ሠ) ባመልካች ፡ ተውላጠ ፡ ስምና ፡ ባመልካች ፡ ቅጽል ፡ ያለውን ፡ ልዩነት ፡ ግለጽ ።

6 ከዚህ ፡ በታች ፡ የተጻፉትን ፡ አ. ነገሮች ፡ በገቢር ፡ የተጻፉትን ፡ ወደ ፡ ተገብሮ ፡ በተገብሮም ፡ የተጻፉትን ፡ ወደ ፡ ገቢር ፡ አዙራቸው ።

(ሀ) አቶ ፡ አየለ ፡ ቤትን ፡ ሠራ ።

(ለ) አንድ ፡ ሌባ ፡ በፖሊሶች ፡ እጅ ፡ ተያዘ ።

(ሐ) አየለ ፡ አንድ ፡ የሳይንስ ፡ መጽሐፍን ፡ ደረሰ ።

(መ) አንድ ፡ የሰዋሰው ፡ መጽሐፍ ፡ ከአበበ ፡ ተጻፈ ።

7 ከዚህ ፡ በታች ፡ ከተጻፉት ፡ አ. ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ ግሶችን ፡ (ማሰሪያ ፡ አንቀጾች) ፡ እየለቀምህ ፡ ከጻፍህ ፡ በኋላ ፡ ስልታቸውንና ፡ ጊዜያቸውን ፡ አመልክት ።

(ሀ) ደምሴ ፡ በስሕተቱ ፡ አዘነ ።

(ለ) ወርቁ ፡ በፈተና ፡ አንደኛ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ተደስቷል ።

(ሐ) ፈለቀ ፡ ወደ ፡ ወንድሙ ፡ ዘንድ ፡ ሄዶ ፡ ነበር ።

(መ) እየለ ፡ ንግግርን ፡ ያሳምራል ።
(ሠ) እየለ ፡ ወደዚህ ፡ አገር ፡ ሊመጣ ፡ ነው ።
(ረ) የተሰጠህን ፡ ትምህርት ፡ አጥንተህ ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ ባልተናደድህ ፡ ነበር ።
ከዚህ ፡ በታች ፡ ከተጻፉት ፡ አርእስት ፡ ስለ ፡ አንደኛው ፡ ብቻ ፡ ጻፍ ።
(ሀ) ስለ ፡ ተወለድህበት ፡ አውራጃ ፡
(ለ) ስለምትኖርበት ፡ ከተማ ፡

ድርሰትህ ፡ ጽዳት ፡ እንዲኖረውና ፡ አሳብህ ፡ በአንቀጽ ፡ (ፓራግራፍ) ፡ የተከፋፈለ ፡ መሆን ፡ አለበት ።

## ፷ኛ ፡ ያማርኛ ፡ ፈተና ፡

1 ከዚህ ፡ በታች ፡ ከተጻፉት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች፡ ውስጥ ፡ የሚገኙትን ፡ ቅጽሎች፡ እየለየህ ፡ አመልክት ።

(ሀ) ልጁ ፡ ሰነፍ ፡ ብጤ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የበቃ ፡ ዕውቀትን ፡ አያገኝም ።
(ለ) ቀይ ፡ ፈረስ ፡ ላይን ፡ ያስደስታል ።
(ሐ) ሃያ ፡ ዘጠኝ ፡ ልጆች ፡ ለሁለተኛ ፡ ደረጃ ፡ ታጭተዋል ።
(መ) አያሌ ፡ ተማሪዎች ፡ በሚመጣው ፡ ዓመት ፡ ይመረቃሉ ።
(ሠ) እነዚህ ፡ ወጣቶች ፡ በችግኝ ፡ ይመስላሉ ።

2 የሚከተለውን ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ በሚከተሉት ፡ ሙያዎች ፡ ዘርዝረው ።
ደመቀ ፡ ላጎቱ ፡ ልጅ ፡ አንድ ፡ የኪስ ፡ ብርዕን ፡ ሸለመው ።
(ሀ) ባለቤት ፡ (ለ) አንቀጽ (ሐ) ዘርፍ ፡ (መ) ፡ የመስተዋድድ ፡ ተገዥ ፡
(ሠ) ቀጥተኛ ፡ ተሳቢ (ረ) ቅጽል ፡

3 ከዚህ ፡ በታች ፡ ከተጻፉት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ መስተፃምሮችን ፡ እየለየህ ፡ አመልክት ።

(ሀ) እኔም ፡ እሱም ፡ ለሠርግ ፡ ታድመናል ።
(ለ) ዛሬ ፡ ወይም ፡ ነገ ፡ ሰልፍ ፡ እንማራለን ።
(ሐ) ኮት ፡ ወይም ፡ ሱሪ ፡ አሰፋልሃለሁ ።
(መ) ሆዴን ፡ አሞኛል ፤ ሆኖም ፡ ለቢስ ፡ አይሰጠኝም ።
(ሠ) አብረኸን ፡ እንድትሄድ ፡ ፈቅደንልሃል ፤ እንግዲያውስ ፡ ልታጠቅ ።

4 ከዚህ ፡ በታች ፡ የተጻፉትን ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ጉድለት ፡ በትእምርተ ፡ አንክሮ ፡ ሙላ ።

(ሀ) ይኸውልሃ ፡ ትቶን ፡ ሄደ ፡ ል ።
(ለ) አዬ ፡ ጉድ ፡ አዬ ፡ ጉድ ፡ ምነዋ ፡ በል ።

5 መደበኛና ፡ ጥገኛ ፡ ያለበት ፡ አንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራና ፡ መደበኛውንና ፡ ጥገኛውን ፡ እየለየህ ፡ ለየብቻው ፡ አመልክት ።

6 የሚከተሉትን ፡ ግለጻቸው ።

(ሀ) ድጋፍ ፡ ፈላጊ ፡ ቅጽል ።

(ለ) የግብር ፡ ቅጽል ፡

(ሐ) የተወሰነ ፡ አኃዝ ፡

(መ) ያልተወሰነ ፡ አኃዝ ፡

(ሠ) መስተፃምር ፡

7 ሰዋስው ፡ ለምን ፡ እንደሚጠቅም ፡ ከስምንት ፡ መሥመር ፡ በማይበልጥ ፡ አሳብህን ፡ ግለጥ ።

## ፩ኛ ፡ ያማርኛ ፡ ፈተና ።

1 (ሀ) ሁለት ፡ ድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮችን ፡ ሥራና ፡ መደበኞቹንና ፡ ጥገኞቹን ፡ ሐረጎች ፡ እየለየህ ፡ አመልክት ።

(ለ) በሚከተሉት ፡ የንኡስ ፡ ሐረግ ፡ ክፍሎች ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ ምሳሌ ፡ ስጥ ።

1 በአርእስታዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡

2 በመስተዋድዳዊ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡

3 በቦዝ ፡ ንኡስ ፡ ሐረግ ፡

(ሐ) ንኡስ ፡ ሐረግ ፡ በሚከተሉት ፡ ሙያዎች ፡ እንዴት ፡ እንደሚገባ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሠርተህ ፡ በግርጌው ፡ ነጠላ ፡ መሥመር ፡ አሥምረህ ፡ አሳይ ።

1 ተውሳከ ፡ ግስ ፡ 2 ስም ፡ እንደ ፡ ተሳቢ ፡

2 (ሀ) በነጠላ ፡ አረፍተ ፡ ነገርና ፡ በድብልቅ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ ልዩነት ፡ ግለጽ ።

(ለ) የሚከተሉትን ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ጉድለት ፡ በተስማሚ ፡ ቃላት ፡ ሙላ።

1 ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ በተቀጣይ ፡ ደንብ ፡ ስምን ፡---በገባ ፡ ጊዜ ፡ ---ተብሎ ፡ ይጠራል ።

2 በባለቤት ፡ ወይም ፡ በተሳቢ ፡ ላይ ፡ የሚደረብ ፡ ቃል ፡ ---------- ወይም ፡ -------------------------------------------------------ይባላል ።

3 ድርብ ፡ አረፍተ ፡ ነገርን ፡ ለመሥራት ፡ ------------------------------------ አስፈላጊ ፡ ናቸው ።

4 የአረፍተ ፡ ነገር ፡ ዐይነቶች ፡ -----------------------------------ና----- ናቸው ።

5 ባለቤትን ፡ ወይም ፡ ተሳቢን ፡ ለመግለጽ ፡ የሚጨመሩት ፡ ቃላት ፡ ---------------------፡---------------------ና----------------------------ናቸው ።

(ሐ) ጥገኛ ፡ ሐረግ ፡ ቅጽል ፡ እንደሚሆን ፡ አድርገህ ፡ አንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራ ።

3 (ሀ) የሚከተሉትን ፡ ቃላት ፡ ልዩነት ፡ አስረዳ ።

1 የአንቀጽ ፡ ተሳቢ ፡ 2 የአንቀጽ ፡ ተጨማሪ ፡

(ለ) በአጋናኝና ፡ በፍላጎት ፡ አንዳንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራ ።

(ሐ) የሚከተሉትን፡ አረፍተ፡ ነገሮች፡ በሚከተሉት ፡ ሙያዎች፡ ተንትናቸው።

1 ታላቁ ፡ ነጋዴ ፡ አቶ ፡ ማንደፍሮት ፡ በስንት ፡ ትግል ፡ ያስመጡትን ፡ ቦንዳ ፡ ላቶ ፡ በፈቃዱ ፡ በርካሽ ፡ ዋጋ ፡ ሸጡላቸው ።

2 አቶ ፡ አየለ ፡ አናጢው ፡ የሠራቸው ፡ ቁም ፡ ሣጥኖችና ፡ ወንበሮች ፡ በጣም ፡ ያማሩና ፡ የተዋቡ ፡ ስለ ፡ ነበሩ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ለመግዛት ፡ በዋጋ ፡ ተሜረቱባቸው ።

1 ባለቤት ፡ 3 ማሰሪያ፡ አንቀጽ ፡ 5 የቃል ፡ መግለጫ ፡ ተጨማሪ ፡
2 ተቀባይ ፡ 4 ተሳቢ ፡ 6 የአንቀጽ ፡ ተጨማሪ ፡

4 ከሚከተሉት ፡ አርእስት ፡ ስላንደኛው ፡ ብቻ ፡ ጻፍ ። <u>ድርሰት</u> ፡

(ሀ) ስለ ፡ ሳይንስ ፡ ጥቅም ፡

(ለ) የእንግሊዝኛ ፡ ቋንቋ ፡ ባገራችን ፡ የተስፋፋበት ፡ ምክንያት ፡

(ሐ) ሰው ፡ እንዴት ፡ አድርጎ ፡ ጤንነቱን ፡ እንደሚጠብቅ ፡

5 መረመረ ፡ የሚለውን ፡ ግስ ፡ በአዕማድ ፡ ክፍል ፡ ባስደራጊ ፡ እነርሱ፡ የሚለው ፡ አድራጊ ፡ እኛ ፡ የሚለው ፡ ተሳቢ ፡ እንደሚሆን ፡ አድርገህ ፡ ባራቱም ፡ የግስ ፡ ስልቶች ፡ አርባው ።

## ፫ኛ ፡ ያማርኛ ፡ ፈተና ፡

1 ለሚከተሉት ፡ ቃላት ፡ ተመሳሳያቸውንና ፡ ተቃራኒያቸውን ፡ ስጥ ።

ጭምት ፡
ለማ ፡
ብርቱ ፡
ፈዛዛ ፡
ዐመለ ፡ ወርቅ ፡
ቸር ፡
ጌታ ፡
ኮሰሰ ፡

ደራ ፡
ቡሩክ ፡
ቀልበቢስ ፡
በድን ፡
አረኸ ፡
ዐዋቂ ፡
ጠራ ፡
ግድየለሽ ፡

ሥራ ፡ ፈት ፡ መተረ፡
ቆዘመ ፡ ደርባባ ፡

2 ቅጽል ፡ የማነጻጸርን ፡ ደረጃ ፡ እንደሚገልጽ ፡ አድርገህ ፡ በግብርና፡ በዐይነት፡ ቅጽሎች ፡ አንዳንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገርን ፡ ሥራ ።

3 ተውሳከ ፡ ግስ ፡ ምን ፡ ምኖችን ፡ ይገልጻል ? እያንዳንዳቸውን ፡ የሚገልጽ ፡ አንዳንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራ ፡

4 የተውሳከ ፡ ግስ ፡ ንኡሳን ፡ ክፍሎች ፡ስንት ፡ ናቸው ? ከነርሱም ፡ ውስጥ ፡ በሦስቱ ፡ አንዳንድ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራ ።

5 አንቱ ፡ የሚባለው ፡ የአክብሮት ፡ ቃል ፡ መሠረቱ ፡ ከየት ፡ ነው ?

6 በሰዋስው ፡ ደንብ ፡ ተስማሚውን ፡ መወሰን ፡ ማለት ፡ ምንድር ፡ ነው ? ተሳሳቢውን ፡ መወሰን ፡ ማለትስ ? የኋለኛውን ፡ ካስረዳህ ፡ በኋላ ፡ አንድ ፡ አረ ፍተ ፡ ነገር ፡ ሥራና ፡ የተሳሳቢውን ፡ ስምምነት ፡ ግለጽ ።

7 ጥገኛ ፡ መስተፃምርና ፡ መስተዋድድ ፡ የሚሆኑ ፡ አሉ ፤ በሁለት ፡ ፊት ፡ ገብ ተው ፡ የሚያገለግሉት ፡ እንዴት ፡ ነው ?

8 ባኋኋንና ፡ በምክንያት ፡ መስተዋድዶች ፡ ሁለት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮችን ፡ ሥራ ።

9 የሚከተሉትን ፡ ተረቶች ፡ ግለጽ ።

(ሀ) ካብሮ ፡ አደግህ ፡ አትሰደድ ።

(ለ) ጨኸቴን ፡ ቀሙኝ ።

(ሐ) ተማሪና ፡ ዶሮ ፡ በሞቱ ፡ ጊዜ ፡ ክቡር ፡ ነው ፤ በቁመናውማ ፡ እራቱ ፡ ጥሬ ፡ ነው ።

(መ) ሕመሙን ፡ የሸሸገ ፡ መድኀኒት ፡ የለውም ።

(ሠ) ያልጠረጠረ ፡ ተመነጠረ ።

## ፯ኛ ፡ ያማርኛ ፡ ፈተና ፡

1 በአንቀጻዊ ፡ ስምና ፡ በአንቀጻዊ ፡ መግለጫ ፡ መካከል ፡ ምን ፡ ልዩነት ፡ አለ ?

2 የግስ ፡ ቍጥር ፡ በባለቤት ፡ የሚወሰንበትን ፡ ምክንያት ፡ ግለጽ ።

3 ሕገኛ፡ ግስ፡ የምንለው፡ እንዴት፡ ያለውን፡ ነው ? ለምሳሌ፡ ሦስት፡ ግሶች፡ጻፍ።

4 ስለ ፡ አርእስትና ፡ ስለ ፡ ቦዝ ፡ የምታውቀውን ፡ ሁሉ ፡ ጻፍ ።

5 በሳቢ ፡ ዘርና ፡ በአርእስት ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ ልዩነት ፡ ካስረዳህ ፡ በኋላ ፡ የሚመሳሰሉበትን ፡ ጻፍ ።

6 የማይሻገር ፡ ግስ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ልዩ ፡ ዐይነት ፡ ተሳቢን ፡ ሊያገኝ ፡ ይች ላል ፤ እስኪ ፡ ለማስረጃ ፡ የሚሆኑ ፡ ሁለት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮችን ፡ ሥራ ።

7 ለሚከተሉት ፡ ቃላት ፡ እስከሚቻልህ ፡ ድረስ ፡ ተመሳሳይ ፡ ስጣቸው ።

(ሀ) በክት ፡ ቀልበቢስ ፡ ጥላ ፡ ቆቅ ፡

(ለ) በሚከተሉት ፡ ቃላት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮችን ፡ ሥራባቸው ።

ማማ ፡ በሦስት ፡ ትርጓሜ ፡ በጥገኛ ፡

ሳተ ፡ በድርብ ፡ ድብልቅ ፡ በሁለት ፡ ትርጓሜ ፡

አከረ ፡ በድርብ ፡ ባንድ ፡ ትርጓሜ ፡ ብቻ ፡

8 የሚከተሉትን ፡ ተረቶች ፡ አስረዳ ።

(ሀ) ሠርገኛ ፡ መጣ ፡ በርበሬ ፡ ቀንጥሱ ።

(ለ) ራስ ፡ ሳይጠና ፡ ጉተና ።

(ሐ) መርፌ ፡ የራሷን ፡ ቀዳዳ ፡ ሳታይ ፡ ለብዙ ፡ ሰው ፡ ትጠቅማለች ።

9 የሚከተሉትን ፡ ንኡስ ፡ ሐረጎች ፡ በአረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ አስገባቸው ።

(ሀ) በጠቃሚ ፡ ተይዞ ፡

(ለ) ኩልኩልትን ፡ ካገር ፡ ላይ ፡ ለማጥፋት ፡

(ሐ) የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አድም ፡

10 ከሚከተሉት ፡ አርእስት ፡ መርጠህ ፡ አንድ ፡ ድርሰትን ፡ ጻፍ ።

(ሀ) አበባ ፡

(ለ) ራዲዮ ፡

(ሐ) ሞት ፡

(መ) ደመና ፡

(ሠ) ዛፎች ፡

(ረ) ቤንዚን ፡

ድርሰቱ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ዋጋ ፡ ስላለው ፡ አስቦ ፡ መሥራት ፡ አስፈላጊ ፡ ነው ።

## ፲ኛ ፡ ያማርኛ ፡ ፈተና ፡

1 የሚከተሉትን ፡ ተረቶች ፡ ባጭሩ ፡ አስረዳ ።

(ሀ) በሬ ፡ ሆይ ፡ ሣሩን ፡ አየህና ፡ ገደሉን ፡ ሳታይ ።

(ለ) ሾላ ፡ በድፍን ፡

(ሐ) ቀድሞ ፡ ሰኞን ፡ አለመሆን ፡

2 የሚከተሉትን ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ በተሰጠው ፡ ሰንጠረዥ ፡ ተንትናቸው ። ከዚህ ፡ በፊት ፡ በተማርኸው ፡ በከፍተኛው ፡ ሰንጠረዥ ፡ ነው ።

(ሀ) ቀን ፡ ጎድሎብኝ ፡ በጠላቶቼ ፡ በሮማውያን ፡ እጅ ፡ የወደቅሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከመማረክ ፡ በገዛ ፡ እጄ ፡ መሞትን ፡ እመርጣለሁ ፡ ብሎ ፡ አኒባል ፡ ከጣቱ ፡ በማይለያት ፡ ባንዲት ፡ ቀለበት ፡ ውስጥ ፡ ዕድሜውን ፡ ሙሉ ፡ መርዝ ፡ ይዞ ፡ ይኖር ፡ ነበር ።

ከበደ ፡ ሚካኤ ።

(ለ) ጣሊያኖች ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ ያላገባብ ፡ እያፈሱ ፡ ስለ ፡ ፈጁት ፡ ብዙ ፡ ጎበዞች ፡ ወደ ፡ አርበኞች ፡ ዘንድ ፡ ሄደው ፡ ተቀላቀሉ ።

(ሐ) ምንም ፡ እንኳ ፡ ጣሊያኖች ፡ ባንዳንድ ፡ ቦታ ፡ ላይ ፡ ሕዝቡን ፡ በማታለያ ፡ ስብከት ፡ ቢያዋኽቁት ፡ ነፃነቱን ፡ አልረሳም ።

3 የሚከተለውን ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ዘርዝር ።

የአጼ ፡ ቴዎድሮስ ፡ የመጀመሪያ ፡ አሳባቸው ፡ መላ ፡ ኢትዮጵያን ፡ አስማምተው ፡ ሽፍታንና ፡ ወንበዴን ፡ አጥፍተው ፡ ለመግዛት ፡ ነበር ።

4 በሚከተሉት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ውስጥ ፡ የሚገኙትን ፡ ጥገኛ ፡ መስተፃምሮች ፡ ልቀምና ፡ በያይነታቸው ፡ አመልክት ።

(ሀ) ጣሊያኖች ፡ ሕዝበ ን ፡ ሁሉ ፡ ያላገባብ ፡ እያፈሱ ፡ ስለ ፡ ፈጁት ፡ ብዙ ፡ ጎበዞች ፡ ወደ ፡ አርበኞች ፡ ዘንድ ፡ ሄደው ፡ ተቀላቀሉ ።

(ለ) ምንም ፡ እንኳ ፡ ጣሊያኖች ፡ ባንዳንድ ፡ ቦታ ፡ ላይ ፡ ሕዝቡን ፡ በማታለያ ፡ ስብከት ፡ ቢያዋኽቁት ፡ ነፃነቱን ፡ አልረሳም ።

(ሐ) ከዚህ ፡ ፈተና ፡ እንደማላመልጥ ፡ ሳውቀው ፡ ለምን ፡ በከንቱ ፡ ታታልለኛለህ ?

(መ) ጉዳዩን ፡ ብትፈጽምልኝ ፡ ውለታህን ፡ እከፍልሃለሁ ።

(ሠ) አቶ ፡ ፈለቀ ፡ በጠና ፡ ስለ ፡ ታመመ ፡ መናዘዝ ፡ አቅቶታል ።

5 «አፈሰ» ፡ በሚባለው ፡ ግስ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ትርጓሜ ፡ አራት ፡ አረፍተ ፡ ነገሮችን ፡ ሥራ ።

(ሀ) በነጠላ ፡ (ሐ) በድርብ ፡
(ለ) በድብልቅ ፡ (መ) በድርብ ፡ ድብልቅ ፡

6 ከሚከተሉት ፡ አርእስት ፡ መርጠህ ፡ አንድ ፡ ድርሰትን ፡ ጻፍ ።

(ሀ) ወታደር ፡ (ሐ) አርበኝነት ፡
(ለ) ወፍ ፡ (መ) መብረቅ ፡

ድርሰቱ ፡ ሙሉ ፡ ስሜትን ፡ እንዲገልጽ ፡ ተደርጎ ፡ መጻፍ ፡ አለበት ።



